# የመጽሐፍ ቅዱስ
# መዝገበ ቃላት



የኢትዮጵያ መጽሐፍ ቅዱስ ማኅበር

# የመጽሐፍ ቅዱስ
# መዝገበ ቃላት

የኢትዮጵያ መጽሐፍ ቅዱስ ማኅበር




አዲስ አበባ
በባናዊ ማተሚያ ቤት ታተመ

## መቅድም ለመጀመሪያው እትም

ስለ መጽሐፍ ቅዱስ በየጊዜው ብዙ መጻሕፍት ተጽፈዋል። አጻጻፋቸውም በስብከት፥ በንግግርና በትርጓሜ መልክ ነው። ነገር ግን በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ የሚገኙትን ዋና ዋና አርእስት ተራ በተራ በማስቀመጥ ትርጓሜአቸውንም በመግለጥ የተጻፉ መጻሕፍት ጥቂቶች ናቸው። ስለዚህም ለወንጌል አስተማሪዎችና ለመጽሐፍ ቅዱስ ወዳጆች ጠቃሚ እንደሚሆን በልዩ ልዩ ቤተ ክርስቲያን መሪዎች ከ1962 ዓ.ም. ጀምሮ ታስቦ እነሆ፥ ይህ «የመጽሐፍ ቅዱስ መዝገበ ቃላት» ተዘጋጀ።

ይህ መጽሐፍ ትርጓሜ አይደለም፤ ሆኖም ብዙ ጥቅሶችን ያብራራል። ማውጫ አይደለም፤ ግን ብዙ አሳቦችን ከመጽሐፍ ቅዱስ ለማግኘት ያስችላል። መጽሐፉ ከመጠን በላይ እንዳይሆን በማለት ሁለት ሺህ የሚያህሉ አርእስት ብቻ እንዲይዝ ተደርጓል። ሙሉ ማውጫ ቢሆን ከዐሥር ሺህ በላይ አርእስት ስለሚኖሩት መጽሐፉ ይከብድ ነበር። እርግጥ የመጽሐፍ ቅዱስን መሠረታዊ አሳብ ከሚገልጹት አርእስት መካከል የቀረ እንደሌለ ተስፋ እናደርጋለን። ብዙ ሰዎችንና ቦታዎችን በስም ዝርዝር ማቅረብ አስፈላጊ ሆኖ አልተገኘም፤ ታሪካውያን አይደሉምና ነው። ብዙ የታወቁ ቃላትንም ማብራራት አላስፈለገም። ነገር ግን ታሪካውያን ሰዎች፥ ቦታዎችና ድርጊቶች፥ የሃይማኖትና ዘመናዊ ያልሆኑ አማርኛ ቃላት፥ የመጽሐፍ ቅዱስ ዘመን ባህል፥ ልማድ፥ ሁኔታ፥ ድርጅት፥ ሥርዓትና የኅብረተሰብ አቋም፥ መጻሕፍት በየርእስ ይገኛሉ። አስተዋይ አንባቢ ብዙ ትምህርት እንደሚያገኝባቸው እንተማመናለን።

ይህን መጽሐፍ ያዘጋጁት፥ በልዩ ልዩ ቤተ ክርስቲያንና ድርጅት የሚገኙ ሰዎች ናቸው። እያንዳንዱ ጸሐፊ መሠረተ አሳቡን ሳይለቅ በራሱ አቀራረብ ጽፎአል። ስለ አንዳንድ አሳቦች በመጽሐፍ ቅዱስ ሊቃውንት መካከል ልዩነት እንዳለ የታወቀ ነው። አንድ ድርጊት ብዙ ዓመታት ካለፉት በኋላ ምን እንደሆነና እንዴት እንደነበረ ለመወሰን የአንድን ጥንታዊ ቋንቋ በትክክል ለመተርጐም አስቸጋሪ ቢሆን አያስገርምም። አስገራሚ ነገር ቢገኝ የመጽሐፍ ቅዱስ ሊቃውንት አልፎ አልፎ በአሳብ ቢራራቁም በብዙ ነገር አለመለያየታቸው ነው። እያንዳንዱ ጸሐፊ በየአርእስቱ ለራሱ የሚያምንበትን ዋና አሳብ ብቻ አቅርቦአል፤ አልፎ አልፎም የልዩ ሰዎችን አስተያየት ጠቅሶአል። አዘጋጆች በሚጽፉበት ጊዜ በተለይ ሊክላንድ ባይብል ዲክሽኔሪን፥ ዘ ኒው ባይብል ዲክሽኔሪን እና መዝገበ ቃላት ዘ ኪዳን ወልድ ክፍሌን ለመመሪያ ተጠቅመውባቸዋል።

ይህ መጽሐፍ በሚዘጋጅበት ጊዜ ጽሑፎችን በማዘጋጀት፥ በምክር የረዱንን ግለሰቦችና ሥዕሎቻቸው በመጽሐፉ ውስጥ እንዲገቡ የፈቀዱልንን ድርጅቶች ከልብ እናመሰግናቸዋለን።

ይህ መጽሐፍ ለእግዚአብሔር ክብርና ለሕዝቡ ጥቅም እንዲሆን እየጸለይን በትሕትና እናበረክታለን።

የኢትዮጵያ መጽሐፍ ቅዱስ ማኅበር።

## መቅድም ለስድስተኛ እትም

ከ1989 ዓ.ም. ጀምሮ ይህን መዝገበ ቃላት ለማሻሻልና ለአዲሱ ትውልድ የበለጠ አገልግሎት እንዲሰጥ ለማድረግ ልዩ ልዩ ሰዎች በዝግጅቱ ተባብረዋል። ይህን መዝገበ ቃላት እንደገና ለእግዚአብሔር ክብርና ለሕዝቡ ጥቅም እንዲሆን እየጸለይን በትሕትና እናበረክታለን።

የኢትዮጵያ መጽሐፍ ቅዱስ ማኅበር።

# የሥዕሎች ባለ መብት

በዚህ መጽሐፍ ውስጥ የሚገኙት ሥዕሎች ከዚህ በታች በተዘረዘሩት ድርጅቶች ልዩ ፈቃድ የታተሙ ሲሆን የተጠቃሾቹ ድርጅቶች መብት በሕግ የተጠበቀ ነው።

1. በሆሬስ ኖልዝ (HORACE KNOWLES) በ1954፥ በ1967፥ በ1972 በኋላም በ1994 በሉኢዝ ባስ (Louise Bass) የተጨመሩና የተሻሻሉ ሥዕሎች ከ BRITISH AND FOREIGN BIBLE SOCIETY, LONDON, ENGLAND (ከሎንዶን የመጽሐፍ ቅዱስ ማኅበር) የተፈቀዱ፤

ሂሶጵ
የለውዝ አበባ
ሊቀ ካሕናት
የሊባኖስ ዝግባ
የሌሊት ወፍ
መለከት
መላጥያ (መርከብ)
መልሕቅ
መሠዊያ
መርበብ (መረብ)
መርከብ (በሸራ)
መስፈሪያ (ደረቅ)
መስፈሪያ (ፈሳሽ)
መቅረዝ
መቅዘፊያ
መንሽ
መንፈስ ቅዱስ
መከፈቻ (ቍልፎች)
መጅ
ሚዳቋ
ማሄጃ
ማቴዎስ
ምኩራብ
ምኩራብ (ውስጥ)
የምድያም ነጋዴዎች
ምግብ (ዳቦ ሲዘጋጅ)
የጭነት ሠረገላ
የጭነት ሠረገላ
የጦር ሠረገላ
ርኩስ እንስሳት
ሮማን
የሮም ከተማ
የሮም አርማ
ሰቅል
ሰቆቃወ ኤርምያስ

ሴኬም
ስቅለት
የስቅለት ጽሑፍ
ሸኮኮ
ሾላ
ቀርሜሎስ
ቀስት
ቀበሮ
ቀንበር
ቀንዲል
ቀንድ
ቂሮስ
ቅዱስ ቍርባን
ቅጥር
ቆብ
በለስ
በር
በትር
በገና
ባቢሎን
ቤተ መቅደስ
የሄሮድስ ቤተ መቅደስ
መመላለሻ
ቤት (ጣራ)
ተምር
ተሰሎንቄ
ተኩላ
ተግባረ እድ (የሴቶች)
ቱንቢ
ነብር
ነነዌ
ነጋሪት
ናርዶስ
የናስ መሠዊያ
ናቡከደነፆር

ናዝሬት
ንስር
ንግድ
አሸንክታብ
አብርሃም
አታሞ
አቴና
አንበሳ
አንበጣ
አክሊል
አዝሙድ
አዞ
ኡሪምና ቱሚም
ኢየሩሳሌም
ኢዮብ
ኤፌሶን
እረኛ
እርያ
የእግዚአብሔር ማደሪያ
ከርቤ
ከበሮ
ካህን
ክርታስ
ወኅኒ
ወይራ
ወይን
የወይን ግንብ
ዋላ
ዐምድ
ዓሣ አጥማጅ
ዕጣን
የዕጣን መሠዊያ
የዜማ ዕቃ
ዲናር
ዳርዮስ

ዳጎን
ድርጭት
ድብ
ድንቢጥ
ድንብላል
ድንኳን
ዶሮ
ጅንጅላቴ ወፍ
ገሊላ
ገቢታ
ጉበን
ጊንጥ
ጋሻ
ግመል
ግሪክ
ግንድ
ጕድጓድ
ጓጕንቸር
ጠባቂ
ጡብ
ጣርያ
ጣዖት
ጣዖት
ጥልፍ
ጥቅልል
ጥና
ጦር ሠራዊት
ጦር ሠራዊት (መቶ አለቃ)
ጸናጽል
ጻፌ
ጽሕፈት
ፈረስ
ፍጥረት

# መግቢያ

ከዚህ መጽሐፍ ጥቅም ለማግኘት የሚከተሉትን መገንዘብ ይረዳል።

1. **አርእስት፤** ቃላት ብዙ ጊዜ በስም ዓይነት ይገኛሉ፥ ስለዚህ «ዳኝ» በሚለው ሳይሆን «ደኀንነት» በሚል ርእስ የመዳን ነገር ተጽፎ ይገኛል። አንዳንድ ጊዜ ግን ግሦች በርእስ ተሰጥተዋል፤ ለምሳሌ፥ «ኩነን»፥ «አበራ፣» ... ወዘተ። ቅጽልና ባለቤት፥ ዘርፍና ባለቤት ያላቸው ቃላት ሲገኙ በሁሉም መሞከር ይገባል። ብዙ ጊዜ ግን በመጀመሪያው፥ ማለትም በባለቤቱ ወይም በቅጽሉ ይገኛል። ለምሳሌ «አላባሽ አግሬ ጋሻ»፥ «አላባሽ» በሚል ርእስ ይገኛል። አንዳንድ አርእስት ደግሞ በሁለተኛው በዘርፉ ይገኛሉ፤ ለምሳሌ «መጽሐፈ ምሳሌ»፥ «ምሳሌ» በሚለው ርእስ ይገኛል። ግን ሰፊ ማብራሪያ የተሰጠበትን ርእስ ለማመልከት እንዲህ ተባለ እንጂ ሁሉም ቃል በየአርእስቱ ይገኛል። አገናዛቢ ያለበትን ቃል ደግሞ በስም ዓይነት ማውጣት ያስፈልጋል። ለምሳሌ «የፍጥረት መጀመሪያ»፥ «ፍጥረት» በሚለው ርእስ ይገኛል።

2. **ጥቅሶች፤** የተጠቀሱትን ጥቅሶች ከመ.ቅ. ማንበብ ያስፈልጋል። የጥቅስ አወጣጥ ሕግ 1980 ዓ.ም. በታተመው መ.ቅ. ይገኛል። ስለ እያንዳንዱ ርእስ ዋና ዋና ጥቅሶች ተሰጥተዋል። ከዚህ በተረፈ ግን በአዲስ ኪዳን ግርጌ ያሉ ተመሳሳይ ጥቅሶችን በመመልከት ሌሎችንም ማግኘት ይቻላል። ከዚህም ጋር ተመሳሳይ አርእስትን መመልከት ተጨማሪ ትምህርትን ለማግኘት ይረዳል።

3. **የቃላት ትርጉም፤** አንዳንድ ቃላት ለምሳሌ እንደ «ሰንበር» ያሉት ብዙ ነገሮችን ሊያመለክቱ ይችላሉ። በዚህ መጽሐፍ ግን ቃሉ በመ.ቅ. ምንን እንደሚያመለክት ይገለጣል። ይህንም ለማድረግ ጸሐፊዎች የቃሉን መሠረተ አሳብ ለመግለጥ የዕብራይስጥ ወይም የግሪክ ቃልን ተመልክተዋል።

4. **የስሞች ትርጓሜ፤** ብዙ ስም ትርጉም ይኖረዋል፤ ነገር ግን ከአንድ ቋንቋ ወደ ሌላ ለመተርጐም ያስቸግራል። ስለ አንዳንድ ስሞች የሊቃውንት አስተሳሰብ የተለያየ በመሆኑ በመግለጫ ከተሰጠው ትርጓሜ ሌላ ሊኖረው ይችላል።

5. **የዓመት አቈጣጠር፤** ልዩ ልዩ አቈጣጠር እንዳለ የታወቀ ነው። ይህ መጽሐፍ በሌሎች ቋንቋዎች ከተጻፉት የመጽሐፍ ቅዱስ መዝገበ ቃላት ጋር እንዲስማማ ዓመታት እንደ ኤሮፓ አቈጣጠር ተጽፈዋል። የክርስቶስ ልደት የዓለም ታሪክ መነሻ በመሆኑ ዓመታትን ከክርስቶስ ልደት በፊት (ከክ.በ.) እና ከክርስቶስ ልደት በኋላ ብለን በዚህ መጽሐፍ እንቆጥራለን። ለምሳሌ ኢሳይያስ ከክርስቶስ በፊት በ700 ዓመታት ከክ.በ. ሲባል ክርስቶስ ሊመጣ 700 ዓመት ሲቀረው ማለት ነው። ይህ ዘዴ ከተለመደው ከ«ዓመተ ዓለም» አቈጣጠር ለየት ያለ መሆኑን እናሳስባለን። ዓመተ ምሕረት መነሻው የክርስቶስ ልደት ስለሆነ ይታወቃል። «ዓመት» ይመ.

6. **የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት፤** በብዙ ሰው እጅ የሚገኘው መ.ቅ. ስድሳ ስድስት መጻሕፍትን ያጠቃልላል። ይህ መጽሐፍ እነዚህን በሰፊው ይጠቅሳል። አብያተ ክርስቲያናት ሁሉ ስድሳ ስድስቱን ይቀበላሉ፤ ስለ ሌሎች መጻሕፍት ግን የተለያየ አሳብ እንዳለ የታወቀ ነው፤ ስማቸውንም «አዋልድ» ወይም «አፖክሪፋ» ይሉአቸዋል፤ ስለ እነዚህም አርእስት ተዘጋጅቶአል፤ ነገር ግን ሌሎች አርእስት ለማስረጃ በብዛት አልተጠቀሱም።

7. **ሥርዓተ ፊደል፤** በአማርኛ መጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ የአንዳንድ ቃላት ፊደሎች አልፎ አልፎ አንድ ዓይነት አይደሉም፤ ለምሳሌ አንድ ጊዜ «ግብጽ» በሌላም ጊዜ «ግብፅ» ይላል፤ እንደዚሁም «ዓላማ»፥ «አላማ» ብሎ ይገኛል። ስለዚህ አንድ ቃል በተለመደው ፊደል ባይገኝም በተመሳሳይ ፊደል መፈለግ ይረዳል። ደግሞም በመ.ቅ. ውስጥ ባለው አንዳንድ ሥርዓተ ፊደል

2. ከ«ዚ ኢንተር ቫርስቲ ፕሬስ (THE INTER VARSITY PRESS) የተፈቀዱ ፡-

| | | | |
|---|---|---|---|
| የታላቁ ሄሮድስ ገንዘብ | | ኔሮ | ዘፈን |
| የሄሮድስ አርኬላዎስ ገንዘብ | | አርኪዎሎጂ | የይሁዳ ሰዎች |
| የሄሮድስ አንቲጳስ ገንዘብ | | አስታሮት | ደንገል |
| የቀዳማዊ ሄሮድስ አግሪጳ ገንዘብ | | አንጾኪያ | ዳርዮስ |
| ልብስ | ሰጐን | ኢዩ | ግርፋት |
| ሎቲ | ሱሳ | ኢያሪኮ | ጠጉር |
| መልእክት | ሶርያ | አባብ | የጥላ ስፍረ ሰዓት |
| መጭመቂያ | ሽኩራ | ከውር | የጦር መሣሪያ |
| ሚዛን | ቀለበት | ክብደት | ጦርነት |
| ማኅተም | ቆማር | ወልደ አዴር | ፈርጥ |
| ሚሮዳክ | በአል | ወንጭፍ | ፊደል |
| ሚዶን | ቤት (ዑር) | ወጥመድ | ፍልስጥኤም |
| ሰማርያ | ተራፊም | ዓላማ | |
| ሰናክሬም | ናስ | ዘውድ | |

3. ከ«ዚ ዌስትሚንስተር ዲክሽነሪ ኦፍ ዚ ባይብል» (THE WESTMINSTER DICTIONARY OF THE BIBLE) በጆን ዲ ዴቪስ ከተዘጋጀ በሄንሪ ስናይደር ጌህማን ታርሞ ከዚዌስትሚንስተር ፕሬስ ከታተመ የተፈቀዱ፥ መቃብር፥ የአገናኝ ዘዴ፥ አንባር፥ ዙፋን፥ የጥጃ ምስል።

4. ከሲንድኪሽን ኢንተርናሽናል ሊሚትድ (SYNDICATION INTERNATIONAL LIMITED) የተፈቀደ ፡- የጭቃ ቅርጽ።

5. ከሲንገር ከተጻፈ ከ«ኤ ሂስቶሪ ኦፍ ቴክኖሎጂ» (A HISTORY OF TECHNOLOGY) የተገኘ ከኦክስፎርድ ዩኒቨርስቲ ፕሬስ የተፈቀደ ፡- ተግባረ እድ፥ የአናጢ መሣሪያዎች።

6. ከዚ ዩኒቨርሲቲ ሙዚዩም ኦፍ ዚ ዩኒቨርሲቲ ኦፍ ፔንሲልቪኒያ የተፈቀደ ፡- የዑር ጣዖት መቅደስ።

ሊቃውንት ላይስማሙ ይችላሉ፤ የዚህ መጽሐፍ አዘጋጆች ግን በመ.ቅ. ውስጥ ባለው ሥርዓተ ፊደል ተመርተዋል።

**8. ሥዕሎች፤** በዚህ መጽሐፍ የሚገኙ ሥዕሎች በመቅድሙ ላይ እንደተገለጠው ከልዩ ልዩ ድርጅትና ማኅበር የተገኙ ናቸው። በመ.ቅ. ዘመን የነበሩት ሕንጻዎች ሁሉ ፈርሰዋል። ሆኖም ልዩ ልዩ የቤት ዕቃዎችና መሣሪያዎች፥ በድንጋይ ላይ የተቀረጹ ሥዕሎች፥ ገንዘቦች፥ መቃብሮችና የቤት ፍርስራሾች በብዛት ተገኝተዋል። እነዚህንም በማጥናት በመ.ቅ. ዘመን ቤት፥ ልብስ፥ ባህል ... ወዘተ እንዴት እንደነበረ ለመገመት ተችሎአል። ስለዚህ አንዳንድ ሥዕሎች ከድንጋይ ቅርጾች የተቀዱ ናቸው፤ ሠዓሊዎችም የተገኘውን ዕቃና ፍርስራሽ፥ ሌላውንም ከመረመሩ በኋላ እየሣሉ እንዴት እንደነበረ ለማሳወቅ ተግተዋል። ከቃላት ጋር የሥዕል ማስረጃ ጠቃሚ ነውና አንዳንድ ጥንታውያን ነገሮች በሥዕል ተገልጠዋል።

**9. ካርታዎች፤** በመጽሐፉ መጨረሻ ቍጥር ያላቸው ካርታዎች ይገኛሉ፤ በካርታዎች ላይ ሰንጠረዥ ተደርጎአል፤ ለየክፍሉም ፊደል ይኖረዋል፤ ስለዚህ በመግለጫው ላይ ካ.2ሀ ተብሎ ቢጻፍ፥ የተጠቀሰው ቦታ በ2ተኛው ካርታ በሰንጠረዥ በ«ሀ» ክፍል ይታያል።

**10. ምኅፃረ ቃል፤** ብዙ ጊዜ ተደጋግመው የሚገኙ ቃላት በምኅፃረ ቃል እንደሚከተለው ተገልጠዋል።

| | | |
|---|---|---|
| መ.ቅ. | ማለት | መጽሐፍ ቅዱስ |
| ም. | ማለት | ምዕራፍ |
| ሥ. | ማለት | ሥዕል |
| ቍ. | ማለት | ቍጥር |
| ቤ.ክ. | ማለት | ቤተ ክርስቲያን |
| ብ.ኪ. | ማለት | ብሉይ ኪዳን |
| አብ.ክ. | ማለት | አብያተ ክርስቲያናት |
| አ.ኪ. | ማለት | አዲስ ኪዳን |
| እ.ኤ.አ. | ማለት | እንደ ኤሮፓ አቈጣጠር |
| እ.ኢ.አ. | ማለት | እንደ ኢትዮጵያ አቈጣጠር |
| ከክ.በ. | ማለት | ዓመት ከክርስቶስ (ልደት) በፊት |
| ኪ.ሜ. | ማለት | ኪሎ ሜትር |
| ካ. | ማለት | ካርታ |
| ዓ.ም. | ማለት | ዓመተ ምሕረት (ከክርስቶስ ልደት በኋላ) |
| ይመ. | ማለት | ይመልከቱ |

# 11. የመጽሐፍ ቅዱስ መጻሕፍት ምኅፃረ ቃል ዝርዝር፤

## የብሉይ ኪዳን መጻሕፍት

| ሙሉ ስም | ባጭሩ | ሙሉ ስም | ባጭሩ |
|---|---|---|---|
| ኦሪት ዘፍጥረት | ዘፍ. | መጽሐፈ መክብብ | መክ. |
| ኦሪት ዘጸአት | ዘጸ. | መኃልየ መኃልይ | መ.መ. |
| ኦሪት ዘሌዋውያን | ዘሌ. | ትንቢተ ኢሳይያስ | ኢሳ. |
| ኦሪት ዘኍልቍ | ዘኍ. | ትንቢተ ኤርምያስ | ኤር. |
| ኦሪት ዘዳግም | ዘዳ. | ሰቆቃወ ኤርምያስ | ሰ.ኤ. |
| ኢያሱ | ኢያሱ | ትንቢተ ሕዝቅኤል | ሕዝ. |
| መሳፍንት | መሳ. | ትንቢተ ዳንኤል | ዳን. |
| ሩት | ሩት | ትንቢተ ሆሴዕ | ሆሴዕ |
| 1 መጽሐፈ ሳሙኤል | 1ሳሙ. | ትንቢተ ኢዩኤል | ኢዩ. |
| 2 መጽሐፈ ሳሙኤል | 2ሳሙ. | ትንቢተ አሞጽ | አሞጽ |
| 1 መጽሐፈ ነገሥት | 1ነገ. | ትንቢተ አብድዩ | አብ. |
| 2 መጽሐፈ ነገሥት | 2ነገ. | ትንቢተ ዮናስ | ዮናስ |
| 1 መጽሐፈ ዜና መዋዕል | 1ዜ.መ. | ትንቢተ ሚክያስ | ሚክ. |
| 2 መጽሐፈ ዜና መዋዕል | 2ዜ.መ. | ትንቢተ ናሆም | ናሆም |
| ዕዝራ | ዕዝ. | ትንቢተ ዕንባቆም | ዕን. |
| ነህምያ | ነህ. | ትንቢተ ሶፎንያስ | ሶፎ. |
| አስቴር | አስ. | ትንቢተ ሐጌ | ሐጌ |
| ኢዮብ | ኢዮብ | ትንቢተ ዘካርያስ | ዘካ. |
| መዝሙረ ዳዊት | መዝ. | ትንቢተ ሚልክያስ | ሚል. |
| መጽሐፈ ምሳሌ | ምሳ. | | |

## የአዲስ ኪዳን መጻሕፍት

| | | | |
|---|---|---|---|
| የማቴዎስ ወንጌል | ማቴ. | 1 ወደ ጢሞቴዎስ | 1ጢሞ. |
| የማርቆስ ወንጌል | ማር. | 2 ወደ ጢሞቴዎስ | 2ጢሞ. |
| የሉቃስ ወንጌል | ሉቃ. | ወደ ቲቶ | ቲቶ |
| የዮሐንስ ወንጌል | ዮሐ. | ወደ ፊልሞና | ፊልሞና |
| የሐዋርያት ሥራ | ሐ.ሥ. | ወደ ዕብራውያን | ዕብ. |
| ወደ ሮም ሰዎች | ሮም | የያዕቆብ መልእክት | ያዕ. |
| 1 ወደ ቆሮንቶስ ሰዎች | 1ቆሮ. | 1 የጴጥሮስ መልእክት | 1ጴጥ. |
| 2 ወደ ቆሮንቶስ ሰዎች | 2ቆሮ. | 2 የጴጥሮስ መልእክት | 2ጴጥ. |
| ወደ ገላትያ | ገላ. | 1 የዮሐንስ መልእክት | 1ዮሐ. |
| ወደ ኤፌሶን | ኤፌ. | 2 የዮሐንስ መልእክት | 2ዮሐ. |
| ወደ ፊልጵስዩስ | ፊል. | 3 የዮሐንስ መልእክት | 3ዮሐ. |
| ወደ ቆላስይስ | ቆላ. | የይሁዳ መልእክት | ይሁዳ |
| 1 ወደ ተሰሎንቄ ሰዎች | 1ተሰ. | የዮሐንስ ራእይ | ራእ. |
| 2 ወደ ተሰሎንቄ ሰዎች | 2ተሰ. | | |

**12. የጥቅስ አገባብ፤** ጥቅስ ሲጠቀስ መጽሐፉ፥ ምዕራፉና ቍጥሩ ይሰጣል። መጽሐፉ በአጭሩ ከተጻፈ በኋላ፥ ከነጠላ ሠረዝ «፥» በስተግራ ምዕራፉ፥ ከነጠላ ሠረዙ በስተቀኝ ደግሞ ቍጥሩ ይኖራሉ። ለምሳሌ ማቴ. 2፥7 የማቴዎስን ወንጌል ምዕራፍ 2 ቍጥር 7 ያመለክታል። በቍጥሮቹ መካከል «-» ካለ «እስከ» ማለቱ ነው። ለምሳሌ ማቴ. 2፥7-10 የማቴዎስን ወንጌል ምዕራፍ 2 ቍጥር 7 እስከ ቍጥር 10 ያለውን ያመለክታል። በቍጥሮች መካከል ሁለት ነጥብ ካለ «፡»ከአንድ ቍጥር በላይ ይነበባል። ለምሳሌ ማቴ. 2፥7፡12፡21 የማቴዎስን ወንጌል ምዕራፍ 2 ቍጥር 7፥ ዐሥራ ሁለትና ኃያ አንድ ያመለክታል። ከጥቅስ በኋላ ድርብ ሠረዝ «፤» ሲገኝ ሌላ ጥቅስ እንደሚከተል ይገልጣል። ም.2፥5-6፥4 ምዕራፍ 2 ቍጥር አምስት እስከ ምዕራፍ 6 ቍጥር አራት ያለው ይነበባል ማለት ነው።

መዝሙረ ዳዊትን በተመለከተ ሁለት ዓይነት አቈጣጠር እንዳለ የታወቀ ነው። ይህ መዝገበ ቃላት በዕብራይስጥና በእንግሊዝኛ እንዲሁም በአማርኛ 1980 ዓ.ም. ትርጒም ያለውን አቈጣጠር ይከተላል። በ1953 ዓ.ም. የታተመው ግን የሰባ ሊቃናትንና የግእዝን አቈጣጠር ስለሚከተል አንባቢው ይህን እትም የያዘ ከሆነ በቅንፍ ውስጥ ያሉትን ቍጥሮች መመልከት አለበት።

**13. የአርእስት ቅደም ተከተል፤** በዚህ መጽሐፍ በሀ ለ ሐ መ መሠረት እንደሚከተለው ነው ፦

| | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|
| ሀ | ሁ | ሂ | ሃ | ሄ | ህ | ሆ | |
| ለ | ሉ | ሊ | ላ | ሌ | ል | ሎ | ሏ |
| ሐ | ሑ | ሒ | ሓ | ሔ | ሕ | ሖ | |
| መ | ሙ | ሚ | ማ | ሜ | ም | ሞ | ሟ |
| ሠ | ሡ | ሢ | ሣ | ሤ | ሥ | ሦ | |
| ረ | ሩ | ሪ | ራ | ሬ | ር | ሮ | ሯ |
| ሰ | ሱ | ሲ | ሳ | ሴ | ስ | ሶ | ሷ |
| ሸ | ሹ | ሺ | ሻ | ሼ | ሽ | ሾ | ሿ |
| ቀ | ቁ | ቂ | ቃ | ቄ | ቅ | ቆ | |
| ቈ | | | ቋ | ቌ | ቍ | | |
| በ | ቡ | ቢ | ባ | ቤ | ብ | ቦ | ቧ |
| ተ | ቱ | ቲ | ታ | ቴ | ት | ቶ | ቷ |
| ቸ | ቹ | ቺ | ቻ | ቼ | ች | ቾ | ቿ |
| ኀ | ኁ | ኂ | ኃ | ኄ | ኅ | ኆ | ኋ |
| ነ | ኑ | ኒ | ና | ኔ | ን | ኖ | ኗ |
| ኘ | ኙ | ኚ | ኛ | ኜ | ኝ | ኞ | ኟ |
| አ | ኡ | ኢ | ኣ | ኤ | እ | ኦ | |
| ከ | ኩ | ኪ | ካ | ኬ | ክ | ኮ | |

| | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|
| ኰ | | | ኳ | ኴ | ኵ | | |
| ኸ | ኹ | ኺ | ኻ | ኼ | ኽ | ኾ | |
| ወ | ዉ | ዊ | ዋ | ዌ | ው | ዎ | |
| ዐ | ዑ | ዒ | ዓ | ዔ | ዕ | ዖ | |
| ዘ | ዙ | ዚ | ዛ | ዜ | ዝ | ዞ | ዟ |
| ዠ | ዡ | ዢ | ዣ | ዤ | ዥ | ዦ | ዧ |
| የ | ዩ | ዪ | ያ | ዬ | ይ | ዮ | |
| ደ | ዱ | ዲ | ዳ | ዴ | ድ | ዶ | ዷ |
| ጀ | ጁ | ጂ | ጃ | ጄ | ጅ | ጆ | ጇ |
| ገ | ጉ | ጊ | ጋ | ጌ | ግ | ጎ | |
| ጐ | | | ጓ | ጔ | ጕ | | |
| ጠ | ጡ | ጢ | ጣ | ጤ | ጥ | ጦ | ጧ |
| ጨ | ጩ | ጪ | ጫ | ጬ | ጭ | ጮ | ጯ |
| ጰ | ጱ | ጲ | ጳ | ጴ | ጵ | ጶ | |
| ጸ | ጹ | ጺ | ጻ | ጼ | ጽ | ጾ | ጿ |
| ፀ | ፁ | ፂ | ፃ | ፄ | ፅ | ፆ | |
| ፈ | ፉ | ፊ | ፋ | ፌ | ፍ | ፎ | ፏ |
| ፐ | ፑ | ፒ | ፓ | ፔ | ፕ | ፖ | |

**ሀብት፤** ማናቸውም ዓይነት የንብረትና የገንዘብ ብዛት ወይም ሥጋዊና መንፈሳዊ ችሎታ፤ ዘፍ. 13፥2፤ ኢያሱ 22፥8፤ ኢዮብ 1፥3፤ 1ቆሮ. 1፥5:6፤ ራእ. 2፥9፤ 3፥17። እግዚአብሔር ለጋስ ነውና ሀብት የእርሱ በረከት ነው፤ በተለይ እግዚአብሔርን የሚፈራ ባለጠጋ ይሆናል፤ መዝ. 1፥1-3፤ 112፥1-3፤ 1ጢሞ. 6፥17። ሀብታም ለጋስ መሆን አለበትና እንደሚገባው ሀብቱን ቢያካፍል መንፈሳዊ በረከትን ያገኛል፤ ምሳ. 11፥24፤ ሉቃ. 12፥33፤ 16፥11፤ 1ጢሞ. 6፥18-19፤ 2ቆሮ. ም. 8-9።

ሀብታም ያለውን ከእግዚአብሔር እንደተቀበለ እንዳይረሳ (ዘዳ. 8፥17:18) በሀብቱም እንዳይመካ መጠንቀቅ አለበት፤ መዝ. 52፥7፤ ማቴ. 13፥22፤ 19፥22-26፤ ሉቃ. 12፥16-21፤ 16፥14-31። ባለጠግነት ማሰናከያ ሊሆን ስለሚችል መጠነኛ ሀብት ይሻላል፤ ምሳ. 30፥8-9። ሰው ባለው መደሰት እንጂ ብዙ ሀብትን መመኘት አይገባውም፤ መዝ. 62፥10፤ 1ጢሞ. 6፥8-10፤ ዕብ. 13፥5።

የኢየሩሳሌም ቤ.ክ. ሀብትን በአንድነት አሰባስባ መያዝ ስለጀመረች ድሀ በመካከልዋ አልነበረም፤ ሐ.ሥ. 4፥32-37። በኋላ ግን በሌሎች አብ.ክ. የኢየሩሳሌም ድሆች መረዳታቸው አስፈላጊ ሆነ፤ ሮም 15፥25-29፤ ገላ. 2፥10። ማንኛዋም ቤ.ክ. ለራስዋ ድሆች ማሰብ ይገባታል፤ ሮም 12፥13። በሀብት ምክንያት ልዩነት እንዳይደረግ ተከልክሏል፤ ያዕ. 2፥1-7።

መዝሙረኛው፥ ብዙ ጊዜ ኃጢአተኞች ባለጠጎች፥ እግዚአብሔርንም የሚፈሩ ድሆች ስለሆኑ እግዚአብሔርን መከተል ምን ይጠቅማል? ብሎ ይጠይቃል፤ መዝ. 73፥12-14። መልሱ በመጨረሻ ባለጠጎች ወደ ፍርድ እንደሚቀርቡ የጻድቅም ሀብት እግዚአብሔርን ማወቅ ነው፤ መዝ. 73፥16-28። በዚህ አንጻር ባለጠጎች ይረገማሉ፥ ድሆችም ይከብራሉ፤ ሉቃ. 6፥20:24፤ ያዕ. 5፥1-6።

**ሁሉ፤** ይህ ቃል ብዙ ጊዜ የዓለም ሰዎችን ሁሉ አንድም ሳይቀር (ሮም 3፥23)፥ ወይም አማኞችን ሁሉ ሊያመለክት ይችላል፤ ዮሐ. 3፥16። አንዳንድ ጊዜ የሚበዙትን ይመለከታል፤ ማር. 1፥33። በሌሎች አንቀጾችም ቃሉ ሰዎችን ከማዕረግ ወይም ከወገን በተለይም ከአይሁድና ከአሕዛብ በአንድነት እንጂ አንድ ሳይቀር ሁሉንም አያመለክትም፤ ዮሐ. 12፥20:32፤ 1ጢሞ. 2፥1-7።

**ሁልጊዜ፤** ቃሉ የእግዚአብሔርን ሥራ ሲያመለክት ያለ ዕረፍት የሚያደርገውን ያሳስባል (ማቴ. 28፥20)፤ ሰውን ሲያመለክት ግን ድርጊት ላይ ተመርኩዞ የሚዘወተረውን ይገልጣል፤ 1ተሰ. 1፥2:3።

**ሂሶጵ (ሁሶፕ)፤** ብ.ኪ. ልዩ ልዩ ተክሎችን በአንድ ቃል አጠቃሎ ይገልጻቸዋል። 1. በአይሁድ ሥርዓት መሠረት ደም የሚረጭበት አጭር ተክል፤ ዘጸ. 12፥22። 2. በግንብ ላይ የሚበቅል አነስተኛ



ተክል፤ 1ነገ. 4፥33። 3. በኢየሱስ ስቅለት ጊዜ ሰፍነጉ የተደረገበት «ሁሶፕ» መቃ የመሰለ ሌላ ዓይነት ተክል። ምናልባት የዘንጋዳ አገዳ ሊሆን ይችላል፤ ዮሐ. 19፥29፤ ደግሞም ማቴ. 27፥48 ይመ.

**ሃሌሉያ፤** በዕብራይስጥ «እግዚአብሔርን አመስግኑ» ማለት ነው፤ መዝ. 111፥1፤ ራእ. 19፥6። ብዙ ጊዜ ቃሉ ለመዝሙራት መግቢያ እና ለመደምደሚያ ይጠቀማል፤ 146፤ 148-150።

**ሃይማኖት፤** ቃሉ እምነት ማለት ነው። ሃይማኖት በአሁኑ አነጋገር የነገረ መለኮትን ትምህርት፥ የአምልኮትን ሥርዓት፥ ከእምነትም የተነሣ የሰውን አካሄድ ያጠቃልላል። የሃይማኖት መሠረት የሰው ምርምር ሳይሆን የእግዚአብሔር የራሱ በተፈጥሮና በመጽሐፍ ቅዱስ መገለጥ ነው። ለዚህም መገለጥ ሰው የሚሰጠው ተገቢ የሆነ የአፀፋ ምላሽ ማመንና መታዘዝ ነው፤ 2ጢሞ. 4፥7፤ ይሁዳ 3:20፤ 1ቆሮ. 2፥11-16። «እምነት» ይመ.

**የሃይማኖት ውሳኔ፤** በአጭር የተጠቃለለ የክርስቲያን ሃይማኖት ሥርዓት። ከመጀመሪያ ጀምሮ ሐዋርያት ወንጌልን አስተማሩ፤ የተወሰነ ትምህርትም ሰጡ። ይህም ትምህርት «የሐዋርያት ትምህርት» ተባለ፤ ሐ.ሥ. 2፥42፤ ሮም 6፥17:18፤ 1ጢሞ. 4፥6፤ ቲቶ 1፥9። ትምህርቱንም በተወሰኑ ቃላት ሊያስተምሩ ጀመሩ። በዚህም ዓይነት አይሁድ አስተምረው ነበር፤ ዘዳ. 6፥4:5። በልዩ ልዩ ጥቅሶች ሐዋርያት በተወሰኑ ቃላት እንዳስተማሩ ይታያል፤ ለምሳሌ 1ቆሮ. 12፥4-6፤ 15፥3:4፤ ፊል. 2፥5-11፤ 1ጢሞ. 3፥16።

የቤ.ክ. አባቶች ስሕተትን ለመቃወም ሃይማኖትን ወሰኑ። ከጥንት የታወቁ የሃይማኖት ውሳኔዎች የሚከተሉት ናቸው ፦

1. የሐዋርያት የሃይማኖት ውሳኔ (ጸሎተ ሃይማኖት)፤ ይህ የሐዋርያትን ትምህርት ይይዛል እንጂ በሐዋርያት አልተጻፈም።

2. የኒቅያ ጸሎተ ሃይማኖት።

3. ጸሎተ ሃይማኖት ዘአፍራቅያ (ዘአፍሪቃ)። ይህ በቅዱስ አትናቴዎስ የተዘጋጀ ነው ይባላል። ከዚያም

ወዲህ የመጀመሪያዎቹን መሠረተ አሳቦች ሳይለቁ ልዩ ልዩ የሃይማኖት ውሳኔዎች ተዘጋጅተዋል።

**ሄልዮቱ፤** በግብፅ አገር ፀሐይ ይመለክበት የነበረ ከተማ፤ ዘፍ. 41፥45፤ ኤር. 43፥13፤ ሕዝ. 30፥17። ሄልዮቱ የነበረበት አሁን የካይሮ ከተማ ካለበት ዐሥራ አምስት ኪ.ሜ. ይርቃል።

**ሄርሜን፤** በግሪክ ሃይማኖት የዋናው አምላክ የድያ ጓደኛና መልእክተኛ ተብሎ ይታመንበት የነበረ አምላክ ነው፤ ሐ.ሥ. 14፥12:13።

**ሄሮድስ፤** ከኤዶም ዘር የተገኙ ቤተሰቦች ስም ነው። እነዚህ ቤተሰቦች የአይሁድን ሃይማኖት ተቀብለው ከ47 ከክ.በ. እስከ 79 ዓ.ም. («ዓመት» ይመ.) በአይሁድ አገር ነገሥታትና ገዥዎች ሲሆኑ የማስተዳደር ችሎታ ነበራቸው። ነገር ግን ከሌላ ዘር በመሆናቸው፥ ብዙ ብልግናም በመሥራታቸው፥ ሥልጣናቸውንም ከሮም መንግሥት ስለተቀበሉ በአይሁድ ዘንድ ተወዳጅነት አልነበራቸውም። ሆኖም በአይሁድ መካከል የሚገኝ «የሄሮድስ ወገን» የሚባል ክፍል ግዛታቸውን ደገፈ፤ ማር. 3፥6፤ 12፥13-17።

መ.ቅ. ከዚህ ቤተሰብ መካከል የሚከተሉትን ዘጠኝ ሰዎች ስም ይጠቅሳል :-

1. ታላቁ ሄሮድስ፤ የአይሁድ ንጉሥ ሆኖ በ37 ከክ.በ. ነገሠ። በእስራኤል አገር ያለውን የቂሣርያ ከተማ ቈረቈረ፤ ቤተ መቅደሱን ማሳደስና ማስጌጥ ጀመረ፤ ሕፃናትንም አስገደለ፤ ማቴ. 2፥1-18። ዐሥር ሚስቶችን አገባ፤ ከቤተሰቡና ከዚያም ውጭ ብዙ ሰዎችን ፈጀ። ከሞተ በኋላ መንግሥቱ ለልጆቹ በሦስት ተከፈለ። ታላቁ ሄሮድስ የሞተበትን ዓመት መወሰን አስቸጋሪ ስለሆነ «ዓመት» የተመዘገበበትን ርእስ ይመ.




የታላቁ ሄሮድስ ገንዘብ በ1ኛው ገጽ የራስ ቍር፥ በሌላው ጋሻ

2. አርኪላዎስ፤ የታላቁ ሄሮድስ ልጅ እስከ 6 ዓ.ም. ይሁዳን ገዛ፤ ማቴ. 2፥22።




የሄሮድስ አርኪላዎስ ገንዘብ በ1ኛው ገጽ የወይን ዘለላ፥ በሌላው የራስ ቍር

3. ሄሮድስ ፊልጶስ፤ የታላቁ ሄሮድስ ልጅ፤ ማቴ. 14፥3።

4. ሄሮድስ አንቲጳስ፤ የታላቁ ሄሮድስ ልጅ እስከ 39 ዓ.ም. ገሊላን ገዛ። የወንድሙን የሄሮድስ ፊልጶስን ሚስት አገባ። መጥምቁ ዮሐንስ ስለዚህ ቢገሥጸው አሰረው፤ በሰይፍ አስቈርጦም አስገደለው፤ ማቴ. 14፥1-12። ኢየሱስ ቀበሮ ብሎ በመጥራቱ ጠባዩን ገለጠ፤ ሉቃ. 13፥32። ጲላጦስ ኢየሱስን ሲልክለት ሄሮድስ በመናቅ ዘበተበት፤ ሉቃ. 23፥6-12።




የሄሮድስ አንቲጳስ ገንዘብ በ1ኛው ገጽ የዘንባባ ዝንጣፊ፥ በሌላው የአበባ አክሊል

5. ሄሮድያዳ፤ የአርስቶቡሎስ ልጅ የታላቁ ሄሮድስ የልጅ ልጅ በመጀመሪያ አጐትዋን ሄሮድስ ፊልጶስን፥ ቀጥሎም ሄሮድስ አንቲጳስን አገባች። መጥምቁ ዮሐንስን አስገደለች፤ ማቴ. 14፥3-12።

6. ፊልጶስ፤ የታላቁ ሄሮድስ ልጅ እስከ 34 ዓ.ም. ኢጡርያስንና ጥራኮኒዶስን ገዛ፤ ሉቃ. 3፥1።

7. ንጉሥ ሄሮድስ ቀዳማዊ አግሪጳ የአርስቶቡሎስ ልጅ የታላቁ ሄሮድስ የልጅ ልጅ ከ41-44 ዓ.ም. ይሁዳን ገዛ። ሐዋርያው ያዕቆብን ገደለ፤ ጴጥሮስንም አሰረ። የጌታ መልአክ ግን ጴጥሮስን አዳነ፤ ንጉሡም በመልአኩ ተቀሥፎ ሞተ፤ ሐ.ሥ. 12።




የቀዳማዊ ሄሮድስ አግሪጳ ገንዘብ በ1ኛው ገጽ ጃንጥላ፥ በሌላው ገብስ

8. ንጉሥ ሄሮድስ ዳግማዊ አግሪጳ፤ የሄሮድስ ቀዳማዊ አግሪጳ ልጅ ከ50 ዓ.ም. ጀምሮ ገሊላን ገዛ። ጳውሎስ በፊቱ ተከሶ ቀርቧል፤ ሐ.ሥ. 25፥13-26፥32።

9. በርኒቄ፤ የንጉሥ ሄሮድስ ቀዳማዊ አግሪጳ ልጅ። አጐትዋን ካገባች በኋላ ከወንድምዋ ከሄሮድስ ዳግማዊ አግሪጳ ጋር ዝሙት እየፈጸመች ኖረች፥ ጳውሎስም ሲከሰስ ከወንድምዋ ጋር ተሰየመች፤ ሐ.ሥ. 25፥23፤ 26፥30።

**የሄሮድስ ቤተሰብ የትውልድ ሐረግ፤** ይህ የትውልድ ሐረግ ዋና ዋና ሰዎችን እንጂ ሁሉን አያሳይም።




**ሄሮድያዳ፤** «ሄሮድስ» ይመ.

**ሄኖም፤** ከጥንታዊው የኢየሩሳሌም ከተማ በምዕራብና ደቡብ ያለ ሸለቆ (ኢያሱ 15፥8)፤ የይሁዳና የብንያም ድንበር ነው። ጣዖትን የሚያመልኩ ነገሥታት ይሠውበት ነበርና ኢዮስያስ አረከሰው፤ 2ነገ. 23፥10-14። የኢየሩሳሌም ቆሻሻ መጣያ ሆነና ቆሻሻው ሁልጊዜ በእሳት ሲቃጠል ይታይ ነበር። የኃጢአተኛ መቅጫ ቦታን ለመግለጥ የተለመደ ምሳሌ ሆነ። ሄኖም በዕብራይስጥ ቋንቋ ሲሆን፥ በግሪክ ግን ገሃነም ይባላል። ሄኖም የአቅኚው ሰው ስም ነው።

**ሄኖን፤** ምንጮች ማለት ነው። በዮርዳኖስ ወንዝ አቅራቢያ ከቤትሳን ወደ ደቡብ ያለ ቦታ። መጥምቁ ዮሐንስ ብዙ ገሊላውያንን በዚህ ቦታ አጥምቋል፤ ዮሐ. 3፥23።

**ሄኖክ፤** የያሬድ ልጅ፤ ዘፍ. 5፥18። በይሁዳ መልእክት ቍ.14 ላይ «ከአዳም ጀምሮ ሰባተኛ የሆነ» ተብሏል። አካሄዱን ከእግዚአብሔር ጋር አደረገ የሚል ቃልም ተጽፎለታል፤ ዘፍ. 5፥22። በእግዚአብሔር አመራር ሥር የኖረ ሰው ነበረ፥ ይኸውም በሕይወቱ ከእግዚአብሔር ጋር አንድነት ነበረው፤ አካሄዱንና አረማመዱን እንደ እግዚአብሔር ቃል አደረገ ማለት ነው። በእምነቱ እግዚአብሔርን ደስ እንዳሰኘ ተመሰከረለት፤ ዕብ. 11፥5። በእግዚአብሔር ያመነ፥ እንደ ፈቃዱ የኖረ ሰው በመሆኑ ሄኖክ በሥጋ (ሞትን ሳያይ) ከዚህ ዓለም ተለየ። በሕይወቱ እንዳለ እግዚአብሔር ወደ ራሱ ወሰደው፤ ዘፍ. 5፥24።

**ሄኖክ፥ መጽሐፈ ሄኖክ፤** ሄኖክ በሰማይ ተሰውሮ ሳለ ስለ መላእክት፥ ስለ መሲሕ፥ ስለ ፀሐይና ጨረቃ እንቅስቃሴ (ዑደት) የተገለጸለትን ነገር የሚተርክ መጽሐፍ ነው። የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤ.ክ. ይህን መጽሐፍ ሄኖክ ራሱ ጽፎታል፥ ይሁዳም ጠቅሶታል በማለት ከብ.ኪ. መጻሕፍት ጋር ቈጥራ ትቀበለዋለች፤ ሌሎች አብ.ክ. መጽሐፉ እጅግ ዘግይቶ የተዘጋጀ ድርሰት ነው በማለት አይቀበሉትም፤ ዘፍ. 5፥21-24፤ ይሁዳ 14። ሄኖክ 1፥9 ይመ.

**ህንደኬ፤** የኢትዮጵያ ንግሥት። ስሙ በዚያ ዘመን የኢትዮጵያ ንግሥታት ሁሉ መጠሪያ ነበር፤ የግብጽ ነገሥታት «ፈርዖን» በሚለው ስም ይጠሩ እንደነበረ ሁሉ የኢትዮጵያም ንግሥታት ህንደኬ ይባሉ ነበር፤ ሐ.ሥ. 8፥27። «ኢትዮጵያ» ይመ.

**ሆ፥ ሆታ፤** የደስታ ድምፅ፤ 2ሳሙ. 6፥15።

**ሆምጣጤ፤** ብዙ ጊዜ የቆየና የኰመጠጠ ወይን ወይም ሌላ የሚያሰክር መጠጥ። መራራነት አለው፤ ጥምንም ያረካል፤ ሩት 2፥14፤ ዮሐ. 19፥29።

**ሆሣዕና፤** አሁን አድን ማለት ነው። የእስራኤል ሕዝብ የዘንባባ ዝንጣፊ ይዘው «ሆሣዕና» (መዝ. 118፥25:26) በማለት እየጮኹ ኢየሱስን ወደ ኢየሩሳሌም ሲገባ አጀቡት፤ ማቴ. 21፥9-15፤ ማር. 11፥9፤ ዮሐ. 12፥13።

**ሆሴዕ፤** የስሙ ትርጉም «እግዚአብሔር ያድናል» ማለት ነው። እንደ ኢያሱ ሁሉ «ኢየሱስ» ከሚለው መጠሪያ ስም ጋር ተመሳሳይ ትርጉም እንዳለው ያሳስበናል፤ ማቴ. 1፥21። 1. ዳግማዊ ኢዮርብዓም በሰማርያ ነግሦ በነበረበት ዘመን በእስራኤል (በሰሜናዊው) መንግሥት ተነሥቶ የነበረ ነቢይ፤ ሆሴዕ 1፥1። 2. ከሰሜናዊው የእስራኤል መንግሥት ነገሥታት የመጨረሻው፥ ከ731-722 ከክ.በ. የነገሠ ንጉሥ። በእርሱ ዘመነ መንግሥት ሰማርያ ወደቀች፤ 2ነገ. 15፥30፤ 17፥1-6፤ 18፥1። በዚህ ስም ሌሎች ሁለት ሰዎች ተጠርተውበታል።

**የሆሴዕ ትንቢት፤** የእስራኤል ነገዶች በሁለት መንግሥታት ተከፍለው ሳሉ ሆሴዕ ከ755 እስከ 725 ገደማ ከክ.በ. ስለ ሰሜናዊው መንግሥት ውድቀት ትንቢት ተናገረ። ዳግማዊ ኢዮርብዓም

ከሞተ በኋላ መንግሥቱ ተዳከማ፥ በ722 ከክ.ቢ. በአሦር እጅ ወደቀች። የእግዚአብሔር ሕዝብ አንድ በመሆኑ ሆሴዕ በትንቢቱ ስለ ይሁዳም ተናግሯል፤ 2፥2። ትንቢት በተናገረበት ዘመን የይሁዳ ነገሥታት ዖዝያን፥ ኢዮአታም፥ አካዝና ሕዝቅያስ ነበሩ፤ 1፥1። በዚያን ዘመን አሞጽ፥ ኢሳይያስና ሚክያስ ትንቢት ይናገሩ ነበር።

የሆሴዕ ዋና መልእክት የእግዚአብሔር የማይለወጥ ፍቅር ሲሆን (2፥23-24፤ 14፥4)፤ ዋና ጥሪው ሕዝቡ እግዚአብሔርን ወደ ማወቅ በመመለስ እንዲድኑ ነው፤ 4፥6፤ 6፥6፤ 13፥4።

አከፋፈል ፡-

1. የሆሴዕ ሚስት የጎሜር ማመንዘር ለእስራኤል መንፈሳዊ አመንዝራነት (ለአምልኮተ ጣዖት) ምሳሌ ሆነ። ሆሴዕም ሚስቱን ወደ እንዲመልሳት ታዝዞ ነበር። እግዚአብሔር እስራኤልን በጽድቅና በምሕረት በገዛ ፈቃዱም ወደደ፤ 1፥1-3:5።

2. እስራኤል ወደ እግዚአብሔር ባይመለስ ከፍርድና ከውድቀት አያመልጥም፤ 4፥1-13:16።

3. ወደ እግዚአብሔር መመለስ ፈውስንና በረከትን ያስገኛል፤ ም.14።

**ሆድ፤** ለመብል ብቻ የሚኖሩ ሆድ አምላካቸው ተብለዋል፤ ፊል. 3፥19። ከባድ አሳብ ከሆድ ይወጣል ወደ ሆድም ይገባል፤ ኢዮብ 15፥35፤ 20፥15፤ ምሳ. 18፥8።

**ለሀፍ፤** የአልጋ ልብስ፥ እንደ ብርድ ልብስም ሊያገለግል ይችላል፤ 2ነገ. 8፥15፤ ምሳ. 7፥16።

**ለማኝ፤** የሙሴ ሕግ ለድሆች ርዳታ እንዲደረግላቸው ያዝዛል። ስለዚህ ለማኞች ብዙ ጊዜ በብ.ኪ. ታሪክ አይገኙም። ሆኖም በክርስቶስ ጊዜ ዕውራን፥ አንካሳዎች ወዘተ... ይለምኑ ነበርና በአ.ኪ. ለማኝን መርዳት ታዟል፤ ግን ለሰነፍ መስጠት አይገባም፤ ማቴ. 5፥42፤ ሉቃ. 14፥12-14፤ 2ተሰ. 3፥10።

**ለምጽ፤** እንደ መ.ቅ. አገላለጥ ቃሉ በሰው ቆዳ ይ የሚታይ ልዩ ልዩ ዓይነት ተላላፊ የቆዳ በሽታን ያመለክታል። ካህናት ለምጽን ለመለየት እንዲችሉ በሙሴ ሕግ መመሪያ ተሰጣቸው። በእስራኤል ዘንድ ለምጻም ከሕዝብ መለየት ነበረበት። ሰዎችም እንዳይቀርቡት «ርኩስ ነኝ» ብሎ ማስታወቅ ነበረበት፤ ዘሌ. 13። ከእሕዛብ ወገን ግን ለምጻም በቤቱ እንዲቀመጥ ይደረግ ነበር፤ 2ነገ. 5፥2:13:18። በእስራኤል ዘንድ ለምጻም ሲፈወስ ልዩ ሥነ ሥርዓትና መሥዋዕት ይደረግ ነበረ፤ ዘሌ. 14፥1-32።

ከለምጻሞች የሚታወቁት፥ የሙሴ እኅት ማርያም (ዘኍ. 12፥10)፥ ንዕማንና ግያዝ (2ነገ. 5)፥ ዖዝያን (2ዜ.መ. 26፥16-23) ስምዖንም ናቸው፤ ማቴ. 26፥6-7። ክርስቶስ ብዙ ለምጻሞችን ፈወሰ፤ ሉቃ. 5፥12-13፤ 7፥22፤ 17፥12-19።

ልብስ ወይም ቤት በተለያየ ምክንያት ሲበሰብስ ለምጽ ይባላል፤ ለሰውም የለምጽ በሽታን ሊያስተላልፍ እንደሚችል ይገመት ነበር። በሙሴ ሕግ ስለ ተበላሸ ልብስና ቤት የተጻፈ የለምጽ ሕግ ነበር፤ ዘሌ. 13፥47-59፤ 14፥33-37።

ዛሬ ለምጽ የሚባለው በሽታና በመ.ቅ. የተገለጠው የበሽታ ዓይነት ቢመሳሰሉም አንድ ዓይነት አይደሉም። ቃሉ ተራው ሕዝብ እንደሚጠቀምበትና እንደ ሳይንስ ሊቃውንት ዕውቀት ልዩ ልዩ በሽታን ሊያመለክት ይችላል። ለምጽ ተላላፊ በሽታ ነውና ጥንቃቄ ማድረግን ይጠይቃል። ነገር ግን በመንፈሳዊ ረገድ ሲታይ ዛሬ እንደሚያረክስ ነገር አይቈጠርም። ማናቸውም በሽታ የኃጢአት ምሳሌ ነው፤ ለምጽም በተለይ ኃጢአት ተላላፊ መሆኑንና ከእግዚአብሔርና ከሰው መለየቱን ያሳያል። ግን ለምጻም ሰው የተለየ ኃጢአት እንደሠራ አይገልጥም። «ርኩስ»፥ «በሽታ» ይመ.

**ለብ አለ፤** በሙቀትና በቅዝቃዜ መካከል ያለ፥ በጣም ያልሞቀ በጣምም ያልቀዘቀዘ። ለብ ማለት የፍቅር፥ የእምነትና የሥራ ድካምን ያመለክታል፤ ራእ. 3፥15:16።

**ለኪሶ፤** ግብጻውያን ነገሥታት የሠሩት ከጌት በስተምሥራቅ በኩል 10 ኪ.ሜ. ርቆ የሚገኝ ጠንካራ ምሽግ። ኢያሱ ድል መታው፤ ኢያሱ 10፥31። ናቡከደነፆር በ587 ከክ.በ. ሌሎች የይሁዳ ከተሞችን ከያዘ በኋላ ለኪሶን ያዘ፤ ኤር. 34፥6:7። ዛሬ ከተማው ተልኤድዱወይር ይባላል።

**ለውዝ፤** ጣፋጭ ፍሬ፥ ቀይና ነጭ አበባ ያለው የኮክን ዛፍ የሚመስል ተክል፤ ዘፍ. 43፥11፤ መክ. 12፥5፤ ኤር. 1፥11። ሙሴ የቤተ መቅደሱን መቅረዝ ሲያሠራ የለውዝ አበባ የመሰለ የጽዋ ጌጥ አስደረገበት፤ ዘጸ. 25፥33-35።



የለውዝ አበባ

**ለውጥ፤** እግዚአብሔር አይለወጥም፥ ፍጥረቱ ግን እየተለወጠ ይሄዳል፤ መዝ. 102፥26፤ ዕብ. 1፥12፤ ያዕ. 1፥17። አማኞች በመለወጥ ላይ ቢገኙም፥ በዓለም መጨረሻ እግዚአብሔር ወዳቀደላቸው ክብር በድንገት በቅጽበተ ዓይን ይለወጣሉ፤ 1ቆሮ. 15፥51:52፤ 2ቆሮ. 3፥18፤ ፊል. 3፥21። «መመለስ»፥ «ቅዱስ» ይመ.

**ሉል፤** «ዕንቍ» ይመ.

**ሉቃስ፤** ስሙ በመ.ቅ. በቆላ. 4፥14፥ በፊልሞና 24 እና በ2ጢሞ. 4፥10 ብቻ የተገለጠ

ሲሆን፥ ቅዱስ ሉቃስ ተወዳጅና ታማኝ የጳውሎስ ረዳት እንደነበረ፥ በሕክምናም እንዳገለገለው ተጠቅሷል። ሉቃስ የግሪክ ስም በመሆኑ በግሪኩ ዓለም የኖረና ከአሕዛብ ወገን እንደነበረም ሊያመለክት ይችላል። የቤ.ክ. አባቶች ሉቃስ 3ኛውን ወንጌልና የሐዋርያትን ሥራ እንደጻፈ ይናገራሉ፤ ከአንዳንዶች በስተቀር ሊቃውንት ሁሉ ይህን ትውፊት ይቀበላሉ። በዚህ መሠረት ሉቃስ ከሐ.ሥ. 16፥10 ጀምሮ «እኛ» እያለ በመጻፉ ከጢሮአዳ ጀምሮ እስከ ሮም ድረስ ከሐዋርያው ጳውሎስ ጋር በወንጌል ሥራ እንደተሳተፈ እናስተውላለን።

ሉቃስ ወዳጁ ለሆነው ቴዎፍሎስ በአክብሮት ሲጽፍ፥ ያሳያቸውን ነገሮች ካዩአቸው የዓይን ምስክሮች አረጋግጦ በብዙ ጥንቃቄ ተርኳል። የአጻጻፉም ዘዴ የተማረና በድርሰት ልዩ ሙያ ያለው ሰው መሆኑን ያሳያል፤ ሉቃ. 1፥1-4፤ ሐ.ሥ. 1፥1-3። ሉቃስ የጻፈው ታሪክ የአርኬኦሎጂ ምርመራ ትክክለኛ መሆኑን ያሳያል። ጳውሎስ በሮም ታስሮ ሳለ «የሐዋርያትን ሥራ» በ64 ዓ.ም. ገደማ ከጻፈው፥ ወንጌሉን ደግሞ ከዚህ በፊት በ62 ዓ.ም. ገደማ የጻፈ ይመስላል። «ቴዎፍሎስ» ይመ.

**የሉቃስ ወንጌል፤** ሉቃስ፥ ቴዎፍሎስና ሌሎች የአሕዛብ ወገኖች ስለ ክርስቶስና ስለ ቤ.ክ. እርግጡን እንዲያውቁ ወንጌሉንና የሐዋርያትን ሥራ ጻፈ፤ 1፥1-4፤ ሐ.ሥ. 1፥1-3:8። ታሪኩን ሲጽፍ ከሮም መንግሥት ፖለቲካና ከአይሁድ ሁኔታ ጋር አዛምዶታል፤ 1፥5፤ 2፥1-2፤ 3፥1-2። የሉቃስ ወንጌል በአቀማመጡ የማርቆስን ወንጌል ቅደም ተከተል በአብዛኛው ሲከተል፥ በተለይ ሦስት ረጃጅም ክፍሎች ተጨምረውበታል፤ እነርሱም፥

ሀ) የቅድስት ድንግል ማርያም ታሪክ፥ የመጥምቁ ዮሐንስ መወለድና የኢየሱስ ልደት (ም. 1 እና 2)፥

ለ) ከገሊላ እስከ ኢየሩሳሌም ድረስ በነበረው ጕዞ የኢየሱስ ትምህርት በተለይም የደጉ ሳምራዊ፥ የጠፋው ልጅ፥ የሀብታሙና የአልዓዛር ... ታዋቂ ምሳሌዎች (9፥51-19፥10)፥

ሐ) ከትንሣኤው በኋላ የኢየሱስ መታየትና ትምህርቱ፥ እንደዚሁም ዕርገቱ (24፥13-53) ናቸው።

ሉቃስ የክርስቶስን አገልግሎት ሲያብራራ በሚከተሉት ነጥቦች ላይ ትኩረት አድርጓል ፦

1. ክርስቶስ ለዓለም ሁሉ መጣ፤ ኢየሱስ በአይሁድ መካከል ቢሠራም ለዓለም ሁሉ እንደመጣ ብዙ ማስረጃዎች አሉ፤ 2፥14:32፤ 3፥3-6 («ሥጋም የለበሰ ሁሉ ...»)፤ 4፥25-27፤ 9፥52፤ 10፥33፤ 17፥16፤ 24፥47።

2. ክርስቶስ ለሰዎች መጣ፤

ሀ) የማቴዎስ ወንጌል ምሳሌዎች የእግዚአብሔርን መንግሥት ምንነት ሲያብራሩ፥ ሉቃስ የመረጣቸው ምሳሌዎች ግን በአብዛኛው ለሰዎች ትኩረት ይሰጣሉ። ይህም እጅንእት በካህኑ ዘካርያስ፥ በቅድስት ድንግል ማርያምና በዘመድዋ ኤልሳቤጥ (ም. 1 እና 2)፥ በእኅትማማቾቹ በማርያምና በማርታ (10፥38-42)፥ በቀራጩ ዘኬዎስ (19፥1-10)፥ በሐዘን ላይ በነበሩት በቀለዮጳና በጓደኛው (24፥13-35) ታሪኮች ይታያል።

ለ) ክርስቶስ ከኅብረተሰብ ውጭ ለሆኑትና ለተናቁት ሰዎች ርኅራኄውን ማሳየቱን ይገልጣል፥ በከተማ ትኖር ለነበረች ኃጢአተኛ ሴት (7፥36-50)፥ ለቀራጩ ዘኬዎስ (19፥5:8-10)፥ ለተሰቀለው ወንበዴ (23፥39-43) እና ለሳምራውያን (9፥52-56፤ 10፥33፤ 17፥16)።

ሐ) ሴቶች በክርስቶስ አገልግሎት የነበራቸው ድርሻ በዚህ ወንጌል ከፍ ያለ ስፍራ ተሰጥቶታል። በተለይም በልደቱ (1፥39-56)፥ በአገልግሎቱ (8፥1-3) በሕማማቱ (23፥27-31:49:55) እና በትንሣኤው፤ 24፥1-11። በሌሎች ወንጌሎች ያልተጠቀሱ 13 ሴቶች በሉቃስ ወንጌል ተጠቅሰው ይገኛሉ። ይህ ወንጌል ለልጆችም የተለየ ስፍራ ይሰጣል፤ 7፥12፤ 8፥42፤ 9፥38፤ 18፥15።

መ) ክርስቶስ በልዩ ልዩ ሰዎች ቤት ተጋብዞ ምግብ እንደበላ ተመዝግቧል፥ ከፈሪሳውያን ጋር (7፥36-50፤ 11፥37-44፤ 14፥1-4)፥ በቢታንያ (10፥38-42)፥ በኢያሪኮ (19፥1-10) እና በኤማሁስ (24፥13-32)።

ሠ) በወንጌል ደስታ እንደሚገኝ ያሳያል፤ 1፥14:44:47፤ 6፥21:23፤ 15፥7:10:23:32፤ 24፥52-53። አራቱ የምስጋና መዝሙሮች ተመዝግበው የሚገኙት በዚህ ወንጌል ብቻ ነው፤ 1፥46-55:68-79፤ 2፥14:29-32።

ረ) የሀብታምነትና የድህነት ሁኔታና ውጤት በብዙ ምሳሌዎች ተብራርቷል፥ በተለይ በሁለት አበዳሪዎች (7፥41-43)፥ በሰነፍ ሀብታም (12፥15-21)፥ በግንብ ሠሪ (14፥28-30)፥ በመጋቢ (16፥1-9)፥ በሀብታሙና በአልዓዛር (16፥19-31)፥ በምናን (19፥11-27)። ገንዘብን በተመለከተም የሚከተሉትን ጥቅሶች ይመ.፤ 1፥53፤ 3፥13-14፤ 6፥20-24፤ 14፥12-14፤ 16፥14።

3. ክርስቶስ ለተከታዮቹ ምሳሌ ለመሆን መጣ። ይህም የሚታየው በተለይ ፦

ሀ) በጸሎት፤ ታላላቅ ተግባራትን ከመፈጸም ጋር ክርስቶስ 9 ጊዜ እንደጸለየ ተመዝግቧል፤ 3፥21፤ 5፥15-16፤ 6፥12፤ 9፥18-22:29፤ 10፥17-21፤ 11፥1፤ 22፥39-46፤ 23፥34:46። ሦስት ምሳሌዎች ስለ ጸሎት ያስተምራሉ፤ 11፥5-13፤ 18፥1-8:9-14። ደቀ መዛሙርትንም ብዙ ጊዜ እንዲጸልዩ መክሯቸዋል፤ 6፥28፤ 11፥2-4፤ 22፥40-46።

ለ) በመንፈስ ቅዱስ ምሪት፤ 4፥1:14:17-19፤ 10፥21። የመንፈስ ቅዱስ ኃይል ለተከታዮቹ ያስፈልጋል፤ 3፥16፤ 11፥13፤ 24፥49።

በአራቱ ወንጌሎች ከተጠቀሱት 36 ተአምራት ውስጥ ሉቃስ 21ዱን በመመዝገብ ክርስቶስ በአጋንንት፥ በበሽታ፥ በተፈጥሮና በሞት ላይ ሥልጣኑን ገልጧልና እርሱ «ጌታ» በመሆን የእግዚአብሔር የባሕርይ ልጅ ነው፤ 1፥35:43፤ 2፥11፤ 3፥3-5፤ 4፥8:12፤ 20፥13: 41-44፤

24፥49። ይህም ቢሆን ሉቃስ፥ ኢየሱስ በሰዎች መካከል በመመላለሱ በተለይ ሰው በመሆኑ ላይ ያተኩራል፤ ይህም ከዚህ በላይ እንደተመለከትነው በወንጌሉ አገላለጥ፥ የትውልድ ሐረጉ እስከ አዳም ድረስ በመጠቀሱ (3፥23-38) እና ከትንሣኤ በኋላ በሰውነቱ የሆነውን በመመዝገቡ ላይ በግልጥ ይታያል፤ 24፥30:37-43።

የሰው ልጅ የጠፋውን ሊፈልግና ሊያድን መጣ፤ 19፥10። ተልእኮውን ሲደመድም በሙሴ፥ በነቢያት በመዝሙራትም መሠረት መከራ እንደሚቀበል፥ እንደሚሞትና እንደሚነሣ፥ ከዚያም ወደ ክብሩ ገብቶ የአባቱን ተስፋ ለደቀ መዛሙርቱ እንደሚሰጥ ነገራቸው። ይህንም ኃይል ተቀብለው በስሙ ንስሓንና የኃጢአት ይቅርታን ወንጌል ለዓለም ሁሉ እንደሚሰብኩ ከተናገረ በኋላ እነርሱን ባርኮ ወደ ሰማይ ዐረገ፤ 24፥44-53።

አከፋፈል :-

1. መግቢያ፤ 1፥1-4
2. የጌታ ይፋ አገልግሎት ዝግጅት፤ 1፥5-2፥52
3. የጌታ ይፋ እንቅስቃሴና ትምህርቱ፤ 3፥1-4፥13
4. ጌታ በገሊላ ማስተማሩ፤ 4፥14-9፥50
5. ጌታ ወደ ኢየሩሳሌም መሄዱ፤ 9፥51-19፥48
6. ጌታ በኢየሩሳሌም ማስተማሩ፥ መያዙና መሰቀሉ፤ መቀበሩም፤ 20፥1-23፥56
7. የጌታ ትንሣኤ፥ እንደገና መታየቱ፥ ማስተማሩና ዕርገቱ፤ 24፥1-53።

**ሉድ**፤ 1. የሴም ልጅ፤ ዘፍ. 10፥22። 2. የአገር ስም፤ ብዙ ሊቃውንት የአሁኑ ሊቢያ ነው ይላሉ፤ ኢሳ. 66፥19፤ ኤር. 46፥9።

**ሊቀ ካህናት**፤ ካህናትን የሚቈጣጠር የካህናት አለቃ። ይህ ማዕርግ በመጀመሪያ ለአሮን፥ በኋላም ከአሮን ቤተሰብ ለዋናው ተሰጠ። በመጀመሪያ ጊዜ አልቅናው እስከ ሞት ድረስ ነበረ፤ በኋላ ግን ነገሥታት እንደፈለጉ ሊቃነ ካህናትን ይሾሙና ይሽሩ ነበር። በክርስቶስ ጊዜም እንደነሐና ያሉ በሮም መንግሥት የተሾሙ ሊቃነ ካህናት ነበሩ፤ 1ነገ. 2፥26፤ ሉቃ. 3፥2። የሊቀ ካህናቱ ልብሶች በዕውቅ (በልዩ ዓይነት) የተሠሩ ነበሩ። እነርሱም :- ኡሪምና ቱሚም የተቀመጡበት የደረት ኪስ፥ ኤፉድ፥ ቀሚስ፥ ዝንጕርጕር ሽሚዝ፥ መጠምጠሚያ፥ «ቅድስና ለእግዚአብሔር» የሚል የተቀረጸበት የወርቅ አክሊልና መታጠቂያ ናቸው፤ ዘጸ. 28፥1-39 ይመ.

አሮን ሲሾም ሙሴ እንዲያለብሰው፥ በዘይትም እንዲቀባው ታዘዘ፤ ዘጸ. 29፥1-9። ሊቀ ካህናት ቤተ መቅደስን ያስተዳድራል፥ ካህናትንም ይቈጣጠራል፤ 1ሳሙ. 3፥12:13፤ 2ነገ. 12፥7፤ 22፥4። በሸንጎም ላይ ሊቀ መንበር ይሆን ነበር፤ ማቴ. 26፥57-65። ሊቀ ካህናት በማስተሰረያ ቀን ልዩ መሥዋዕት ለሕዝብ ያቀርባል፥ በዚህም ቀን ብቻ ወደ ቅድስተ ቅዱሳን ገብቶ በታቦቱ ላይ ደም ይረጫል፤ ዘሌ. 16። «የማስተሰረያ በዓል» ይመ.

አሁን የብ.ኪ. የሊቀ ካህናት ሥራ ቀርቷል። ክርስቶስ የአ.ኪ. ሊቀ ካህናት በመሆን ራሱን አንድ ጊዜ ሠውቶ ወደ ሰማያዊት መቅደስ ገብቷልና፤ ዕብ. 9፥1-28፤ 10፥12-21። «ካህን»፥ «የቤተ ክርስቲያን አስተዳደር» ይመ.



ሊቀ ካህናት ልብሰ ተክህኖ እንደለበሰ

**ሊቃኦንያ**፤ በትንሹ እስያ መካከል የምትገኝ ሜዳማ ቀበሌ። ጳውሎስ የጐበኛቸው ልስጥራንና ደርቤን የሊቃኦንያ ከተሞች ነበሩ፤ ሐ.ሥ. 14፥6:11። ዛሬ በቱርክ አገር ውስጥ ትገኛለች። ካ.6በ።

**ሊቅ፥ ሊቃውንት**፤ በትምህርት ወይም በሥልጣን ከፍተኛ ደረጃ ያለው ታላቅ ምሁር። ክርስቶስ ደቀ መዛሙርቱን ሊቃውንት ተብለው እንዳይጠሩ አስጠነቀቃቸው፤ ማቴ.23፥10።

**ሊቢያ**፤ በሰሜን አፍሪቃ ከግብጽ በስተምዕራብ የምትገኝ አገር፤ ዳን. 11፥43፤ ሐ.ሥ. 2፥10። ቀሬና የሊቢያ ከተማ ነበረች። ካ 7በ።

**ሊባኖስ**፤ ከገሊላ በስተሰሜንና ከፊንቄ በስተምሥራቅ ያለው ተራራማ አገር፤ ዘዳ. 1፥7። ዋናው የሊባኖስ ተራራ አርሞንዔም ነው፤ ኢያሱ 13፥5። ሊባኖስ በዝግባ ዛፍ የታወቀ ነበርና ሰሎሞን ለቤተ መቅደሱ ሥራ ከዚያ ያስመጣ ነበር፤ 1ነገ. 4፥33፤ 5፥6:9። የሊባኖስ ዝግባ የመንፈሳዊ ክብር እድገትን (መዝ. 92፥12) ኩራትን በምሳሌነት ያመለክታል፤ ኢሳ. 2፥12-16።

**ላሜሕ**፤ 1. በቃየል ትውልድ በኩል ከአዳም

ሰባተኛ ሆና የያባል፥ የዮባል፥ የቱባልቃይንና የናዕማ አባት ነበር። ባለ ሁለት ሚስቶች ከሆኑት መጀመሪያው ነበር። ሰው ገድሎ ፎከሯል፤ ዘፍ. 4፥18-24። 2. በሴት ትውልድ በኩል ተወልዶ የማቱሳላ ልጅ የኖኅ አባት ላሜሕ ይባል ነበር፤ ዘፍ. 5፥25:28-31።

**ላሽ**፤ ሚለጠ፥ ላላ፥ የምላሱ፥ የወፍጮ ስለቱ ሲበርድ ላሽ ይባላል። የወፍጮ መላሸት የደከመ ድምፅ ምሳሌ ነው፤ መክ. 12፥4።

**ላባ**፤ የአብርሃም ወንድም የናኮር ልጅ የባቱኤል ልጅ፥ የርብቃ ወንድም ነበር፤ ዘፍ. 11፥29፤ 22፥20-23፤ 24፥24:29። ርብቃ የይስሐቅ ሚስት እንድትሆን ፈቀደ፤ ዘፍ. 24፥50-60። የእኅቱ ልጅ ያዕቆብን ተቀበለው፤ ልጆቹንም ልያንና ራሔልን ለሚስትነት ሰጠው፤ ዘፍ. 29፥13-30። ያዕቆብ ሃያ ዓመት እያገለገለው አስቀድሞ በሚስቱ ጉዳይ (ቍ. 25) በኋላም በደመወዙ ያታልለው ነበር፤ ዘፍ. 30፥27-36፤ 31፥7። ያዕቆብም በሸሸው ጊዜ እግዚአብሔር፥ ሳይጐዳው እንዲያሰናብተው ላባን አስጠንቀቀው፤ 31፥22-55።

**ላት**፤ የበግ ጅራት። ስብ ይበዛበታል፤ በብ.ኪ. ከሚቃጠለው መሥዋዕት አንዱ ክፍል ላት ነበር፤ ዘጸ. 29፥22፤ ዘሌ. 3፥9።

**ላይ፥ በላይ፥ ከላይ**፤ የታች፥ በታች፥ ከታች ተቃራኒዎች ሲሆኑ፥ ስለ ማዕረግ እንደዚሁም ስለ መንፈሳዊ ሁኔታዎች ሊያመለክቱ ይችላሉ። እግዚአብሐር በየትም ስፍራ የሚገኝ ቢሆንም (መዝ. 139፥7-10)፥ በሥልጣን፥ በክብርና በኃይል ከሁሉ በላይ ሆኖ በስፍራ ደግሞ ከሰው በላይ እንዳለ እንዲታሰብ ተገልጧል፤ ዳን. 7፥13፤ ሐ.ሥ. 1፥9፤ ኤፌ. 1፥21።



የሊባኖስ ዝግባ

**ላጬ**፤ ካህናትና ናዝራውያን ጠጕራቸውን መላጨት አይፈቀድላቸውም፤ ዘሌ. 21፥5፤ ዘኍ. 6፥5። ሰዎች ለሞት ሰው ሲያዝኑ (ኢዮብ 1፥20)፥ ናዝራዊ ሲረክስ (ዘኍ. 6፥9)፥ ሌዋዊ ለክህነት ሲቀርብ (ዘኍ. 8፥7)፥ ለምጻም ሲነጻ (ዘሌ. 14፥8) ለውርደትም ምልክት ይላጩ ነበር፤ 2ሳሙ. 10፥4።

**ሌሊት**፤ ከፀሐይ መግቢያ እስከ መውጫ በጥንት ጊዜ በሦስት (መሳ. 7፥19)፥ በክርስቶስ ጊዜ በአራት ክፍል ይከፈል ነበር፤ ማር. 6፥48።

**የሌሊት ቍር**፤ የሌሊት ብርድ፤ የቀን ሐሩር ተቃራኒ፤ ዘፍ. 31፥40።

**የሌሊት ወፍ**፤ እንስሳት ይመ.



የሌሊት ወፍ

**ሌባ**፤ በቀንና በሌሊት ሌባን ስለ መያዝ ልዩ ሕግ ነበረ፥ ሲያዝም ደግሞ ቅጣቱ እንደሰረቀው ነገር እየታየ ይወሰን ነበር፤ ዘጸ. 22፥1-4፤ ዘዳ. 24፥7። ሌባ በተራበ ጊዜ ምግብ ቢሰርቅ ሰዎች ቢያዝኑለትም እንኳ ቅጣቱ አይቀርለትም ነበር፤ ምሳ. 6፥30:31። ሌቦች የእግዚአብሔርን መንግሥት አይወርሱምና በክርስቶስ ሲያምኑ ሌብነታቸውን ትተው በገዛ እጃቸው ሠርተው ለራሳቸውና ለሌሎች እንዲደክሙ ታዝዘዋል፤ 1ቆሮ. 6፥10፤ ኤፌ. 4፥28። የሌባ ድንገተኛ አመጣጥ ለክርስቶስ ዳግም ምጽአት ምሳሌ ሆኗል፤ 1ተሰ. 5፥4፤ 2ጴጥ. 3፥10።

**ሌዊ፥ ሌዋውያን**፤ ስሙ «ይጠጋል» ማለት ነው። ልያ ለያዕቆብ የወለደችለት ሦስተኛ ልጅ፤ ዘፍ. 29፥34። በእኅቱ በዲና ምክንያት ከወንድሙ ከስምዖን ጋር የሴኬምን ሰዎች ገደለ፤ ዘፍ. 34፥25:30:31፤ 49፥5-7። ሌዊ ከእስራኤል ነገዶች የአንዱ አባት ሆነ፥ በስሙም ነገደ ሌዊ (ሌዋውያን) ተብሎ ተሰየመ፤ ዘፍ. 46፥11። በሙሴ ዘመን የሌዊ ልጆች በረከትን አገኙ፤ ዘጸ. 32፥25-29፤ ዘዳ. 33፥8-11። ሙሴና አሮን ከሌዊ ነገድ ነበሩ፤ ዘጸ. 2፥1፤ 6፥16-27። የአሮን ልጆች ለክህነት፥ ሌዋውያንም ሁሉ ለእግዚአብሔር አገልግሎት ተለዩ። የሌዋውያን ሥራና አገልግሎት በኦሪት ዘሌዋውያን ተገልጧል። በከነዓን የርስት ድርሻ ሳይሆን 48 ከተሞች ተሰጡአቸው፤ የእስራኤልም ልጆች አሥራት ርስታቸው ሆነ፤ ዘኍ. 18፤ ኢያሱ 21። «ነገድ» ይመ.

**ሌጌዎን**፤ ጭፍራ ማለት ነው። በሮም የጦር ሠራዊት ዋናው ክፍለ ጦር ሌጌዎን ይባል ነበር። በአንድ ሌጌዎን ውስጥ እስከ ስድስት ሺህ እግረኞችና ፈረሰኞች ነበሩ፤ ማር. 5፥9።

**ሌጦ**፤ ከበግና ከፍየል ከሌላም እንስሳ ቆዳ የሚሠራ ዐጽፍ። መናንያን ይለብሱታል፤ ሌጦ ዓለምን የመናቅ ምልክት ነው፤ ዕብ. 11፥37።

**ልመና፤** በጸሎት የምንጠይቀው ነገር ሁሉ ልመና ይባላል። «ጸሎት» ይመ.

**ልሙኤል፤** በምሳ. 31፥1 «የማሣ ንጉሥ» ተብሎ በቍ. 2-9 የሚገኘውን የእናቱን ትምህርትና ምክር ያስታወቀ ነበረ። ከዚህ በቀር ስለ እርሱ የሚታወቅ ነገር የለም። የአይሁድ ሊቃውንት ሰሎሞን ራሱ ነው ይላሉ።

**ልሳን፤** የሚከተሉትን አሳቦች ይገልጣል፤ አንደበትን፥ ቋንቋን (1ቆሮ. 14፥26)፥ የባሕር ሰላጤን (ኢያሱ 15፥2)፥ የእሳት ላንቃን፤ ሐ.ሥ. 2፥3።

**በልሳን መናገር፤** ደቀ መዛሙርትና ሌሎች ሰዎችም በበዓለ ኀምሳ ቀን በአዲስ ልሳን ተናገሩ፥ ይህም የሆነው መንፈስ ቅዱስ በሞላባቸው ጊዜ ነው፤ ሐ.ሥ. 2፥1-21። ወንጌል ወደ አሕዛብ ለመድረሱ ማረጋገጫ እንዲሆን ይህ ስጦታ ተሰጠ፤ ሐ.ሥ. 10፥44-47፤ 11፥15። ደግሞም በኤፌሶን ለነበሩት ለዮሐንስ ደቀ መዛሙርት ተሰጠ፤ ሐ.ሥ. 19፥6።

ሐዋርያት በበዓለ ኀምሳ ቀን ሰሚዎች በሚያስተውሉት ልሳን (ቋንቋ) ተናገሩ፤ በቆሮንቶስ ግን ሰሚዎች እንዲያስተውሉ ከመንፈስ ቅዱስ የሚገኝ የመተርጐም ስጦታ ያለው ሰው አስፈላጊ ሆነ።

በቆሮንቶስ ቤ.ክ. በልሳን ስለ መናገር ብዙ ጥያቄ ተነሥቶ ስለነበረ፥ ጳውሎስ በ1ቆሮ. 12፥10-11:28-30 እና በም. 14 ላይ ለችግሩ የበኩሉን መፍትሄ ሰጥቷል።

አንዳንዶች በመ.ቅ. የእግዚአብሔር መገለጥ አንድ ጊዜ ፈጽሞ ስለተሰጠና በልሳን መናገር የመገለጥ ስጦታ በመሆኑ ዛሬ አይሠራም ይላሉ። ሌሎች ግን ጳውሎስ እንደተናገረው በሥርዓት እስከተደረገ ድረስ የልሳን ስጦታ አሁንም አለ ይላሉ።

**ልስጥራን፤** በትንሹ እስያ በሊቃኦንያ አገር የነበረች ከተማ፤ ሐ.ሥ. 14፥6። ጳውሎስ በሦስቱ ጕዞዎቹ ልስጥራንን ጐብኝቷል፤ ሐ.ሥ. 14፥6-23፤ 16፥1፤ 18፥23። ከተማዋ አሁን ፈርሳለች፤ ካ. 6በ።

**ልቅሶ፤** አይሁድ ሰው በሞተ ጊዜ የልቅሶ ልማድ ነበራቸው። ለታላላቅ ሰዎች ረጅምና ከፍ ያለ ሥርዓት ይፈጸምላቸዋል፤ ዘፍ. 50፥3:7-11፤ ዘዳ. 34፥5-8፤ 2ዜ.መ. 16፥14። ሙሾ የኀዘን ቅኔ ይቀኙላቸው ነበር፤ 2ሳሙ. 1፥18-27። ሥርዓቱ እንደ ዘመኑ፥ እንደ አገሩ፥ እንደ ቤተሰቡ ነበር። ጾም መጾም (1ሳሙ. 31፥13)፤ ልብስ መቅደድ፥ በራስም ላይ ትቢያን መነስነስ (2ሳሙ. 1፥2)፥ ማቅ መልበስ፥ ራስንም መንጨት (ኢሳ. 22፥12) የተለመደ ነበር። ሆኖም እስራኤል የከነዓናውያንን ልማድ እንዳይከተሉ ተከልክለዋል፤ ዘሌ. 19፥27:28፤ ዘዳ. 26፥14። አስለቃሾች ይቀጠሩ ነበር (ኤር. 9፥17-18)፥ ኢየሱስ ግን አልተደሰተባቸውም፤ ማቴ. 9፥23-25። ኢየሱስ እውነተኛውን የኀዘን ምልክት በአልዓዛር ሞት ጊዜ ገልጧል፤ ዮሐ. 11፥35:36። ምእመናን ተስፋ እንደሌላቸው በማሰብ ማዘን አይገባቸውም፤ በክርስቶስ የሞቱት ከክርስቶስ ጋር ናቸው፤ ወደፊትም ይነሣሉና፤ 1ቆሮ. 15፤ ፊል. 1፥21-24፤ 1ተሰ. 4፥13-18። «መቃብር» ይመ.

**ልብ፤** በመ.ቅ. አሳብ ልብ የሕይወት መውጫ ነው፤ ምሳ. 4፥23፤ 23፥7። ልብ አእምሮን (ዳን. 4፥16፤ 7፥4)፥ ፈቃድን (ማር. 3፥5)፥ አሳብን (ማር. 2፥6:8) ስሜትንም ያጠቃልላል፤ ሉቃ. 24፥32። ሰው በፍጹም ልቡ እግዚአብሔርን እንዲወድ ታዝዟል፤ ማር. 12፥30።

የሰው ልብ ክፉ ነው፤ ምሳ. 26፥25፤ ኤር. 17፥9፤ ማር. 7፥21-23። እግዚአብሔርም የሰው ልብ ክፉ በመሆኑ የእስራኤላውያን ልብ እንዲገረዝ አዝዟል፤ ዘዳ. 10፥16-17፤ 30፥6። ስለዚህም ሰው ወደ እግዚአብሔር እንዲደርስ ትእዛዙንም እንዲጠብቅ የተሰበረና የታደሰ የነጻም ልብ ያስፈልገዋል፤ መዝ. 51፥17፤ ኤር. 31፥31-34፤ ሕዝ. 36፥25-28፤ ማቴ. 5፥8፤ ሮም 12፥2፤ ኤፌ. 3፥16። «መመለስ» ይመ.

**ልብሰ ተክህኖ፤** በጸሎትና በቅዳሴ ጊዜ ካህን የሚለብሰው የክህነት ልብስ። ካህናት በቤተ መቅደስ ሲያገለግሉ የሚለብሱት ማንኛውም ልብስ ሁሉ በአጠቃላይ ልብሰ ተክህኖ ተብሎ ይጠራል፤ ዘጸ. 31፥10።

**ልብስ (አልባሳት)፤** 1. የልብስ ዓይነት ፦ ማቅ (ዘፍ. 37፥34)፥ ቀይ ግምጃ (ምሳ. 31፥22)፥ ቁርበት ወይም ቆዳ (ዘፍ. 3፥21፤ 2ነገ. 1፥8)፥ የበግ ጠጕር (ሕዝ. 44፥17)፥ በፍታ (መሳ. 14፥12)፥ የተልባ እግር (ሕዝ. 44፥17)፥ የግመል ጠጕር፤ ማቴ. 3፥4።

2. የወንዶች ልብስ ፦ መታጠቂያ (1ሳሙ. 18፥4)፥ መደረቢያ (1ሳሙ. 2፥19)፥ መጐናጸፊያ (ዳን. 3፥21)፥ ሰናፊል (ዳን. 3፥21)፥ ቀሚስ (ምሳ. 31፥24)፥ እጀ ጠባብ (ዮሐ. 19፥23)፥ ካባ (ኢያሱ 7፥21)፥ ድግ፤ ምሳ. 31፥24።

3. የሴቶች ልብስ ፦ በኢሳ. 3፥20-24 ልዩ ልዩ የሴቶች ልብስ ተዘርዝሯል፤ በተለይም፥ ልግምበገላ፥ መታጠቂያ፥ መጐናጸፊያ፥ ራስ ማሰሪያ፥ ቀጸላ፥ ዓይነ ርግብ ናቸው።

4. የካህናት ልብስ ፦ መታጠቂያ (ዘጸ. 39፥29)፥ መጠምጠሚያ፥ ሱሪ፥ ሸሚዝ፥ ቆብ (ዘጸ. 28፥40-42፤ 39፥27-29)፥ ኤፉድ፤ 1ሳሙ. 22፥18። የሊቀ ካህናት ልብስ፤ ኤፉድ፥ የኤፉድ ቀሚስ፥ መጠምጠሚያው ከነአክሊሉ። ሸሚዝና መታጠቂያው የተለዩ ነበሩ፤ ዘጸ. 28፥3-39።

5. የተለየ ልብስ ፦ ብዙ ኅብር ያለው (2ሳሙ. 13፥18)፥ የሠርግ (ማቴ. 22፥11)፥ የዓመት በዓል፤ ኢሳ. 3፥22።

6. የወታደር ልብስ ፦ «የጦር መሣሪያ» ይመ.

7. ጫማ ፦ ዘጸ. 3፥5፤ ሐ.ሥ. 12፥8፤ የጫማ ማዘቢያ ወይም ጠፍር፤ ዘፍ. 14፥23፤ ማር. 1፥7።

**ልብና፤** በለኪሶና በጌት መካከል የነበረ የከነዓናውያን ከተማ። ኢያሱ አጠፋው፤ ኢያሱ 10፥29:30። ጦር ሠራዊቱ በእግዚአብሔር መልአክ ከመመታቱ በፊት ሰናክሬም ልብናን ወጋ፤ 2ነገ.





1 2 3 4






5 6

1. አንድ የባቢሎን ሰው በአብርሃም ዘመን። 2. አንድ የባቢሎን ንጉሥ። 3. አንድ ፈርዖን። 4. የግብጽ እመቤት። 5. አንድ የአሦር ንጉሥና ንግሥት። 6. የይሁዳ ሰዎች በይሁዳ መንግሥት ዘመን።


1

2

3

4

ልዩ ልዩ ዓይነት ጫማ። 1. የግብጽ፥ 2. የግሪክ፥ 3. የባቢሎን፥ 4. የሮም።

19፥8።

**ልብን፤** በፍጥነት የሚያድግ፥ በቁመቱ መካከለኛ የሆነ የጥላ ዛፍ፤ ዘፍ. 30፥37፤ ሆሴዕ 4፥13።

**ልከኛ፤** ሥጋዊ ጥቅም የማይፈልግ፥ መጠጥ የማያበዛ፥ በልክ የሚኖር፤ 1ጢሞ. 3፥2፤ ቲቶ 2፥2።

**ልያ፤** የያዕቆብ ሚስት፥ የላባ ታላቅ ልጅ። አባትዋ በተንኰል ለያዕቆብ አጋባት። እንደ እኅትዋ እንደ ራሔል የተወደደች ሚስት አልነበረችም፤ ዘፍ. 29፥16:17:21-30። ነገር ግን የሮቤል፥ የስምዖን፥ የሌዊ፥ የይሁዳ፥ የይሳኮር፥ የዛብሎንና የዲና እናት በመሆንዋ ተደሰተች፤ ዘፍ.29፥31-35፤ 30፥14-21፤ ሩት 4፥11። ከያዕቆብ ጋር ወደ ከነዓን ትጓዘች፤ ዘፍ. 31፥5-18፤ 32፥22፤ 33፥1:2። ለሣራ በተገዛው መቃብር ተቀበረች፤ ዘፍ. 49፥29-32።

**ልደት፤** በእስራኤል ዘንድ ሕፃን ሲወለድ የሚፈጸም ሥርዓት በዘሌ. 12 ላይ ተገልጧል። ክርስቶስ ሕግን ለመፈጸም ስለተወለደ የሕግ ሥርዓት ተፈጸመለት፤ ሉቃ. 2፥21-24:39። «ግዝረት» እና «ዳግም ልደት»ይመ.

**ልዳ፤** ከኢየሩሳሌም በስተምዕራብ 35 ኪ.ሜ. ርቆ የሚገኝ ከተማ። ጴጥሮስ በልዳ ኤንያን ፈወሰ፤ ሐ.ሥ. 9፥32-35። ዛሬ የእስራኤል ኤሮፕላን ማረፊያ ነው። በታውም ሉድ ይባላል፤ ካ. 5መ።

**ልድያ፤** ጳውሎስ ወደ አውሮጳ ከተሻገረ በኋላ በመጀመሪያ ያመነች የእስያ ሴት፤ ሐ.ሥ. 16፥13-15:40።

**ልጅ፤** ልጆች የእግዚአብሔር ስጦታ ናቸው፤ መዝ. 127፥3። በእስራኤላውያን ዘንድ ልጆች በጣም ይፈለጉ ነበር፤ ዘፍ. 15፥2፤ 2ሳሙ. 18፥33። ልጆች ወላጆቻቸውን እንዲያከብሩ ሲሸመግሉም እንዲረዱአቸው ይጠበቅባቸው ነበር። በዚህም እግዚአብሔር ይባርካቸዋል፤ ዘጸ. 20፥12፤ ምሳ. 23፥22-25፤ ማቴ. 15፥4-6።

ልጅ በብ.ኪ. ዘመን አጥፊ ሆኖ ሲገኝ ይቀጣ፥ ከጥፋቱ ካልተመለሰም ይገደል ነበር፤ ዘዳ. 21፥18-21።

እግዚአብሔር ከአማኝ ወላጆች ጋር ቃል ኪዳን ሲመሠርት ከልጆቻቸውም ጋር መሥርቶታል፤ ዘፍ. 17፥7:9-10፤ ዘዳ. 30፥6፤ ሕዝ. 16፥21፤ ሐ.ሥ. 2፥39፤ 1ቆሮ. 7፥14።

ኢየሱስ ልጆችን እንደሚወድ በወንጌል ተገልጧል፤ ማር. 9፥36፤ 10፥13-16፤ ሉቃ. 8፥51-56። ሐዋርያትም፥ ልጆች ለወላጆች በጌታ እንዲታዘዙ አስተምረዋል፤ ኤፌ. 6፥1-3፤ 1ጢሞ. 5፥4፤ 2ጢሞ. 3፥2። ነገር ግን ከወላጆች ይልቅ ክርስቶስን መውደድና መከተል ይገባቸዋል፤ ማቴ. 10፥21:37። በሙሴ (ዘጸ. 2፥1-10)፥ በሳሙኤል (1ሳሙ. 1፥20-3፥19)፥ በኢየሱስም እድገት ጥሩ ምሳሌዎችን እናገኛለን፤ ሉቃ. 2፥7-52። «ወላጆች»፥ «መታዘዝ» ይመ.

ልጅ የሚለው ቃል ከአንድ ሰው በሥጋ የተወለደው ብቻ ሳይሆን የሚከተሉትን ሊያመለክት ይችላል :- 1. ከብዙ ዘመን በኋላ በትውልድ ሐረግ የሚገኝ፤ ሚል. 3፥6። 2. የሥራ ወይም የትምህርት ተከታይ፤ 2ነገ. 2፥3:5። 3. በሃይማኖት የተወለደ፤ 1ጢሞ. 1፥2። 4. በዕድሜ የበታች የሆነ፤ 1ሳሙ. 3፥6። 5. የአገር ወይም የአካባቢ ተወላጅ፤ ሰ.ኤ. 4፥2። 6. የችሎታ፥ የጠባይ፥ የጥበብ ወዘተ... ባለቤት፤ ሉቃ. 10፥6። 7. በሌላ አሳዳጊ ሥር ያለ፤ ሉቃ. 2፥48፤ 3፥23። «በኵር»፥ «ወላጅ» ይመ.

**ልጅነት፤** በብ.ኪ. ዘመን ሰው የሌላውን ልጅ ወስዶ በሕግ የራሱ ልጅ ሊያደርገው ይችል ነበር፤ ዘጸ. 2፥10፤ 1ነገ. 11፥20፤ አስ. 2፥7። በእስራኤል ዘንድ «አባት» ማለት ወላጅ ብቻ ሳይሆን ጠባቂና አሳዳጊ ማለትም ነበር። በዚህም መሠረት በአብርሃም ጠባቂነት የኖሩ ሁሉ እንደ ራሱ ልጆች ሆነው ተገረዙ፤ ዘፍ. 17፥9:23።

እግዚአብሔር ለእስራኤል ሕዝብ ልጅነትን ሰጣቸው፤ ሆሴዕ 11፥1፤ ሮም 9፥4። ክርስቶስ የእግዚአብሔር የባሕርይ ልጅ ነው፤ ዮሐ. 1፥14፤ ዕብ. 1፥3። የአማኞች ልጅነት ግን በመንፈስ ቅዱስ ዳግመኛ በመወለድ የሚገኝ የጸጋ ልጅነት ነው። እግዚአብሔር ዓለም ሳይፈጠር በክርስቶስ መረጣቸው፤ ኤፌ. 1፥4:5። ከባርነት ወደ ልጅነት አመጣቸው፥ ይህም ልጅነት ወራሽነታቸውን ያስከትላል። ሰዎች የእግዚአብሔር ልጆች የሚሆኑት ሲያምኑ ነው፤ ዮሐ. 1፥12፤ ገላ. 3፥23-29፤ 1ዮሐ. 3፥1። መንፈስ ቅዱስም ይህን ያረጋግጥላቸዋልና በዓለም መጨረሻ ለፍጥረት ሁሉ ይገለጣል፤ ሮም 8፥14-17:20-23፤ ገላ. 4፥1-6። «እግዚአብሔር 7»፥ «ዳግም ልደት» ይመ.

**ልግምበገላ፤** ባለ ጥልፍ ጥለት ሰፊ ያለ ኩታ፥ የዱሮ ልብስ፤ ኢሳ. 3፥22።

**ሎላልት፤** ሎሌዎች ሠራተኞች ወይም አሽከሮች ማለት ነው፤ ዘፍ. 50፥7።

**ሎሩሃማ፤** ለነቢዩ ሆሴዕ ሴት ልጅ የተሰጠ ስም። ትርጉሙም «ምሕረት የሌለው» ማለት ነው፤ ሆሴዕ 1፥6:8፤ 2፥6:25፤ 1ጴጥ. 2፥10። «ሩሃማ» ይመ.

**ሎቲ፤** ከብርና ከወርቅ ከሌላም የሚሠራ በጆሮ የሚንጠለጠል ጌጥ፤ ዘጸ. 35፥22።

**ሎዓሚ፤** ለነቢዩ ሆሴዕ ሦስተኛ ልጅ የተሰጠው ስም። ትርጉሙም «ሕዝቤ ያልሆነ» ወይም «ሕዝቤ አይደለም» ማለት ነው፤ ሆሴዕ 1፥9፤ 2፥1:25፤ ሮም 9፥25:26፤ 1 ጴጥ. 2፥10። «ዓሚ» ይመ.

**ሎዶቅያ፤** በእስያ የምትገኝ ብዙ ሀብት ያለባት ከተማ። በዚች ከተማ ለልብስ የሚሆን ጥቁር ሱፍ በብዛት ይገኝ ነበር። ዝነኛ የሆነ የዓይን መድኃኒትም በሎዶቅያ ይሠራ ነበር። ከከተማይቱ ራቅ ብሎ ከሚገኘው ጠበል ተነሥቶ በድንጋይ ቧምቧ ስለሚመጣ የከተማይቱ ውኃ ከከተማይቱ ሲደርስ ለብ

ያለ ነበረ። ዮሐንስ ለሎዶቅያ ቤ.ክ. መልእክት ሲጽፍ እነዚህን ነገሮች ምሳሌ አድርጎ በመጥቀስ መንፈሳዊ ትምህርት ይሰጣል። ጳውሎስ በኤፌሶን ሳለ ቤተ ክርስቲያን በሎዶቅያ የተመሠረተች ይመስላል፤ ሐ.ሥ. 19፥10፤ ቆላ. 2፥1፤ ራእ. 1፥11፤ 3፥14-22። ዛሬ ጆኒዝሊ የምትባል ከተማ በጠበሉ አጠገብ ትገኛለች፤ ካ. 7ለ።

**ሎማ**፤ የዕብራይስጥ ቃል፤ የዘይት መስፈሪያ፤ ዘሌ. 14፥10። «መስፈሪያ» ይመ.

**ሎጥ**፤ የአብርሃም የወንድሙ የሐራን ልጅ። በከለዳውያን ዑር ተወለደ፤ ከአብርሃም ጋር ወደ ከነዓን ተጓዘ፤ ዘፍ. 11፥27፤ 12፥5፤ 13፥1። ለምለም በሆነው በዮርዳኖስ ሜዳ ለመኖር መረጠ፤ ዘፍ. 13፥5-11። ክፉት በሞላባት በሰዶም ከተማ ተቀመጠ፤ ቍ. 12:13። ከሰዶም ሰዎች ጋር በተማረከ ጊዜ አብርሃም ሎጥን መለሰው፤ ዘፍ. 14፥12-16። ሰዶምንም ለማጥፋት የመጡትን መላእክት በቤቱ ተቀበለ፤ ዘፍ. 19፥1-11። መላእክቱም ሚስቱንና ሴቶች ልጆቹን ይዘው በግድ አውጥተው አዳኑአቸው፤ ዘፍ. 19፥16። ይህንም ምሕረት ያሳዩት እግዚአብሔር አብርሃምን ስላሰበ ነው፤ ዘፍ. 18፥20-33፤ 19፥29። የሎጥ ሚስት ግን ወደ ኋላ በመመልከትዋ የጨው ሐውልት ሆነች፤ ዘፍ. 19፥17:26። ሴቶች ልጆቹም አባታቸውን አሰከሩት፥ ከእርሱም ጸነሱ፤ ሞዓብንና አሞንንም ወለዱለት፤ ዘፍ. 19፥30-38። ክርስቶስ የሎጥንና የሚስቱን ታሪክ ለፍርድ ማስጠንቀቂያ ጠቀሰ (ሉቃ. 17፥28-33)፤ እንዲሁም የሎጥ ታሪክ እግዚአብሔር ጻድቃንን ከመከራ ሊያድናቸው መቻሉን የሚያስረዳ ምሳሌ ነው፤ 2ጴጥ. 2፥6-10።

**ሐመልማል**፤ የእህልና የተክል፥ የሣርና የቅጠል ቡቃያ፤ ዘፍ. 1፥29።



በ1350 ገደማ ከክ.ል. የተሠሩና ከከነዓን የተገኙ ሉቲዎች

**ሐመር**፤ ሐምራዊ የቀይ ዳማ። ደም የሚመስል ቀይ ማለት ነው፤ 2ዜ.መ. 2፥7፤ ዘጸ. 28፥8:15። አብዛኛውን ጊዜ የፈረስ መልክ መግለጫ ነው፤ ዘካ. 1፥8፤ ራእ. 6፥8።

**ሐማ**፤ የፋርስ ንጉሥ አርጤክስስ ከፍተኛ ሥልጣን የሰጠው የአይሁድ ጠላት። አይሁድን ለማጥፋት መርዶክዮስንም ለመስቀል አሰበ። ለመርዶክዮስ ባዘጋጀው መስቀል ራሱ ተሰቀለበት፤ አስ. 3፥1-15፤ 5፥9-14፤ 7፥3-10።

**ሐሜት**፤ አንድ ሰው ሌላውን ዐውቆ እንዲጐዳ ወይም እንዲዋረድ ስለዚያ ሰው ውሸት ወይም ክፉ ነገር ማውራት። መ.ቅ. ሐሜትን እንዳንናገር ብዙ ጊዜ ያስጠነቅቀናል፤ መዝ. 50፥20፤ 101፥5፤ ምሳ. 10፥18፤ ኤር. 9፥4፤ 1ጴጥ. 2፥1፤ 1ጢሞ. 3፥11።

**ሐሞት**፤ 1. ከጉበት የሚወጣና ወደ አንጀት ገብቶ ከምግብ ጋር የሚቀላቀል መራራ ፈሳሽ፤ ኢዮብ 16፥13። 2. የእባብ መርዝ፤ ኢዮብ 20፥14። 3. የሚመር ተክል፤ ኤር. 9፥15። ለማደንዘዣ ይጠቀሙበት ነበር፤ ማቴ. 27፥34።

**ሐሞንጎግ**፤ የጎግ ሠራዊት፤ ሕዝ. 39፥11:15፤ «ጎግ» ይመ.

**ሐሤት**፤ ታላቅ ደስታ። ሐሤት አደረገ ማለት እጅግ ደስ አለው ማለት ነው፤ ሉቃ. 10፥21፤ ዮሐ. 8፥56።

**ሐሩር**፤ ሙቀት፥ የሚያቃጥል የፀሐይ ትኩሳት፤ ዘፍ. 31፥40፤ ማቴ. 20፥12።

**ሐር**፤ ከትል የሚገኝ ድር። ለጌጥና ለክብር ልብስ ያገለግላል። ነጋዴዎች ከቻይና አገር ያመጡት ነበር፤ ሕዝ. 16፥10:13፤ ራእ. 18፥12።

**ሐሰተኞች**፤ ኢየሱስ ሐሰተኞች ክርስቶሶችና ሐሰተኞች ነቢያት እንደሚነሡ አስቀድሞ ተናግሯል፤ ማቴ. 24፥5:11:23-25። እንደ እነዚህም ያሉ ሌሎች በሐሰተኛ መንፈስ ተመርተው ይናገራሉ (2ዜ.መ. 18፥22)፥ ወይም ከራሳቸው ልብ ትንቢት ይናገራሉ፤ ኤር. 14፥14። «ነቢያት» ይመ.

**ሐና**፤ የቃሉ ትርጉም «ጸጋ» ማለት ነው።

1. የሕልቃና አንደኛ ሚስት። ልጅ ባለመውለድዋ ታዝን ነበር፤ «ለእግዚአብሔር እሰጠዋለሁ» ብላ በመሳል ልጅ እንድትወልድ ጸለየች። ሳሙኤልንም ወለደች። ስእለትዋንም ለመፈጸም ወደ ካህኑ ዔሊ አመጣችው፤ እግዚአብሔርንም አመሰገነች። በየዓመቱ ሳሙኤልን ትጐበኝ ነበር፤ ሌሎችንም ልጆች ወለደች፤ 1ሳሙ. 1፥1-2፥21።

2. ነቢይት፤ ሰማንያ አራት ዓመት መበለት ሆና ኖራለች። እርስዋም እንደ ስምዖን ከብ.ኪ. ስለ ተረዳች መሲሕን ትጠብቅ ነበር። ከዚህም የተነሣ ኢየሱስ ሕፃን ሆኖ ወደ ቤተ መቅደስ በገባ ጊዜ ዐወቀችው፤ ለሌሎችም መሰከረች፤ ሉቃ. 2፥36-38።

3. ከ6 ዓ.ም. እስከ 15 ዓ.ም. የነበረ የእስራኤል ሊቀ ካህናት። በሮም መንግሥት ከሊቀ ካህንነቱ ቢሻርም

አይሁድ ያከብሩት ነበር፤ ኢየሱስ ወደ ቀያፋ ሳይላክ እርሱ ፊት ተከስሶ ቀርቧል። ከልጆቹ መካከል አምስቱ እንዲሁም ቀያፋ የተባለው የልጁ ባል ደግሞ ሊቃነ ካህናት ነበሩ፤ ሉቃ. 3፥2፤ ዮሐ. 18፥13:24፤ ሐ.ሥ. 4፥6።

**ሐናንያ**፤ 1. የሰጲራ ባል፥ እርሱና ሚስቱ ሐሰት ስለተናገሩ ሁለታቸውም በጴጥሮስ እግር ሥር ወድቀው ሞቱ፤ ሐ.ሥ. 5፥1-10። 2. በደማስቆ ከተማ ይኖር የነበረ ምእመን። ጳውሎስ ባመነ ጊዜ ሐናንያ ወደርሱ ተልኮ ዓይኑ እንዲበራ ለጳውሎስ ጸለየለት በኋላም አጠመቀው፤ ሐ.ሥ. 9፥10-19። 3. ሊቀ ካህናት፤ በዚህ ሰው ፊት ጳውሎስ ተከሶ ቀርቦ ነበር፤ ሐ.ሥ. 23፥1-5።

**ሐዊላ**፤ «ኤውላጥ» ይመ.

**ሐኪም**፤ ኤር. 8፥22፤ ቆላ. 4፥14። «ፈውስ» ይመ.

**ሐዋርያ**፤ «የተላከ መልእክተኛ» ማለት ነው፤ በላኪው ስለሚመረጥ ሥልጣንን ተቀብሎ የላኪውን ትእዛዝ የሚፈጽም ባለሟል እንደራሴ ነው። በመ.ቅ. ሐዋርያ የሚለው ቃል ልዩ ልዩ ሰዎችን ያመለክታል። ኢየሱስ የሃይማኖታችን ሐዋርያ ነው፤ ዕብ. 3፥1። እነበርናባስ በቤ.ክ. ሲላኩ ሐዋርያት ተባሉ፤ ሐ.ሥ. 14፥4:14፤ ራእ. 2፥2። ሆኖም ብዙ ጊዜ «ሐዋርያት» ሲል ቃሉ ኢየሱስ የመረጣቸውን ዐሥራ ሁለቱን ያመለክታል። ስማቸው ፦ ጴጥሮስ (ስምዖን/ወይም ኬፋ) እና ወንድሙ እንድርያስ፥ የዘብዴዎስ ልጆች ያዕቆብና ዮሐንስ፥ ፊልጶስ፥ በርተሎሜዎስ (ናትናኤል ይሆናል)፥ ቶማስ (ዲዲሞስ)፥ ቀራጩ ማቴዎስ (ሌዊ)፥ የእልፍዮስ ልጅ ያዕቆብ (ታናሹ ያዕቆብ ይሆናል)፥ ታዴዎስ የተባለው ልብድዮስ (የያዕቆብ ልጅ ይሁዳ ይሆናል)፥ ቀናተኛ (ቀነናዊ) ስምዖን (አንዳንዶች ናትናኤል ይሆናል ይላሉ)፥ የአስቆሮቱ ይሁዳም ናቸው፤ ማቴ. 10፥1-4፤ ማር. 3፥13-19፤ ሉቃ. 6፥12-16፤ ሐ.ሥ. 1፥12-14።

<u>የማትያስና የጳውሎስ ሐዋርያነት</u>

የአስቆሮቱ ይሁዳ ራሱ ታንቆ ከሞተ በኋላ በእርሱ ምትክ በጴጥሮስ መሪነት በጸሎትና በዕጣ ማትያስ ተመርጦ «ከዐሥራ አንዱ ሐዋርያት ጋር ተቈጠረ»፤ ሐ.ሥ. 1፥15-26።

ክርስቶስ በምድር ሳለ ጳውሎስ አልተከተለውም። ነገር ግን ክርስቶስ በደማስቆ መንገድ ታየው፤ የአሕዛብም ሐዋርያ እንዲሆን ጠራው፤ ሐ.ሥ. 22፥14-21፤ ሮም 1፥1፤ ገላ. 1፥1-2፥10። ጳውሎስ ተአምራትን በማድረጉ፥ ወንጌልን በማስፋፋቱና አብያተ ክርስቲያናትን በመትከሉ ሐዋርያነቱን አረጋገጠ፤ 1ቆሮ. 15፥9-10፤ 2ቆሮ. 12፥12።

አንዳንዶች ጳውሎስ እንጂ ማትያስ በጌታ ባለመመረጡ ከ12ቱ ጋር ሐዋርያ ሆኖ መጠራት አይገባውም ይላሉ። ሆኖም ጳውሎስ አንድም ጊዜ ከ12ቱ ጋር ተቈጥሮ ስለማይገኝ ሉቃስ እንደሚገልጠው ማትያስን ከ12ቱ ጋር መቍጠሩ ተገቢ አማራጭ ነው። ይህ ደግሞ የጳውሎስን ሙሉ ሐዋርያነት የሚያስክድ አይደለም፤ ገላ. 1፥11-12።

<u>የ12ቱ አገልግሎት ሂደት</u>

ዐሥራ ሁለት ነገዶች በእስራኤል እንደነበሩ ክርስቶስ ዐሥራ ሁለት ሐዋርያትን በመንግሥቱ ሾመ፤ ማቴ. 19፥28። ክርስቶስ በስሙ ወንጌልን እንዲሰብኩ፥ ድውዮችን እንዲፈውሱ፥ አጋንንትን እንዲያወጡ ሥልጣን ሰጥቶ ላካቸው፤ ማቴ. 10፥1:40፤ ማር. 3፥14:15፤ ሉቃ. 10፥16። ክርስቶስ በምድር ሳለ ለመንግሥቱ መግቢያ የሆነው የሐዋርያት ሥራ በተለይ በእስራኤል ተወሰነ፤ ማቴ. 10፥5። ከትንሣኤው በኋላ ግን ወደ ዓለም ሁሉ ላካቸው፤ ማቴ. 28፥18-20። ሐዋርያት መንፈስ ቅዱስን ተቀብለው በኃይል ሰበኩ፤ ሐ.ሥ. 1፥8፤ እንዲሁም ም. 2-4 ይመ.። ሲሰብኩም የሚከተሉትን ነገሮች ደጋግመው ተናገሩ ፦ 1. ክርስቶስ በሰዎች ኃጢአት ምክንያት ሞተ፤ ተነሣም። 2. ይህም የትንቢት ፍጻሜ ነው። 3. ክርስቶስን በማመን ብቻ መዳን ይገኛል። 4. አይሁድም ግሪክም ንስሓ ቢገቡ፥ በኢየሱስ ስም ቢጠመቁም የኃጢአትን ስርየትና መንፈስ ቅዱስን ይቀበላሉ። የሐዋርያትን ሥራ፥ መልእክታትን በተለይ ሐ.ሥ. 2፥16-40፤ 1ቆሮ. 15፥3:4 ይመ.

<u>የ12ቱና የጳውሎስ ሥልጣን</u>

ሐዋርያት በቤ.ክ. አስተዳዳሪዎችና የትምህርት ኀላፊዎች ነበሩ፤ ዮሐ. 20፥23፤ ሐ.ሥ. 2፥42፤ 1ቆሮ. 5፥3-5። ሐዋርያት ከነቢያት ጋር የቤ.ክ. መሥራቾች ናቸው፤ ኤፌ. 2፥20፤ 4፥1፤ ማቴ. 16፥18። ለትምህርትና ለሥነ ምግባር አስፈላጊ የሆነው ነገር ሁሉ በሐዋርያት ለቤ.ክ. ተሰጥቷል፤ ገላ. 1፥8-9፤ ይሁዳ 3። ይህ ትምህርት የሚገኘው በአ.ኪ. መጻሕፍት ስለሆነ፥ ከጥንት ጀምሮ ቤ.ክ. እንደ መሠረት አድርጋ ትቀበላቸዋለች።

እንደ 12ቱና እንደ ጳውሎስ ያሉ ሐዋርያት አሁን የሉም፤ እነርሱ ልዩ ሥልጣን ተሰጥቶአቸዋልና፤ የተነሣውንም ጌታ በዓይን አይተውታልና፤ ማቴ. 28፥19-20፤ ሐ.ሥ. 1፥21-22፤ 1ቆሮ. 9፥1፤ 15፥8፤ 2ቆሮ. 12፥11-12፤ 1ዮሐ. 1፥1-4። አሁን የሚገኙት እውነተኛ የወንጌል ሰባኪዎች በሐዋርያት የተሰጠውን እውነተኛ ወንጌል ሳይጨምሩ ወይም ሳይቀንሱ ለአዲሱ ትውልድ ከማስተላለፍ ጋር ሐዋርያት ሊባሉ አይገባቸውም፤ 2ጢሞ. 2፥2፤ ራእ. 22፥18-19።

ከጴጥሮስና ከጳውሎስ በቀር መ.ቅ. ስለ ሐዋርያት ብዙ አይገልጥም። ብዙዎቹ እንደ ያዕቆብ በወንጌል ምክንያት እንደሞቱ በቤ.ክ. ታሪክ ይነገራል።

**የሐዋርያት ሥራ**፤ በአራቱ ወንጌሎችና በመልእክቶች መካከል የሚገኝ የአዲስ ኪዳን መጻሕፍት ማያያዣ መጽሐፍ በመሆን የቤ.ክ.ን መመሥረት፥ መስፋፋትና ሁኔታ ይገልጣል፤ የወንጌል ጸሐፊው ሉቃስ ሁለተኛ የሆነውን ይህን መጽሐፍ ደግሞ ለቴዎፍሎስ የጻፈ ሲሆን፥ ኢየሱስ

የጀመረው አገልግሎትና የማስተማር ተግባር በሐዋርያት መቀጠሉን ያሳያል፤ ሉቃ. 1፥1-4፤ ሐ.ሥ. 1፥1-3። «ሉቃስ»፥ «የሉቃስ ወንጌል»፥ «ቴዎፍሉስ» ይመ.

መጽሐፉ «መንፈስ ቅዱስ በእናንተ ላይ በወረደ ጊዜ ኃይልን ትቀበላላችሁ ... እስከ ምድር ዳርም ድረስ ምስክሮቼ ትሆናላችሁ» የሚለው የኢየሱስ የመጨረሻ ቃል በደቀ መዛሙርቱ ሕይወት እንዴት እንደተፈጸመ ይተርካል፤ 1፥8። ይህም ከመግቢያው ቀጥሎ በስድስት ክፍሎች ተመዝግቧል፤ በየክፍሉም የተመለከተው የመጨረሻ ጥቅስ የወንጌልን ስርጭት ተግባር ይደመድማል።

<u>የመጽሐፉ አከፋፈል</u> ፦

<u>መግቢያ</u>፤ ከትንሣኤው በኋላ ለሐዋርያት የተነገሩት የኢየሱስ የመጨረሻ ቃላት፥ ዕርገቱ፥ የማትያስ መመረጥ፤ 1፥1-26።

1. በበዓለ ኀምሳ ቀን የመንፈስ ቅዱስ መውረድ፥ የጴጥሮስ ስብከት፥ ከ15 ወገኖች በመነሣት የ3000 ሰዎች አምነው መጠመቅና ወደ ቤ.ክ. መጨመር፥ የበሽተኞች መፈወስ፥ የኢየሩሳሌም ሸንጎ ተቃውሞና ስደት፥ የቤ.ክ. ሰዎች ግብዝነትና መለያየት መወገድ፥ የካህናት መመለስ፤ 2፥1-6፥7።

2. ከእስጢፋኖስ መገደል በኋላ የግሪክ ቋንቋ ተናጋሪዎች ምእመናን መበታተን፥ በሰማርያና ለኢትዮጵያዊው ጃንደረባ የተሰጠው የፊልጶስ ምስክርነት፥ የሳውል (የጳውሎስ) መለወጥ፤ 6፥8-9፥31።

3. በይሁዳና እስከ ታላቁ ባሕር ድረስ የተሰማው የጴጥሮስ ምስክርነት፥ ጴጥሮስ ከአሕዛብ ወገን የመጀመሪያውን ሰው (ቆርኔሌዎስን) ወደ ቤ.ክ. እንዲገባ መፍቀዱ፥ ወንጌል ወደ አንጾኪያ መድረሱ፥ የሐዋርያው ያዕቆብ መገደልና የጴጥሮስ ከሞት መዳን፥ የሄሮድስ ሞት፤ 9፥32-12፥24።

4. ወደ ቆጵሮስና ወደ ገላትያ የተደረገ የጳውሎስ የወንጌል ጕዞ፥ በግዝረትና በሙሴ ሕግ አሕዛብ እንዳይገደዱ በሐዋርያት ጉባኤ መወሰኑ፥ ጳውሎስ ውሳኔውን ይዞ ገላትያ መድረሱ፤ 12፥25-16፥5።

5. ጳውሎስና ጓደኞቹ ወደ ግሪክ አገር፥ ወደ እስያ፥ በተለይም በፊልጵስዩስ፥ በተሰሎንቄ፥ በቤርያ፥ በአቴና፥ በቆሮንቶስና በኤፌሶን ያደረጋቸው ሐዋርያዊ ጕዞዎች፤ 16፥6-19፥20።

6. በኤፌሶን የተነሣው ግርግር፥ በግሪክ የጳውሎስ ጕዞ፥ የኤፌሶንን ሽማግሌዎች መሰናበቱ፥ እርዳታ ይዞ ወደ ኢየሩሳሌም መድረሱ፥ በአሳዳጆቹ መያዙ፥ ለሸንጎው የሰጠው ምስክርነት፥ በቂሣርያ ለፊልክስ፥ ለፊስጦስና ለንጉሥ አግሪጳ የሰጠው ምስክርነት፥ ሮም ደርሶ ፍርድን በመጠባበቅ ላይ ሳለ ሁለት ዓመት በተከራየው ቤት እየመሰከረ መኖሩ፤ 19፥21-28፥20።

<u>መጽሐፉ የሚያተኵርባቸው አሳቦች</u>

የሉቃስ ዋና ዓላማ ወንጌል እየተስፋፋ መሄዱን መመዝገብ ሲሆን፥ ከዚህም ጋር በሰባት ነገሮች ላይ ሲያተኵር ይታያል፥ እነርሱም ፦

ሀ. ወንጌል ለሰዎች ሁሉ ነው፥ ለአይሁድ (2፥5-11)፥ ለሳምራውያን (8፥4-25)፥ ለአሕዛብ (10፥1-11፥18)፥ ለአረማውያን (14፥8-18)፥ ለመጥምቁ ዮሐንስ ደቀ መዛሙርት፤ 19፥1-7።

ለ. ክርስቶስ፥ ሰዎች ከልዩ ልዩ ወገን በመምጣት በእርሱ ሲያምኑ እንደተቀበላቸው አረጋግጧል፥ ይህም የሆነው መንፈስ ቅዱስ በእነርሱ ላይ ሲወርድ በልሳን የመናገርን ወይም ሌላ መንፈሳዊ ስጦታን በመስጠት ነበር። በዚህም አማኞች ሁሉ የአንዲት ቤ.ክ. አባላት መሆናቸውን አሳይቷል፤ 2፥4፤ 8፥15-17፤ 10፥44-48፤ 11፥15-18፤ 19፥5-6፤ 1ቆሮ. 12፥12-13።

ሐ. ወንጌል የጨለማውን ሥራ ሁሉ ያሸንፋል፤ የተሸነፉት ክፉ ሥራዎች ስደት (8፥2-4)፥ ጥንቆላ (8፥9-25)፥ ምዋርት (16፥16-18)፥ ዓለማዊ ፍልስፍና (17፥34)፥ መናፍስትን የማስወጣት ሐሰተኛ እውቀት፥ አስማተኛነት፥ ባዕድ አምልኮ (19፥13-27) ናቸው።

መ. ወንጌል በልዩ ልዩ ወገን ዘንድ የሚገኘውን የአሳብ መለያየት ያስታርቃል፤ 15፥1-29።

ሠ. ወንጌል የብሉይ ኪዳን ፍጻሜ ነውና አይሁድ ሊቀበሉት ይገባቸዋል፤ 2፥16-36፤ 13፥26-43።

ረ. በወንጌል ምክንያት ችግር ቢፈጠር ኀላፊነቱ የወንጌል ጠላቶች እንጂ የክርስቲያኖች ስላልሆነ ባለሥልጣናት የወንጌልን ተከታዮች ሊደግፉ ይገባቸዋል፤ 14፥2:19፤ 16፥17-20፤ 17፥5፤ 19፥24-27፤ 21፥27-28።

ሰ. የወንጌል እውነተኛነት በክርስቶስ ትንሣኤ ተረጋግጧል። ሉቃስ ዐሥር ንግግሮችን በአጭሩ የመዘገበ ሲሆን በንግግሮቹ ውስጥ ትንሣኤው በጉልህ ተጠቅሷል፤ ለምሳሌ 2፥24-33፤ 17፥31፤ 23፥6-8 ይመ.። የጳውሎስ መመለስ ደግሞ እንደ ትልቅ ማስረጃ በመቈጠሩ ሉቃስ ሦስት ጊዜ ጽፎታል፤ 9፥1-18፤ 22፥6-16፤ 26፥12-18። ምስክርነቱን ለመቀበል የሚችሉ ግን እግዚአብሔር በሰው ልብ ሲሠራ ነው፤ 2፥47፤ 5፥14፤ 11፥18፤ 16፥14፤ 18፥9-10።

«የሐዋርያት ሥራ»፥ ጳውሎስ ፍርድን ሲጠብቅ ሳለ በ64 ዓ.ም. ገደማ እንደተጻፈ ይገመታል። «ሐዋርያ»፥ «መንፈስ ቅዱስ»፥ «ጴጥሮስ»፥ «ጳውሎስ» ይመ.

**ሐውልት**፤ የመታሰቢያ ድንጋይ ወይም የድንጋይ ክምር፤ ዘፍ. 28፥18፤ 31፥45-54፤ ኢያሱ 4፥1-9፤ 24፥26:27፤ 1ሳሙ. 7፥12፤ 2ሳሙ. 18፥18። በከነዓን ሐውልት ለአማልክቶቻቸው መስገጃ ስለሆነ እስራኤል ሐውልቶችን እንዲሰብሩ ታዘዙ፤ ዘጸ. 23፥24። የሎጥ ሚስት የጨው ሐውልት ሆነች፤ ዘፍ. 19፥26።

**ሐጌ**፤ በ520 ከክ.በ. በኢየሩሳሌም ለነበሩት አይሁድ «በትንቢተ ሐጌ» የሚገኘውን ትንቢት የተናገረ ነቢይ፤ ዕዝ. 5፥1:2። እነርሱ ከምርኮ ከተመለሱ በኋላ ቤተ መቅደስን ለመሥራት ጀምረው ነበር። ከሳምራውያን መቃወም የተነሣ ሥራው

ተቋረጠ፤ ሳይፈጽሙትም 16 ዓመት ዘገየ፤ ዕዝ. ም. 3-4። ከዚህ በኋላ ሐጌ ሥራውን እንዲፈጽሙት አነሣሣቸው።

<u>የሐጌ ትንቢት አከፋፈል</u> ፦

1. «የእግዚአብሔርን ቤት ለመሥራት ተነሡ» የሚል ወቀሳ፤ ም. 1።

2. «እግዚአብሔር ከእናንተ ጋር ይኖራል» የሚል ማበረታቻ፤ ም. 2፥1-9።

3. «እግዚአብሔር ይባርካችኋል» የሚል ተስፋ፤ ም. 2፥10-19።

4. «እግዚአብሔር ዘሩባቤልን ከፍ ከፍ ያደርገዋል» የሚል ትንቢት፤ ም. 2፥20-23። ኤር. 22፥24 ይመ.

**ሐጾር**፤ «አሶር» ይመ.

**ሔሬብና ዜብ**፤ በጌዴዎን የተገደሉ ሁለት የምድያም መኳንንት፤ መሳ. 7፥24:25፤ መዝ. 83፥11።

**ሔዋን**፤ የሕያዋን ሁሉ እናት ማለት ነው፤ የመጀመሪያዋ ሴት የአዳም ሚስት። እግዚአብሔር ከአዳም ሥጋ ፈጠራት፤ አዳምም በደስታ ተቀበላት፤ ዘፍ. 2፥20-25። ሰይጣን በእባብ ምሳሌ አታለላትና የተከለከለውን ፍሬ በላች፤ ፍሬውንም ለአዳም ሰጠች። በኋላም ስሕተትዋን በእባቡ አመካኘች፤ ዘፍ. 3፥1-13። በስሕተት ስለወደቀች ለባልዋ እንድትታዘዝ በጭንቅም ልጅ እንድትወልድ ተፈረደባት፤ ዘፍ. 3፥16። አዳም ግን በእግዚአብሔር ቃል ተስፋ አድርጎ ዘር እንደሚኖራት አምኖ ሔዋን ብሎ ሰየማት፤ ዘፍ. 3፥15:20። በአ.ኪ. የመተላለፍ መጀመሪያ ሆና ተጠቅሳለች፤ 1ጢሞ. 2፥14:15።

**ሕሊና**፤ በመልካምና በክፉ መካከል የሚለይ፥ በጥፋቱ ሰውን የሚወቅስ፥ ስለ ክፉም ሆነ ስለ መልካም ሥራው ሰውን እንዲያመዛዝን የሚያሳስብ፥ እግዚአብሔር በሰው የተከለለት የግብረ ገብነት (የሞራል) ምዕዝር ነው፤ 1ቆሮ. 4፥4፤ 2ቆሮ. 5፥11።

የእግዚአብሔርን ቃል ያልሰሙ በተፈጥሮቸው በተረዱት መሠረት ሕሊናቸው ይመሰክራል፤ ሮም 2፥14:15።

ሰው ንጹሕ ሕሊና እንዲኖረው የሚታየውን መልካም ነገር ሁሉ ማድረግና መጥፎ ነገርን ማስወገድ አለበት፤ ሐ.ሥ. 23፥1፤ ሮም 13፥5፤ 1ጴጥ. 3፥16። ሰው በስሕተት መልካም የመሰለው ክፉ ሊሆን ይችላልና የመልካምና የክፉ ነገር መለያ ዋና ዳኛ ሕሊናው ሳይሆን የእግዚአብሔር ቃል ነው፤ 1ቆሮ. 8፥7። ሰው መልካሙን በውቀ ባያደርገው ሕሊናው ይደነዝዛል፤ በመጨረሻም አይሠራም፤ 1ቆሮ. 8፥12፤ 1ጢሞ. 4፥2፤ ቲቶ 1፥15።

ስለዚህ አዲስ አማኝ ወይም ደካማ ክርስቲያን ሕሊናው እንዳይጐዳ በሚጠራጠርበት ጊዜ ሊገደድ አይገባም፤ 1ቆሮ. 8፥7-13። ሰው ንጹሕ ሕሊና የሚያገኘው በእንስሳት ደም ሳይሆን በክርስቶስ ሥራ ነው፤ ዕብ. 9፥9:14፤ 10፥22፤ 1ጴጥ. 3፥21።

**ሕልም**፤ በእንቅልፍ ጊዜ የሚታይ ነገር። ሕልም አንዳንድ ጊዜ በቀን ከታየና ከታሰበ ነገር፥ ከአድራጎትም የተነሣ ይታለም ይሆናል። ብዙ ጊዜ ልዩ ትርጉም አይኖረውም፤ መክ. 5፥3። እግዚአብሔር ለብዙ ሰዎች በሕልም በመታየት ፈቃዱን ገልጦላቸዋል፤ ዘፍ. 20፥3፤ 28፥12፤ 37፥5-11። መላእክት የጌታን ፈቃድ ለሰዎች በሕልም ይናገራሉ፤ ማቴ. 1፥20፤ 2፥13:19። ሕልምን የመተርጐም ስጦታ ለዮሴፍና ለዳንኤል ተሰጠ፤ ዘፍ. 40፥5-23፤ 41፥14-36፤ ዳን. 2፥25-45፤ 4፥4-27። ሰዎች በመንፈስ ቅዱስ ሕልምን ሊያልሙ ይችላሉ፤ የሐ.ሥ. 2፥17። ሕልም አንዳንድ ጊዜ ሰውን ሊያስት ይችላል፤ ዘዳ. 13፥1-4። «ራእይ»፥ «ትንቢት» ይመ.

**ሕንፃ**፤ የጥንት ሰዎች ሕንፃን የሚሠሩት በአቅራቢያ ከሚገኙ እንጨት፥ ጭቃና ድንጋይ ነበር። በፀሐይ ወይም በእሳት ከተቃጠለ ጭቃ ጡብን ይሠሩ ነበር። ወርቅ፥ ብር፥ ናስ፥ የዝሆን ጥርስ፥ የተቀረጸ ድንጋይና እንጨትም ለቤት ጌጥ ያገለግሉ ነበር። በድሮ ዘመን የተሠሩ ብዙ ሕንጻዎች ዛሬ አሉ። አርኪዎሎጂስቶች የብዙ ሺህ ቤቶችና ሕንጻዎች መሠረቶችን ቈፍረው አግኝተዋል። አሠራሩ እንደ አገሩ የተለያየ ነበር። በሕንጻ ሥራ ከሁሉ የሚበልጡ ግብፆች ናቸው። በሰሎሞንና በሄሮድስ የተሠሩት አብያተ መቅደስ በዓለም ሁሉ የታወቁ ናቸው። «ቤት»፥ «ግንብ»፥ «ከተማ»፥ «በር»፥ «አርኪዎሎጂ» ይመ.

**ሕዝቅኤል**፤ የስሙ ትርጉም «እግዚአብሔር ብርታትን ይሰጣል» ማለት ነው። በ597 ከክ.ል. የእስራኤል ልጆች ወደ ባቢሎን በተማረኩ ጊዜ ነቢዩ ሕዝቅኤል ከምርኮኞቹ አንዱ ነበር። የእስራኤል ካህን ነበር። በምርኮ አገር ከሌሎች እስራኤላውያን ጋር ኮቦር ከተባለው ወንዝ አጠገብ ይኖር ነበር፤ ሕዝ. 1፥3። ወንዙ የትኛው እንደሆነ ዛሬ አይታወቅም፤ ሆኖም ከባቢሎን ከተማ ብዙ እንደማይርቅ ይገመታል። ሕዝቅኤል ዳንኤልን ያውቀው ይሆናል፤ ሕዝ. 14፥14:20፤ 28፥3። ሕዝቅኤል ባለሚስትና ባለቤት ነበር፤ ሕዝ. 8፥1፤ 24፥16-18።

ሕዝቅኤል በሠላሳ ዓመት ዕድሜው እግዚአብሔርን በኪሩቤል ላይ እንዳለ በራእይ አየ፤ ሕዝ. ም. 1። ለተማረኩት ለእስራኤል ሕዝብ ቃሉን እንዲናገር ተጠራ፤ ሕዝ. 2፥1-4። ባይናገር ግን እግዚአብሔር የኃጢአተኛውን ደም ከእጁ እንደሚፈልግ ሁለት ጊዜ አስጠነቀቀው፤ ሕዝ. 3፥18፤ 33፥6። የሕዝቅኤልን የአገልግሎት ዘመን በሁለት የተለያዩ ክፍሎች ልንከፍለው እንችላለን ፦

1ኛ. ኢየሩሳሌም በ587 ከክ.ል. በጠላት እጅ ከመውደቅዋ አስቀድሞ በባቢሎን ምርኮኞች መካከል የፈጸመው የስብከት አገልግሎት፤ ም. 4-24።

2ኛ. ኢየሩሳሌም በጠላት እጅ ከወደቀች በኋላ በባቢሎን የፈጸመው የስብከት አገልግሎት፤ ም. 33-48።

ሕዝቅኤል ከኢየሩሳሌም ውድቀት በፊት ያደረገው ስብከት የንስሐ ስብከት ነበር። ምክንያቱም

ተማርከው የነበሩ አይሁድ በቶሎ ወደ አገራችን እንመለሳለን፥ ባቢሎን ተሸንፎ አሁኑኑ ከአገራችን ይወጣልናል የማለት አሳብ ስላደረባቸው ነበር። በዚህም ሁሉ ወደ እግዚአብሔር የመመለስ ምልክት አላሳዩም። ኢየሩሳሌም ልትወድቅ አትችልም የሚል እጉል እምነት ነበራቸው። ይህም እግዚአብሔር ቅዱስ መሆኑንና ኃጢአታቸውም ፍርድን እንደሚያስከትል ስላልተረዱ ነው፤ ከተማይቱ ከወደቀች በኋላ ግን የሕዝቡ መንፈስ ተለወጠና በሆነው ነገር እያዘኑ ተስፋ ቈረጡ። ከዚህም የተነሣ የነቢዩም ስብከት ተለውጦ የሚያጽናና ቃል ሆነ። እግዚአብሔር በምሕረቱ ሕዝቡን እንደሚያድን፥ እግዚአብሔር ራሱ እረኛ እንደሚሆናቸው (ሕዝ. ም. 34)፥ አዲስ ልብም እንደሚሰጣቸው (ሕዝ. 36፥26-28)፥ ዳዊትም ንጉሥ እንደሚሆንላቸው (ሕዝ. 34፥24፤ 37፥24-28) ተነበየ። ይህን አዲስ ሁኔታ በአዲሱ ቤተ መቅደስ ምሳሌነት ገለጠላቸው፤ ሕዝ. ም. 40-48። የዚህ ሁሉ ፍጻሜ በወንጌል ዘመን መታየቱ እሙን ነው።

ቃሉ ለሰዎች እንዲሰማቸው ሕዝቅኤል ለረጅም ጊዜ በጐኑ በመተኛት፥ የሚያረክሰውን በመብላት፥ ጠጕሩን ቈርጦ በመበተን፥ ዲዳ በመሆን፥ ሚስቱ ስትሞት ባለማልቀስ በሌላም በአዲስ ሁኔታ ያስተምር ዘንድ ታዘዘ፤ ሕዝ. ም. 4፤ 5፤ 12፤ 24። ሽማግሌዎች የነበሩ ምርኮኞች ይሰሙት ነበር። በመጀመሪያ ግን በቃሉ አልተደሰቱም። ከኢየሩሳሌም መፍረስ በኋላ በቃሉ ቢደሰቱም ብዙዎች በቃሉ መሠረት አልተለወጡም፤ ሕዝ. 2፥4፤ 33፥30-33። ሆኖም በነቢዩ አገልግሎት ወደ ኢየሩሳሌም እንዲመለሱ እግዚአብሔር ከሕዝቡ ፈቃደኛ የሆኑትን አዘጋጀ።

**የሕዝቅኤል ትንቢት**፤ ሕዝቅኤል በባቢሎን ሳለ ከ592-570 ከክ.በ. ለእስራኤል ምርኮኞች ትንቢት ተናገረ፤ 1፥1፤ 29፥17።

አከፋፈል :-

1. ከኢየሩሳሌም ውድቀት በፊት ስለ እግዚአብሔር ፍርድ የተናገረው ትንቢት፤ ም. 1-24።

2. በአሕዛብ መንግሥታት ላይ የተናገረው ትንቢት፤ ም. 25-32።

3. ከኢየሩሳሌም ውድቀት በኋላ ስለ እስራኤል መመለስ የተናገረው ትንቢት፤ ም. 33-48።

**ሕዝቅያስ**፤ የስሙ ትርጕም «እግዚአብሔር ኃይሌ ነው» ማለት ነው። በነቢዩ ኢሳይያስ ዘመን ከ716-687 ከክ.በ. የነገሠ ዐሥራ ሦስተኛው የይሁዳ ንጉሥ። አስቀድሞ ከአባቱ ከአካዝ ጋር በአንድነት ከ729-716 ከክ.በ. የነገሠ ይመስላል፤ 2ነገ. 18፥9-10:13።

ከይሁዳ ነገሥታት ሁሉ እርሱን የሚመስል አልነበረም፤ 2ነገ. 18፥5። ባዕድ አምልኮትን አጠፋ፥ ሙሴ የሠራውን የናሱን እባብ ሰበረ፤ ቤተ መቅደስንም አሳደሰ። የእስራኤልን ነገዶች ሁሉ ፋሲካን ለማክበር ጠራ። በዘመነ መንግሥቱ ሁሉ አሦር ይሁዳን አስቸገረ፤ በዚህ ጊዜ ሕዝቅያስ ከልዩ ልዩ አገሮች ጋር ስምምነትን ያደረገ ይመስላል (2ነገ. 20፥12-13)፤ የኢየሩሳሌምን ቅጥር አስፋፋ፥ ግንቦችን ሠራባት፥ ከከተማዋ በታች ቦይ በማስቈፈር ከቅጥሩ ውጭ የግዮንን ምንጭ ውኃ ወደ ውስጥ እንዲገባ አደረገ፤ ካ.8ሀ። ሰናክሬም ብዙ ከተሞችን ሲወስድ ከሕዝቅያስም ብዙ ሀብት ወሰደ። በኋላም ሕዝቅያስ የአሦርን ንጉሥ ዛቻ በጸሎት ተቃወመ፤ እግዚአብሔር አሦራውያንን ቀሠፈ። በታመመ ጊዜ በበለስ ጥፍጥፍ ተፈወሰ። በዕድሜው ላይ ዐሥራ አምስት ዓመት ተጨመረለት፤ በስፍረ ሰዓት ምልክት ተደረገለት። ነገር ግን የባቢሎን ንጉሥ መልእክተኞች በመጡ ጊዜ ልቡ ታበየ፤ 2ነገ. ም. 18-20፤ 2ዜ.መ. ም. 29-32፤ ኢሳ. ም. 36-39።

**ሕዝብ ቈጠራ**፤ እግዚአብሔር በሲናና በሞዓብ ሜዳ ከእስራኤል ሕዝብ ለጦርነት ሊሰለፉ የሚችሉት እንዲቈጠሩ ትእዛዝ ሰጠ፤ ዘኍ. 1፥26፤ 26፥2። በዕዝራና በነህምያ ዘመን ደግሞ እግዚአብሔር የኢየሩሳሌም ሕዝብ እንዲቈጠሩ አዘዘ፤ ዕዝ. 2፥1-65፤ ነህ. 7፥6-67። ዳዊት ግን ሳይታዘዝ ሕዝቡን በመቍጠሩ እግዚአብሔርን አስቈጣ፤ ምክንያቱም ንጉሡ በሕዝብ ብዛት እንዲመካና እንዲተማመን ያደረገው ይመስላልና፤ 2ሳሙ. 24፥1-9፤ 1ዜ.መ. 21፥1-6። «ቍጥር» ይመ.።

የሮም ቄሣሮች ግብርንና ቀረጥን ለመሰብሰብ ብዙ ጊዜ ሕዝቡ በቤተሰብ እንዲጻፍ ትእዛዝ ሰጥተዋል። ዓለሙ ሁሉ እንዲጻፍ የአውግስጦስ ቄሣር ትእዛዝ ወጥቶ ነበር፤ ሉቃ. 2፥1-3። ከአይሁድ መካከል «ቀናተኞች» የተባሉ በመጻፋቸው ምክንያት በ6 ዓ.ም. ሸፈቱ፤ ሐ.ሥ. 5፥37

**ሕይወት**፤ ከግዑዝ ነገር በስተቀር የሚኖርና የሚንቀሳቀስ ሁሉ ሕይወት አለው። እግዚአብሔር በራሱ ሕይወት አለው (ዮሐ. 5፥26)፥ ስለዚህ ሕይወት ከሌላቸው «አማልክት» ለመለየት ሕያው አምላክ ተብሏል፤ ዘዳ. 5፥26፤ ዕብ. 10፥31። እግዚአብሔር ለፍጥረቱ ልዩ ልዩ ዓይነት ሕይወት በመስጠቱ የመላእክት፥ የሰዎች፥ የእንስሳትና የዕፀዋት ሕይወት አንድ አይደለም፤ 1ቆሮ. 15፥37-41። የመላእክት ሕይወት አይጠፋም፤ ሰው ግን በሥጋ ቢሞትም ተነሥቶ ለዘለዓለም ይኖራል። የእንስሳት ሕይወት ደማቸው በመሆኑ ይጠፋል፤ የዕፀዋት ደግሞ ግዑዝ ሕይወት ነው። እግዚአብሔር የሕይወትን እስትንፋስ በሰው ላይ እፍ በማለቱ ልዩ ክብር ሰጠው፤ ዘፍ. 2፥7፤ ዮሐ. 1፥4። የሥጋ ሕይወት በደሙ ነውና የሰውን ደም የሚያፈስስ በሞት እንዲቀጣ ተጽፏል፤ ዘፍ. 9፥4-6፤ ዘሌ. 17፥11። ሞት የሕይወት ተቃራኒ ነው፤ ሮም 6፥23። ሥጋዊ ሕይወት (ዘጸ. 1፥14፤ ዘሌ. 17፥1-12)፥ መንፈሳዊ ሕይወት (ሮም 8፥6፤ ቆላ. 3፥3) እና የዘለዓለም ሕይወት አለ፤ ኤፌ. 2፥5-7። «የዘለዓለም ሕይወት»፥ «ነፍስ»፥ «መንፈስ» ይመ.

**የሕይወት መጽሐፍ**፤ የእግዚአብሔር ሰዎች በእርሱ ዘንድ እንደሚታወቁ የሚገልጥ ምሳሌ። በብ.ኪ. የእስራኤላውያን ስም የተጻፈበትን መጽሐፍ አንዳንድ ጊዜ ቢያመለክትም (ዘጸ. 32፥32-33፤ መዝ. 69፥28፤ 139፥16)፥ ብዙ ጊዜ ከሥጋዊ

ሕይወት ቀጥሎ የዘለዓለምን ሕይወት የሚወርሱትን ምእመናንን ሁሉ ያሳያል፤ ኢሳ. 4፥3፤ ዳን. 12፥1፤ ሉቃ. 10፥20፤ ፊል. 4፥3፤ ራእ. 3፥5፤ 20፥12:15። በዚህ መጽሐፍ ሰዎች የተመዘገቡት ከዓለም ፍጥረት ጀምሮ ነው፤ ራእ. 13፥8፤ 17፥8፤ ሐ.ሥ. 13፥48። ይህን አሳብ ይዞ የተመዘገቡት ወደ እምነት እንደሚደርሱ ያሳያል። ኢየሱስ የተመዘገቡትን በመሞቱ በማዳኑ መጽሐፉ «የበጉ ሕይወት መጽሐፍ» ተብሏል፤ ራእ. 13፥8፤ 21፥27።

## የሕይወትና የዕውቀት ዛፎች፤

እግዚአብሔር በገነት ሁለት ልዩ ዛፎችን አበቀለ፤ ዘፍ. 2፥9። ሰው መልካምንና ክፉን ከሚያሳውቀው ዛፍ እንዳይበላ ተከለከለ። ይህ ዛፍ የሰው የመታዘዝ መግለጫ ነበር። ከእርሱ ባይበላ ኖሮ ከሕይወት ዛፍ ለመብላት ይበቃ ነበርና ሳይሞት ለዘለዓለም ይኖር ነበር። ባለመብላትም የተሻለውን ሁኔታ አግኝቶ የመልካምና የክፉ ዕውቀትን ያገኝ ነበር፤ በመብላቱ ግን ወደባሰ ሁኔታ ስለገባ የመልካምና የክፉ ልዩነትን ተረዳ። ከሕይወት ዛፍ እንዳይበላ እግዚአብሔር ከገነት አስወጣው። አሁን ግን የሕይወት ዛፍ በመንግሥተ ሰማያት ይገኛል። የሕይወት ዛፍ የሚያመለክተው ሰው ሲበቃ የዘለዓለምን ሕይወት ከእግዚአብሔር እንደሚያገኝ ነው፤ ዘፍ. 2፥9፤ 3፥1-6:22-24፤ ራእ. 2፥7፤ 22፥14።

**ሕግ፤** አንድን ነገር ለመፈጸም የሚያዝዝ ወይም ከማድረግ የሚከለክል ትምህርት፥ መመሪያ፥ ውሳኔና ሥርዓት። ሕግ በማናቸውም ጊዜ አለ፤ ለምሳሌ ትእዛዛት ለአዳም፥ ለኖኅ፥ ለአብርሃም፥ ለሙሴ እንዲሁም ለሐዋርያት ተሰጥተዋል፤ ሮም 3፥19-21:28። እግዚአብሔር ሰዎችን የሚያስተዳድረው በቃል ኪዳን ሥርዓት ነው፤ «ቃል ኪዳን» ይመ.። ሕግ በቃል ኪዳን ውስጥ የሰውን ድርሻ ያሳያል። ሰው በእግዚአብሔር ሕግ መደሰት ይገባዋል፤ መዝ. 1፥2፤ 19፥7-11፤ 119።

1. የእግዚአብሔር ሕግ አመጣጥ፤

ሕገ ልቡና (በተፈጥሮ በሰው አእምሮ ውስጥ የሚገኝ፤ ሮም 2፥12-15)፥ ሕገ ኦሪት (ዮሐ. 1፥17) እና ሕገ ወንጌል ተብሎ ሊከፈል ይችላል፤ ማቴ. 5፥17።

2. ሕግ በብሉይ ኪዳን ዘመን፤

በመሠረቱ ዐሥርቱ ቃላት ሕግ ነበሩ፤ ዘዳ. 4፥13። ትእዛዛቱ በቃል ኪዳን መልክ ተሰጡ፤ ዘጸ. 20፥1-17። የብሉይ ኪዳን ሕግ በሦስት ክፍሎች ሊመደብ ይችላል፤ እነርሱም የግብረገብ መመሪያዎች (የሞራል ሕግ)፥ የመንግሥት መተዳደሪያ ሕግጋትና የመሥዋዕት አገልግሎት መመሪያዎች ናቸው።

«ሕግ» አምስቱን የሙሴ መጻሕፍት (ማቴ. 5፥17፤ ሉቃ. 16፥16) እና ብ.ኪ. በሙሉ (ዮሐ. 10፥34፤ 12፥34) ሊያመለክት ይችላል። የብሉይ ኪዳን የአስተዳደር ዘመንንም ሊያሳይ ይችላል፤ ዮሐ. 1፥17።

ሕግ ስለ ክርስቶስ ይመሰክራል፥ ኃጢአተኝነትን በማሳወቅ ሰውን ወደ ክርስቶስ ይመራል፤ ሉቃ. 24፥44-47፤ ዮሐ. 5፥39: 45-47፤ ሮም 3፥20፤ 7፥7፤ ገላ. 3፥24።

3. ክርስቶስ ሕግን ሊፈጽም መጣ፤

በራሱ ሕይወት ለሕግ በመታዘዙ (ገላ. 4፥4፤ 1ጴጥ. 2፥22:23)፥ ሕግን በማብራራትና በማጽናት ሕግ እንዳልቀረ በመደገፍ (ማቴ. 5፥17-48)፥ የሕግን ቅጣት ስለ ሌሎች በመቀበል (ገላ. 3፥10-13)፥ በብ.ኪ. መሥዋዕት ፈንታ ራሱን በቂ መሥዋዕት አድርጎ አንድ ጊዜ በማቅረቡ (ዕብ. 9፥11-14)፥ ተከታዮቹንም በሕግ መንገድ እንዲሄዱ በማድረግ (ሮም 8፥3:4) ሕግን ፈጸመ። ክርስቶስ የአ.ኪ. ዘመን ጀማሪ በመሆኑ ምክንያት የልዩ ልዩ ሥርዓት መኖር አስፈላጊ አለመሆኑን ተናግሯል፤ ማር. 7፥19፤ ቈላ. 2፥16-23። ክርስቶስ ሕግን በሁለት ትእዛዛት ማለትም እግዚአብሔርን በመውደድና ሰውን በመውደድ አጠቃሎታል፤ ማቴ. 22፥35-40።

4. ወንጌል የብሉይ ኪዳንን ሕግ አስረጅቶታል፤

ዕብ. 8፥13። ከአይሁድ ወገን ካመኑት ውስጥ ብዙዎች ለደኅንነት ሕግን መፈጸም አስፈላጊ መሆኑን አስተምረው ነበር። ሐዋርያት ግን ትምህርቱን አልተቀበሉትም፤ ሐ.ሥ. 15፥1:5:7-21። ምክንያቱም ሰው ሕግን ፈጽሞ መጠበቅ ስለማይችል የሕግን ሥራ በመሥራት ሳይሆን ከእግዚአብሔር ጸጋ የተነሣ፥ በክርስቶስ ሥራ መሠረት፥ በእምነት ይጸድቃልና፤ ሮም 3፥24:28፤ ገላ. 2፥16። ስለዚህ አማኝ አሁን «ከሕግ በታች» ባይሆንም እንኳ በሕግ የተገለጠውን የእግዚአብሔርን ፈቃድ መፈጸም ይፈልጋል፤ ይጥራልም፤ ሮም 6፥14-15፤ 7፥14-16:22፤ ኤፌ. 2፥8-10።

በሰው ውስጥ «የኃጢአት ሕግ» አለ፥ አማኙም ሊያሸንፈው የሚችል «በመንፈስ ሕግ» ማለትም በውስጡ በሚኖር በመንፈስ ቅዱስ ኃይል ብቻ ነው፤ ሮም 7፥21-23፤ 8፥2:13። በእነዚህ ጥቅሶች «ሕግ» ተብሎ የተጠቀሰው መሠረታዊ ሐቅን እንጂ ትእዛዝን ወይም ሥርዓትን አያመለክትም።

**ሖር፤** 1. ከአሮን ጋር የሙሴን እጆች የደገፈ (ዘጸ. 17፥12) ከአሮንም ጋር ፈራጅ የነበረ፤ ዘጸ. 24፥14። 2. በሴይር አገር ይኖር የነበረ ሕዝብ፤ ዘፍ. 14፥6። 3. በኤዶም ዳርቻ የሚገኝ አሮን የሞተበት ተራራ፤ ዘኁ. 20፥22-29።

**መሃናይም፤** የቦታ ስም። ሁለት ጭፍራዎች ማለት ነው። የእግዚአብሔር መላእክት ከያዕቆብ ጋር በመሃናይም ተገናኙ፤ ዘፍ. 32፥2። የኢያቡስቴ መናገሻ ከተማ ነበር፤ 2ሳሙ. 2፥8። ዳዊት ከአቤሴሎም በሸሸ ጊዜ በመሃናይም ዐረፈ፤ 2ሳሙ. 17፥24፤ 19፥32። በገለዓድና በያቦቅ ወንዝ አጠገብ ይገኝ ነበር።

**መለመለ፤** 1. የተለዩ ሰዎችን ለሥራ መረጠ፤ 1ነገ. 9፥15:21። 2. የዛፍን ቅርንጫፍ ቈረጠ፤ ኢሳ. 18፥5።

**መለከት**፤ ከከብት ቀንድ ወይም ከብረትና ከብር ከሌላም የሚሠራ ለመጥሪያና ለመዘመሪያ ለአዋጅ መንገሪያም የሚያገለግል ዕቃ (ዘፍ. 4፥21፤ ኢያሱ 6፥20፤ ዘኍ. 10፥1-10፤ 2ዜ.መ. 5፥12:13)፣ ቀንደ መለከትም ይባላል፤ ይህም ከቀንድ መሠራቱን ያሳያል፤ 2ሳሙ.6፥15፤ 1ዜ.መ. 15፥28።



ሊቀ ካህናት መለከት ሲነፋ

**መለኮት**፤ ግዛትና መንግሥት፣ ክብርና ባሕርይ፣ አምላክነት፣ የእግዚአብሔር ልዩ ስም። ሌላም ትርጉም እንደ አንቀጹ ይኖረዋል። «አብ፣ ወልድና መንፈስ ቅዱስ በመለኮት አንድ ናቸው» ሲባል ከላይ የተገለጠውን የቃሉን ፍች ያመለክታል። ቃሉ ለእግዚአብሔር ብቻ እንጂ ለሌላ የሚነገር አይደለም፤ 2ጴጥ. 1፥3:4፤ ቈላ. 2፥9።

**መለየት**፤ በብ.ኪ. ዘመን በተቀደሰውና ባልተቀደሰው፣ በርኩሱና በንጹሑም መካከል የመለየት ሥራ የካህናት አገልግሎት ነበረ፤ ዘሌ. 10፥10። በሐ.ኪ. እውነተኛንና ሐሰተኛ ትምህርትንና መናፍስትን የመለየት ስጦታ ተሰጥቷል፤ ሁሉም እንዲፈተን የቤ.ክ. ሽማግሌዎች ኀላፊነት አለባቸው፤ 1ቆሮ. 12፥10፤ 14፥29፤ 1ተሰ. 5፥21፤ ዕብ. 5፥14። «ቅዱስ» ይመ.

**መላጣ**፤ በእግዚአብሔር ሕዝብ ዘንድ በማናቸውም ዓይነት ሰው ራስ ላይ ጸጉር ከሌለ እንደ ነውር፣ ውርደት ወይም ፍርድ ይቈጠር ነበር፤ 2ሳሙ. 10፥4-5፤ ኢሳ. 15፥2፤ 22፥12፤ ኤር. 47፥5። ኤልሳዕ በራ በመሆኑ ወይም በነቢይነት አገልግሎቱ ምክንያት ራሱን በመላጨቱ ሊሆን ይችላል፤ ዘኍ. 6፥18፤ 2ነገ. 2፥23፤ ሐ.ሥ. 18፥18።

**መላጥያ**፤ ከኢጣልያ አገር በስተደቡብ በታላቅ ባሕር የምትገኝ ደሴት። ጳውሎስ ታስሮ ወደ ሮም ሲሄድ መርከቡን ዓውሎ ነፋስ ስለሰባበረው ተሳፋሪዎቹ በዚች ደሴት ከረሙ፤ ሐ.ሥ. 27፥27-28፥10። በአሁኑ ዘመን ማልታ ተብላ ትጠራለች። ካ. 7ሠ።



መርከብ በማዕበል ኃይል ሲሰበር

**መልሕቅ**፤ ከብረት የተሠራ የመርከብ ማቆሚያ። «መርከብ»፣ ሥዕሉን በገጽ 28 ይመ.

**መልአክ፥ መላእክት**፤ የቃሉ ትርጉም መልእክተኛ ማለት ነው።

1. የተፈጥሮ ሁኔታቸው ፦ መላእክት በፍጥረታቸው ረቂቃን መናፍስት ናቸው። ሥጋና አጥንት ባይኖራቸውም፣ ማሰብ የሚችል ነፃ አእምሮ ስላላቸውና ስለሚታዘዙ መንፈሳዊ አካል አላቸው። አያገቡም አይጋቡም፤ ሉቃ. 24፥39፤ ማቴ. 22፥30። ብዛታቸው የማይቈጠር፣ ዕውቀታቸው ከፍ ያለ፣ ኃይላቸውም ታላቅ ነው፤ ራእ. 5፥11፤ ማቴ. 24፥36፤ መዝ. 103፥20። የእግዚአብሔር ልጆች፣ መናፍስት፣ ቅዱሳን ጠባቂዎችም ተብለው ይጠራሉ፤ ኢዮብ 1፥6፤ ዕብ. 1፥6-14፤ ዘካ. 14፥5፤ ዳን. 4፥13።

2. ደረጃቸው ፦ ኪሩቤልና ሱራፌል ልዩ የደረጃ ስም ተሰጥቷቸዋል፤ 2ሳሙ. 22፥11። ኢሳ. 6፥2:6፤ ይሁዳ 9። በስም የታወቁት ገብርኤልና ሚካኤል ናቸው፤ ዳን. 8፥16፤ 10፥13። በመጽሐፈ ሄኖክም ሩፋኤልና ፋኑኤል፤ እንዲሁም በመጽሐፈ ዕዝራ ሱቱኤል ዑርኤል በመባል የታወቁ መላእክት ይገኛሉ፤ ሄኖክ 10፥6-8፤ ዕዝ. ሱቱ. 2፥1።

3. አገልግሎታቸው ፦ ዋና ሥራቸው እግዚአብሔርን ማመስገን ነው፤ ኢሳ. 6፤ ራእ. 5፥11-12። ሰው

በኃጢአት ስለወደቀ ምእመናንን ያገለግላሉ፤ ዕብ. 1፥14። ንስሓ በሚገቡ ሰዎች ደስ ይላቸዋል፤ ሉቃ. 15፥10። እግዚአብሔርን የሚፈሩትን ይጠብቃሉ (መዝ. 34፥7)፥ ስለ ታናናሾቹ በእግዚአብሔር ፊት ይቆማሉ፤ ማቴ. 18፥10። በክርስቶስ ለሰዎች የተደረገውን ጥበብ ለማወቅ ይሻሉ፤ ኤፌ. 3፥10፤ 1ጴጥ. 1፥12። ብዙ ጊዜ የእግዚአብሔርን ቃል ሲገልጡ፤ በብዙ ዓይነት ሲያገለግሉ ኃጢአተኞችንም ሲቀጡ ይገኛሉ፤ ለምሳሌ ዘኁ. ም. 4፤ ዘፍ. ም. 19፤ 2ነገ. 19፥35። መላእክት ክርስቶስን አገለገሉ፤ ማር. 1፥13፤ ሉቃ. 22፥43። ሲያገለግሉ ብዙ ጊዜ በሰው መልክ ይታዩ ነበር፤ ዘፍ. 19፥1:12፤ ሉቃ. 24፥4:23፤ ዳን. 8፥15-26፤ 9፥21-27።

4. የወደቁ መላእክት፤ ቅዱሳን ሆነው ተፈጥረው ነበር፤ ዘፍ. 1፥31። ግን ከመካከላቸው ብዙዎች ኃጢአት ሠርተው ወደቁ፤ 2ጴጥ. 2፥4፤ ይሁዳ 6። እነርሱም ርኩሳን መናፍስት፥ አጋንንት ይባላሉ። አለቃቸው ሰይጣን ነው፤ ማቴ. 25፥41። ሰይጣንና መላእክቱ ምንም እንኳን በሰው ላይ ብዙ መጥፎ ነገር ቢሠሩ ከእግዚአብሔር ሥልጣን በታች ናቸው። በመጨረሻም ለዘላለም ይፈረድባቸዋል፤ ኢዮብ 1፥12፤ 2፥3-6፤ ማቴ. 12፥29፤ ራእ. 20፥2:10።


የተሰባበረ መርከብ በዐውሎ ነፋስ መልሕቁን ሲጥል

## መልአክ፥የእግዚአብሔር መልአክ

በብ.ኪ. ከእግዚአብሔር ቢላክም፥ እንደ እግዚአብሔር ሆኖ ተገልጧል፤ ሰዎች እግዚአብሔርን እንዳዩ አድርገው ቈጥረዋል። ዘፍ. 16፥7-13፤ ዘጸ. 3፥2-6፤ መሳ. 13፥11-23፤ 2ሳሙ. 24፥16፤ ዘካ. 1፥12:13። ከዚህ የተነሣ «የእግዚአብሔርን መልአክ» እግዚአብሔር ወልድ ነው የሚሉ አሉ። በአ.ኪ. ውስጥ ግን የእግዚአብሔር መልአክ ሲል ከመላእክቱ መካከል አንድን መልአክ እንጂ ወልድን አያመለክትም፤ ማቴ. 28፥2፤ ሉቃ. 1፥19፤ ራእ. 19፥10፤ 22፥8-9።

**መልእክተኛ፤** ሌላ የመገናኛ ዘዴ ባልነበረበት ዘመን መልእክትን የሚያደርስ ታማኝ ሰው አስደሳች ነበር፤ ምሳ. 25፥13። በተለይም እግዚአብሔር ቃሉን ለሕዝቡ ለማድረስ ነቢያትን መልእክተኛ አድርጎ ላከ። ዮሐንስ ከክርስቶስ በፊት መልእክተኛ ሆኖ መጣ፤ ሚል. 3፥1፤ ሐጌ. 1፥2-3።

**መልእክት፤** ጉዳይ የሚገልጽ ጽሑፍ ምንባብ፥ በወረቀትና በሌላም የሚጻፍ ወይም ቃል በቃል የሚነገር ማስረጃ። ሐዋርያት ቤተ ክርስቲያናትን ወይም ሰዎችን ለመጐብኘት ባልቻሉ ጊዜ መልእክትን በመጻፍ ትምህርትን ይሰጡ ነበር፤ በመልእክታቸውም ስሕተትን ይቃወሙ፥ አካሄድን ያርሙ ነበር፥ ያጽናኑ ነበር። በአ.ኪ. ዐሥራ አራት የጳውሎስ፥ የሌሎች በጠቅላላው 21 መልእክቶች ይገኛሉ። ሐዋርያት በአ.ኪ. ውስጥ ከሚገኙት ሌሎች መልእክቶችን የጻፉ ይመስላል፤ ሆኖም እነዚህ መልእክቶች አልተገኙም፤ 1ቆሮ. 5፥9።


በኤርምያስ ዘመን በዕብራይስጥ ቋንቋ በሸክላ ላይ ተጽፎ ከለኪሶ ከተገኘ መልእክት የተሣለ

**መልከ ጼዴቅ፤** የጽድቅ ንጉሥ ማለት ነው። የሳሌም ንጉሥ ነበር። ይህም የሰላም ንጉሥ ማለት ነው። ምናልባትም «ሳሌም» ኢየሩሳሌም ይሆናል። የእግዚአብሔርም ካህን ነበር፤ ዕብ. 7፥1-3። አብርሃም ከጦርነት በተመለሰ ጊዜ መልከ ጼዴቅ ባረከው፤ አብርሃምም ከሀብቱ ሁሉ ዐሥራትን ሰጠው፤ ዘፍ. 14፥18-20። የክርስቶስ ክህነት በመልከ ጼዴቅ ሥርዓት ተገልጧል፤ መዝ. 110፥4።

ክህነቱ ከአሮን ክህነት እንደሚበልጥ ተጽፎለታል። ይህም አንደኛ፥ በሥጋዊ ትውልድ ሳይሆን በእግዚአብሔር መሐላ በመሾሙ፤ ዕብ. 5፥5:6፤ 7፥13-17። ሁለተኛ በሞት ሳይወሰን ለዘለዓለም በማገልገሉ ነው፤ ዕብ. 6፥20፤ 7፥3:23-25። ክርስቶስ እንደ መልከ ጼዴቅ በእግዚአብሔር ሊቀ ካህናት በመባሉ የአሮንን ክህነት አስቀርቷል፤ ዕብ. 5፥7-10፤ 7፥11-19።

**መልክ፤** ቃሉ ብዙ ትርጉም ሲኖረው መሠረታዊ ትርጉሙ ከራስ እስከ እግር ያለውን የሰውን አቋም ይገልጣል። በተለይ በመ.ቅ. በሦስት መንገድ ይነገራል። 1. ዓይነት፥ ሁኔታ፥ አቋም፥ ቅርጽ፤ 2ሳሙ. 14፥20፤ ኢሳ. 52፥14፤ 53፥2፤ ዳን. 2፥31፤ ማቴ. 22፥20። 2. እንደ ጥላ የሌላውን ምሳሌ መያዝ። ሰው በእግዚአብሔር መልክ ተፈጠረ፤ ዘፍ. 1፥26። «የእግዚአብሔር አርአያ» ይመ.። ምእመናን የክርስቶስን መልክ ሊመስሉ ይገባቸዋል፤ ሮም 8፥29፤ 2ቆሮ. 3፥18። የአምልኮት መልክ ሲል ሥርዓት ማለት ነው፤ 2ጢሞ. 3፥5። 3. እውነተኛ ምሳሌ። ክርስቶስ በእግዚአብሔር መልክ ሆኖ በሰው መልክ ተገለጠ፤ ፊል. 2:6:7።

**መሐላ፤** ሰው የሚናገረው ቃሉ እውነተኛ መሆኑን ለማረጋገጥ የእግዚአብሔርን ስም ወይም ሌላ ነገርን ይጠራል። ይህም ምስክር እንዲሆንለት ነው። እንደዚሁም እውነትን ካልተናገረ ወይም ቃሉን ባይፈጽም መሐላው በሚምለው ላይ እንዲመለስበት ይጠይቃል ማለት ነው፤ ዘፍ. 21፥23፤ ዘጸ. 22፥11፤ 1ነገ. 8፥31-32፤ ነህ. 10፥29፤ ዘካ. 5፥3። መሐላ በልዩ ልዩ ዓይነትና መንገድ ተሰጥቷል፤ ዘፍ. 14፥22፤ 24፥2-3፤ 1ሳሙ. 20፥23፤ ኤር. 34፥18:19። ክርስቲያን ሁልጊዜ እውነትን መናገር ይገባዋል፤ ሲምልም በተፈጠረው ሳይሆን በእግዚአብሔር ብቻ መሆን አለበት። ደግሞም የእግዚአብሔርን ስም በከንቱ መጥራት አይገባም። ስለ ከባድ ነገር ቃሉን ለማረጋገጥ መሐላ ቢፈቀድም፥ በተራ ንግግሩ ሳይምል ቃሉ «አዎ አዎ» እና «አይደለም አይደለም» ብሎ እውነትን መናገር እንዳለበት ክርስቶስ አስተምሯል፤ ማቴ. 5፥33-37፤ 2ቆሮ. 11፥31፤ ገላ. 1፥20፤ ዕብ. 6፥16-18። «መርገም» ይመ.

**መሐሪ፤** እግዚአብሔር ትክክለኛ ፈራጅ ሆኖ ሳለ መሐሪ በመሆኑ ሰዎችን እንደሚገባቸው አይቀጣቸውም፥ መልካም ነገርንም ያደርግላቸዋል፤ ለተከታዮቹም ምሳሌ ነው፤ ዘጸ. 34፥6፤ ማቴ.5፥7።

**መመለስ፤** 1. በብ.ኪ. ሕዝቡ ጥፋት ከሠሩ በኋላ ወደ እግዚአብሔር ሲመለሱ ባዕድ አምልኮትን ትተው፥ ቃል ኪዳኑን አሳደሱ፥ የእግዚአብሔርንም ትእዛዛት ጠበቁ፥ በተመለሱም ጊዜ እግዚአብሔር ባረካቸው፤ 2ነገ. 17፥13፤ 23፥25፤ ኢሳ. 19፥22፤ ኤር. 3፥12፤ ዮናስ 3፥7-10፤ ሚል. 3፥7። የእስራኤል ሕዝብ የቃል ኪዳን ሕዝብ ናቸውና ሲመለሱ በአንድነት ቃል ኪዳን አደረጉ፤ ኢያሱ 24፥25፤ 2ነገ. 11፥17፤ 2ዜ.መ. 15፥12፤ 29፥10፤ 34፥ 31። እውነተኛ መመለስ ኀዘንን መግለጥና የሚታየውን አድራጎት መለወጥ ብቻ ሳይሆን የልብ ለውጥ ጭምር አለበት፤ ዘዳ. 4፥29-31፤ 30፥2-10፤ ኤር. 24፥7። ሰው ወደ እግዚአብሔር ሲመለስ የተሰበረ ልብ የተዋረደም መንፈስ ይኖረዋል፤ ይህም በዳዊት (2ሳሙ. 12፥13-16፤ መዝ. 51፥17) በንዕማን (2ነገ. 5፥11-15)፥ በምናሴም ይታያል፤ 2ዜ.መ. 33፥10-13። ሰው ወደ እግዚአብሔር የሚመለሰው በእግዚአብሔር ቀስቃሽነት ነው፤ ኤር. 31፥18፤ ሰ.ኤ. 5፥21።

2. በአ.ኪ. ንስሐ በማለት የመመለስ አሳብ ይገለጣል። መመለስ ንስሐንም እምነትንም በአንድነት ሊያመለክት ይችላል፤ ማቴ. 18፥3፤ ሐ.ሥ. 3፥19። ሰዎች አንድ በአንድ እንደተመለሱ ይተርካል። ከሁሉም የታወቀ የጳውሎስ መመለስ ነው፤ ሐ.ሥ. ም.9። ሰው በራሱ የእግዚአብሔርን ነገር አያስተውልም (1ቆሮ. 2፥14)፥ እግዚአብሔርን አይፈልግም፤ (ሮም 3፥11፤ 8፥7)፥ የሞተ ነውና በራሱ ሊመለስ አይችልም፤ ኤፌ. 2፥1። ሰው ንስሐ እንዲገባና በወንጌል እንዲያምን እግዚአብሔር በሕይወቱ ይሠራል፤ ዮሐ. 16፥8፤ 1ቆሮ. 2፥4፤ 1ተሰ. 1፥5። ይህም ሥራ ዳግመኛ መወለድ (ዮሐ. 1፥13፤ 3፥3-8)፥ አዲስ ፍጥረት (2ቆሮ. 5፥17፤ ኤፌ. 2፥10)፥ ልብን መክፈት (ሐ.ሥ. 16፥14)፥ ሕይወትን መስጠት (ኤፌ. 2፥5)፥ የታወረውን ልቡና ማብራት (2ቆሮ. 4፥4-6)፥ ልቡናንም መስጠት ይባላል፤ 1ዮሐ. 5፥20። ሰዎች በኃጢአታቸው ንስሐ እንዲገቡና በወንጌል እንዲያምኑ ታዝዘዋል፤ ማር. 1፥14-15፤ ሐ.ሥ. 2፥37-41፤ 3፥14-20፤ 8፥35-38፤ 20፥20-21፤ 1ተሰ. 1፥9-10። «ንስሐ»፥ «እምነት» ይመ.

**መማፀኛ ከተማዎች፤** በስሕተት (በአደጋ) ነፍስ የገደለ ከደም ተበቃዩ የሚሸሽበት ከተማ። በእስራኤል ስድስት ከተማዎች ለዚህ ተግባር ተመድበው ነበር። እነርሱም ፦ ኬብሮን፥ ሴኬም፥ ቃዴስ፥ ቦሶር፥ ራሞት፥ ጎላን ናቸው። ነገሩ ተጠንቶ ሰውየው ከደም ንጹሕ ሆኖ ሲገኝ ሊቀ ካህናቱ እስኪሞት ድረስ በመማፀኛው ከተማ መቆየት ነበረበት፤ ዘኍ. 35፥9-15፤ ዘዳ. 19፥4-13፤ ኢያሱ 20።

**መምሬ፤** በኬብሮን አጠገብ ያለ ቦታ። የአድባር ዛፍ ነበረበት፤ ቦታው በአብርሃም ወዳጅ በአሞራዊው በመምሬ ስም ተጠርቷል፤ ዘፍ. 13፥18፤ 14፥13። አብርሃም በመምሬ ሦስት እንግዶችን ተቀበለ፤ ዘፍ. 18፥1። በመምሬም የመቃብር ቦታ ገዛ፤ ዘፍ. 23፥17። አብርሃምና ይስሐቅ ለረጅም ጊዜ በዚህ ኖሩ፤ ዘፍ. 35፥27።

**መሞት፤** (ለኃጢአት)፤ ከኃጢአት መለየት፥ ከኃጢአት ሥልጣንና ኃይል መውጣት ማለት ነው። ክርስቶስ በሞቱ ኃጢአትን አጠፋ፥ ከኃጢአት ዓለም ወጣ። እንደዚሁም ምእመናን በክርስቶስ ከኃጢአት ዓለም ወጥተዋል፤ ሮም 6፥2:10-11።

**መሠረት፤** ግድግዳ ወይም ሕንፃ የሚቆምበት። በምሳሌ ረገድ ክርስቶስ የምእመናን የሕይወታቸው መሠረት ይባላል፤ 1ቆሮ. 3፥10-15። እንደዚሁም የነቢያት፤ የሐዋርያትም ትምህርትና ሥራ የቤ.ክ. መሠረት ይባላል፤ ኤፌ. 2፥20-22፤ ራእ. 21፥14-20።

**መሠዊያ፤** ሰው መሥዋዕት የሚያቀርብበት፥ ከእንጨት ወይም ከድንጋይና ከሌላም የሚሠራ። ቃየልና አቤል ኪሩቤል በነበሩበት ከገነት በስተምሥራቅ መሥዋዕትን አቀረቡ፤ ዘፍ. 3፥24-4፥4። አባቶች በልዩ ልዩ ቦታዎች በተለይ እግዚአብሔር ለእነርሱ በተገለጠላቸው ቦታዎች መሠዊያቸውን ሠሩ። ኖኅ (ዘፍ. 8፥20)፥ አብርሃም (ዘፍ. 12፥6-8፤ 13፥18፤ 22፥9)፥ ይስሐቅ (ዘፍ. 26፥25)፥ ያዕቆብ (ዘፍ. 33፥20፤ 35፥1-7)፥ ሙሴ (ዘጸ. 17፥15) መሠዊያዎችን እንደሠሩ እናነባለን። እስራኤላውያን ከጭቃና ብረት ካልነካቸው ድንጋዮች መሠዊያዎችን ሠሩ፤ ዘጸ. 20፥24-26፤ 24፥4፤ ኢያሱ 8፥30-31፤ መሳ. 6፥24-26። ለመገናኛ ድንኳን የሚሆኑ በናስ የተለበጠ የሚቃጠል መሥዋዕት መሠዊያና በወርቅ የተለበጠ የዕጣን መሠዊያ ከእንጨት ተሠሩ፤ ዘጸ. 30፥1-10፤ 38፥1-7። እስራኤል ወደ ከነዓን ሳይገቡ ከነዓናውያን ብዙ ዓይነት መሠዊያዎችን ሠርተው ነበርና እስራኤል ከእግዚአብሔር ሲርቁ እንደ እነርሱ መሠዊያዎችን ሠሩ፤ «ኰረብታ» ይመ.



ሰዎች ለመሥዋዕት የሚሆነውን በግ ሲያርዱ

ሮማውያን ቤተ መቅደስን በ70 ዓ.ም. ባፈረሱ ጊዜ የአይሁድ መሥዋዕት ቀረ። ለክርስቲያን ግን መሥዋዕቱም፥ መሠዊያውም መሥዋዕት አቅራቢውም ክርስቶስ ነውና ሌላ አያስፈልገውም፤ ዕብ. 13፥10። አሁን እግዚአብሔር መሥዋዕታችንንና ጸሎታችንን እንደሚቀበል ዮሐንስ በቤተ መቅደስ በነበሩት መሠዊያዎች ምሳሌነት ይገልጣል፤ ራእ. 6፥9-11፤ 8፥3-5።

**መሥዋዕት፤** ሰው ለአምላኩ አንዳች ነገር ቢሰጥ ወይም ቢያቃጥል ያ ነገር መሥዋዕት ወይም ቍርባን ይባላል። መሥዋዕቱም እንደ ሥርዓቱ ዓይነት ሲሠዋ መሠዋቱ ልዩ ልዩ አሳብ ሊገልጥ ይችላል። ለምሳሌ በአምላክ ፊት ተቀባይነትን ለማግኘት ወይም ለማጠንከር ይሆናል፤ እንዲሁም የሰጪውን እምነት ወይም ንስሐ፥ ምስጋና ወይም ፍቅር ያሳያል። መሥዋዕትን ያቀርቡ የነበሩ ሰዎች አንድ እግዚአብሔርን የሚያመልኩት እስራኤላውያን ብቻ ሳይሆኑ አረማውያንም ደግሞ ለጣዖቶቻቸው ያቀርቡ ነበር።

1. በብሉይ ኪዳን። ቃሉ ለመጀመሪያ ጊዜ በዘፍ. 4፥4 ላይ ይገኛል። እንዲሁም መሠረተ አሳቡ በዘፍ. 3፥21 ላይ ተገልጧል። ከሙሴ በፊት የጥንት አባቶች ለእግዚአብሔር ይሠው ነበር፤ ዘፍ. 4፥4፤ 8፥20፤ 12፥7። በኦሪት ሕግ ግን የካህናት ወገኖች ብቻ እንዲሠዉ ተፈቅዶላቸዋል፤ ዘኁ. 3፥10። የኦሪትም መሥዋዕቶች ከሥጋ፥ ከእህልና ከመጠጥ ነበሩ። ከሥጋም ሲሆን ነውር ከሌላቸው ንጹሓን ከተባሉ እንስሶችና ወፎች መሆን ነበረበት፤ ዘፍ. 8፥20፤ ዘሌ. 22፥17-25።

እግዚአብሔር ከእስራኤል ያዘዛቸው መሥዋዕቶች አምስት ዓይነት ናቸው፤ እነዚህም የሚቃጠል መሥዋዕት፥ የእህል ቍርባን፥ የደኅንነት መሥዋዕት፥ የኃጢአት መሥዋዕትና የበደል መሥዋዕት ናቸው፤ ዘሌ. ም. 1-5።

የመሥዋዕት አቀራረብ ሥነ ሥርዓት በእንስሳት ሲፈጸም፥

(ሀ) እንስሳው ንጹሕ የሆነ፥ እንከን የሌለበት ነበረ፤ ዘጸ. 12፥5፤ ዘሌ. 22፥24:25፤ 1ጴጥ. 1፥18:19።

(ለ) አቅራቢው እጁን በእንስሳው ራስ ላይ ይጭናል፤ ዘሌ. 1፥4። ይህን በማድረጉ በምሳሌነት ራሱን ከእንስሳው ጋር አንድ ያደርጋል፥ ኃጢአቱንም ያሸክመዋል፤ ዘሌ. 16፥21፤ ኢሳ. 53፥6፤ 1ጴጥ. 2፥24።

(ሐ) አቅራቢው ያርደዋል፥ የኃጢአት ደመወዝ ሞት ነውና፤ ሮም 6፥23፤ ዕብ. 9፥28።

(መ) ካህን የመሥዋዕቱን ደም በእግዚአብሔር ፊት ያቀርባል፤ ዘሌ. 1፥5፤ 17፥11፤ ዕብ. 9፥12።

(ሠ) ካህን ከእንስሳው እንደ መሥዋዕቱ ዓይነት ልዩ ልዩ ክፍልና ብልት ያቃጥላል። ይህ በምሳሌነት አቅራቢው ራሱን ለእግዚአብሔር አገልግሎት እንደሚያቀርብ ይገልጣል፤ ዘፍ. 8፥21፤ ሮም 12፥1፤ 2ቆሮ. 2፥14-16፤ ኤፌ. 5፥2።

(ረ) ካህን አንዳንድ ጊዜም አቅራቢው ከእንስሳ ያልተቃጠለውን በመሠዊያ አጠገብ ይበላል፤ ዘሌ. 6፥26። ይህም በመሥዋዕቱ መሠረት ከእግዚአብሔር ጋር ኅብረት እንዳለው ያሳያል፤ 1ቆሮ. 10፥14-22፤ ይሁዳ 12።

2. በአዲስ ኪዳን።

(ሀ) የክርስቶስ መሥዋዕት፤ የኢየሩሳሌም ቤተ መቅደስ በሮማውያን እጅ እስከ ፈረሰ ድረስ (በ70 ዓ.ም.) አይሁድ የደም መሥዋዕቶችን ይሠዉበት ነበር። ከዚያ በኋላ ግን ቀርቷል። ታላቁ የአ.ኪ. መሥዋዕት ኢየሱስ ክርስቶስ ራሱ ነው። ሕይወቱን

በመስቀል ላይ ሲሠዋ የብ.ኪ. መሥዋዕቶች ሁሉ በእርሱ ተፈጽመዋል፤ ዮሐ. 1፥29፤ ዕብ. 7፥27፤ 9፥13፤ 10፥3-14። ምክንያቱም እነርሱ የክርስቶስ መሥዋዕት ምሳሌና ጥላ ብቻ ነበሩና፤ ቈላ. 2፥16:17፤ ዕብ. 8፥1-7። ክርስቶስ የተሠዋ እውነተኛው የፋሲካ በግ በመሆኑ ነውና (1ቆሮ. 5፥6-8)፥ በእርሱ ደም እንድናለን፤ ሮም 5፥9፤ 1ጴጥ. 1፥18:19፤ 1ዮሐ. 1፥7።

(ለ) የክርስቲያን መሥዋዕት፤ ክርስቲያን የሚያቀርባቸው መንፈሳውያን መሥዋዕቶች አሉ፤ 1ጴጥ. 2፥5። እነርሱም የሚከተሉት ናቸው፤ ይኸል ሰውነቱን ለእግዚአብሔር አገልግሎት መስጠት (ሮም 12፥1)፥ ለመንፈሳዊ ሥራ የሚሆን ስጦታ (ፊል. 4፥18)፥ ምስጋናና ለጌታ መመስከር (ዕብ. 13፥15)፥ ጸሎት (ራእ. 8፥3-4)፥ ምሕረት፤ ማቴ. 12፥7፤ ዕብ. 13፥16። እነዚህ ሁሉ እግዚአብሔርን ደስ የሚያሰኙ ተግባሮች ናቸው እንጂ የኃጢአት ማስተስረያ መሥዋዕቶች አይደሉም።

**መረባርብ፤** አንባቢ መጽሐፍ የሚያነብበት በእንጨት ርብራብ የተሠራ መስበኪያ፤ ነህ. 8፥4።

**መረን፤** ስድነት፥ ያለ ሥርዓት መኖር። ከእግዚአብሔር የተገለጠ ነገር ባይኖር ዓለም ሥርዓት የሌለው ይሆን ነበር፤ ምሳ. 29፥18።

**መረግድ፤** አረንጓዴ ወይም ጥቁርና ነጭ ዐይነት የከበረ ድንጋይ፤ ዘጸ. 25፥7፤ ኢዮብ 28፥16፤ ሕዝ. 28፥13፤ ራእ. 21፥19።

**መረፈቅ፤** ለግብዣ በጠረጴዛ ዙሪያ መቀመጥ፤ 1ሳሙ. 16፥11።

**መሪሳ፤** ከለኪሶ ወደ ሰሜን የነበረ ከተማ። አንድ ሚሊዮን የኢትዮጵያን ሰዎች አሳ በመሪሳ አጠገብ አሸነፈ፤ 2ዜ.መ. 14፥8-14።

**መሪባ፤** ክርክር ማለት ነው። 1. እስራኤል በራፊዲም በውሃ እጦት ምክንያት ስለ ተከራከሩ ቦታው መሪባ ተባለ፤ ዘጸ. 17፥1-7። 2. በቃዴስ አጠገብ ሳሉ እስራኤላውያን ስለ ውሃ እጦት ከሙሴ ጋር ተከራከሩ። በዚህ ጊዜ ሙሴና አሮን እግዚአብሔርን ስላከበሩምና ወደ ከነዓን ለመግባት አልተፈቀደላቸውም። ቦታውም መሪባ ተባለ፤ ዘኍ. 20፥1-13።

## መራ፥ ምሪት፥ የእግዚአብሔር አመራር፤

እግዚአብሔር ሕዝቡን ይመራል፤ ዘጸ. 40፥36-38፤ ሮም 8፥14። እግዚአብሔር ለሚታዘዙለት አንድ ጊዜ ፈጽሞ የተሰጠ ሃይማኖት ገልጧልና ማድረግ የሚገባቸውን አሳይቷል፤ ይህም በመ.ቅ. ተጽፎ ይገኛል፤ ይሁዳ 3። ሰውም ለግል ሕይወቱና ለአገልግሎቱ የእግዚአብሔርን ፈቃድ መፈለግ አለበት፤ ዘዳ. 29፥29፤ ምሳ. 3፥5-6። እግዚአብሔር በብ.ኪ. ዘመን በሕልም፥ በራእይ፥ በመልአክ፥ በደመናና በእሳት ዓምድ፥ በተአምር፥ በኡሪምና በቱሚም፥ በዕጣ፥ በድምፅ፥ በነቢይ ቃል፥ በሰው ምክር፥ በሁኔታዎች መመቻቸት፥ የእግዚአብሔርን ቃል በማንበብ ... ወዘተ. ሕዝቡን ሲመራ በመ.ቅ. ታሪክ እናያለን፤ ዕብ. 1፥1።

በአ.ኪ. ዘመን እነዚህ ከሥተቶች ቢገኙም፥ ዋና ትኩረት የሚሰጠው ለመንፈስ ቅዱስ መሪነት ነው፤ ሐ.ሥ. 2፥17-18፤ 8፥29:39፤ 10፥19፤ 11፥12:28፤ 15፥28፤ 16፥6-7፤ 21፥4፤ 1ቆሮ. 2፥13። መንፈስ ቅዱስ አንዳንድ ጊዜ በነቢይ አማካይነት ቢናገርም፥ ብዙ ጊዜ የአማኙን አሳብና መንፈስ በመቃኘት ፈቃዱን ይገልጣል። የመንፈስ ቅዱስን መሪነት ከሌላ መንፈስ ለመለየት የምንችለው፥ አሳቡ፥ ሀ) መሠረታውያን የሆኑ መጽሐፍ ቅዱሳዊ እውነቶችን የማይቃረን፥ ለ) በቤ.ክ. መሪዎችና በጸሎት ጓደኞች የሚደገፍ፥ ሐ) ከሁኔታዎች መመቻቸት ጋር የሚስማማ ሲሆን ነው። በመጨረሻ አሳቡ ከእግዚአብሔር ሲሆን የክርስቶስ ሰላም እንደ ዳኛ ሆኖ የአማኙን ልብ ይገዛል፤ ቈላ. 3፥15። «መንገድ» ይመ.

**መራራ፥ ማራ፤** ጣፋጭ ያልሆነ የቅጠል ወይም የውሃ ጣዕም፤ ከባድ ሐዘን በምሳሌ የሚገለጥበት ቃል፤ ዘጸ. 12፥8፤ 15፥23፤ ሩት 1፥20፤ ማቴ. 26፥75።

**መራጃ፤** የድንጋይ መሰበሪያ ትልቅ መዶሻ፤ 1ነገ. 6፥7።

**መርበብ፤** 1. ወጥመድ፥ አሸክላ፤ ምሳ. 29፥5። 2. የራስ መሸፈኛ ሰርመዴ፤ ኢሳ. 3፥18። 3. የጐልላት ልባስ፤ 1ነገ. 7፥17:18፤ 2ዜ.መ. 4፥13።



ዓሣ የሚጠመድበት መርበብ (መረብ)

**መርከብ፤** የእስራኤል ሕዝብ በግብርና ሥራ ይተዳደሩ ስለነበር በመርከቦች ብዙም አይጠቀሙም ነበር። ሆኖም ወሰንተኞቻቸው የጢሮስና የሲዶና ሰዎች የታወቁ መርከበኞች ነበሩ። ሰሎሞን የጢሮስን ሰዎች ቀጥሮ በኤርትራ ባሕር በመርከቦች ይነግድ ነበር፤ 1ነገ. 9፥26-28። ኢዮሳፍጥ ይዞ ሲሞክር መርከቦቹ ወደ ያው ተሰበሩ፤ 2ዜ.መ. 20፥35-37። የጢሮስ

ሰዎች እስከ እንግሊዝ አገር በመርከቦቻቸው ይነግዱ ነበር። ግብጻውያን ከደንገል መርከቦቻቸውን ይሠሩ ነበር፤ ኢሳ. 18፥2። ሮማውያን በብዙ መቅዘፊያዎች የሚነዱ መርከቦች ነበሩአቸው። ታላላቅ የጭነት መርከቦች ግን መጋረጃዎቻቸው ተዘርግተው በነፋስ ይነዱ ነበር። ጳውሎስ ወደ ሮም የሄደባት መርከብ ከጭነትዋ በላይ 276 ሰዎች ይዛ ነበርና ተሰበረች፤ ሐ.ሥ. 27። በታላቁ ባሕር በተለይ ከመስከረም እስከ የካቲት ወር ድረስ መሄድ አደገኛ ነበር። ጳውሎስም ሮም ሳይደርስ የተሳፈረባቸው መርከቦች ሦስት ጊዜ ተሰበሩበት፤ 2ቆሮ. 11፥25። መሪው መርከቦችን በስተኋላ በሚገኝ በአንድ መቅዘፊያ ይመራ ነበር፤ ያዕ. 3፥4:5። የሰው አንደበት መርከብንና በመርከብ ያሉትን ሰዎች ሁሉ ሊመራ በሚችል መቅዘፊያ ይመስላል። መርከብ 3 ወይም 4 ከብረት የተሠሩ መልሕቆች አሉአት። መርከብዋ ወዲያና ወዲህ ተገፍታ እንዳትሰበር መልሕቆቹን በረጅም ገመድ ወደ ጥልቁ ባሕር ሲያወርዱ መርከብዋ ትቆም ነበር። የክርስቲያን ተስፋ የማይናወጥ ስለሆነ በመልሕቅ ይመሰላል፤ ዕብ. 6፥19። «ጀልባ»፥ «መልሕቅ»፥ «መቅዘፊያ»፥ «የኖኅ መርከብ» ይመ.



መርከብ በሸራና በመቅዘፊያዎች ሲነዳ

**መርዝ**፤ የብ.ኪ. ሰዎች መርዝ በአንዳንድ ቡቃያ ላይ እንደሚገኝ (ሆሴዕ 10፥4)፥ የበረሃ ቅል መርዝ እንዳለበት (2ነገ. 4፥39:40)፥ የእባብ (ዘዳ. 32፥24:33)፥ የእፉኝትም ምላስ (መዝ. 140፥3) አደገኛ መሆኑን ያውቁ ነበር። የኃጥእን ቍጣና ንግግር በመርዝ ተመስሏል (መዝ. 58፥4፤ 140፥3፤ ያዕ. 3፥8)፥ የእግዚአብሔር ተግሣጽም እንደ መርዝ ነው፤ ኢዮብ 6፥4። እግዚአብሔር የወንጌል መልእክተኞችን ከመርዝ ሊያድናቸው ይችላል፤ ማር. 16፥18።

**መርዶክዮስ**፤ በአይሁድ ጊዜ ወደ ባቢሎን ከተማረኩት አንዱ፥ በፋርስ ቤተ መንግሥት በሱሳ ይኖር የነበረ ብንያማዊ ሰው፤ አስ.2፥5:6። ያሳደጋትን የአጎቱን ልጅ አስቴርን ንግሥት እንድትሆን እስቦ ለምርጫ አቀረባት፤ አስ. 2፥7-11። ንጉሥ አርጤክስስን ከሞት አዳነው፤ አስ. 2፥21-23። ለሐማ አልሰግድም በማለቱ አስቈጣው፤ አስ. 3፥1-6። አይሁድን ከሞት እንድታድን አስቴርን አነሣሣት፤ አስ. 4። በሐማ ምትክ ባለሥልጣን ሆኖ አዲስ ሕግ በማሳወጅ አይሁድን አዳነ፤ አስ. 8፥1-9፥19። «ፉሪም» የሚባል ዓመት በዓል እንዲከበር አዘዘ፤ አስ. 9፥20-32።

**መርገም**፤ በሌላው ላይ ክፉ ነገር እንዲደርስ መመኘትና መናገር። በብ.ኪ. ለእግዚአብሔር የማይታዘዙ ሲረገም የእስራኤል ሕዝብም አሜን ብለው ርግማንን አረጋገጡ፤ ዘዳ. 27፥11-26። ሰው የሚረገምባቸው ነገሮች በዘዳ. 28፥15-68 ተዘርዝረዋል። ሴቶች በእርግማን መሐላ ይፈተኑ ነበር፤ ዘኍ. 5፥11-28። ኢዮብ ሰውን በመራገም ኃጢአትን አላደረገም፤ ኢዮብ 31፥30።

ክርስቲያን ሲሰደድ እንዲመርቅ እንጂ እንዳይረግም ታዝዟል፤ ማቴ. 5፥44፤ ሮም 12፥14። ጳውሎስ ወንጌልን የሚያጣምሙትን ረገመ፤ ሐ.ሥ. 13፥11፤ ገላ. 1፥6-9። የእግዚአብሔርን ሕግ ሁሉ የማይፈጽም የተረገመ ነው፤ ክርስቶስ ግን በመስቀሉ ምእመናንን ከሕግ ርግማን አድኗል፤ ገላ. 3፥10:13። «መሐላ» ይመ.

**መርግ**፤ የድንጋይ ናዳ። በጥንት ጊዜ ሰዎች ትልቅ ምሽግ ወይም ግንብ ሠርተው ከዚያ ላይ መርግ በማንከባለል ጠላታቸውን ይከላከሉ ነበር፤ 2ዜ.መ. 26፥15።

**የመርፌ ቀዳዳ**፤ ኢየሱስ «...ግመል በመርፌ ቀዳዳ ቢገባ ይቀላል» ሲል ነገሩ ከባድና ብዙ ጊዜ የማይሆን መሆኑን በምሳሌ ይገልጣል፤ ማቴ. 19፥24።

**መሰንቆ**፤ አውታርና መከርከሪያ ያለው የዜማ ዕቃ። በመ.ቅ. ውስጥ ለእግዚአብሔር ክብር እንደሚዘመርበት ብዙ ጊዜ ተጠቅሷል፤ 1ዜ.መ. 15፥16፤ ኢዮብ 30፥31፤ መዝ. 92፥3፤ 150፥3።

**መሲሕ**፤ በዕብራይስጥ «የተቀባ» ማለት ነው። «ክርስቶስ» ከሚለው የግሪኩ ቃል ጋር አንድ ነው። በብ.ኪ. እግዚአብሔር የቀባው ሲል በተቀደሰ ዘይት የተቀቡትን ነገሥታትና ካህናት ያመለክታል፤ 1ሳሙ. 26፥9፤ 1ዜ.መ. 16፥21። እግዚአብሔር በተቀቡት አድሮ እስራኤልን ያድን ነበር፤ እውነተኛ መሲሕ እስከሚላክ ድረስ ሕዝቡ በእምነትና በተስፋ ይኖሩ ዘንድ እግዚአብሔር እነዚህን በብ.ኪ. የተቀቡትን መሪዎች የመሲሑ ጥላዎች አድርጎ ላካቸው። በተጨማሪም መዳን ከምድራዊ ጠላት ብቻ ሳይሆን ከኃጢአትና ከሞት ጭምር መሆኑን እንዲያስተውሉ በነቢያት አፍ አስተማራቸው፤ ኢሳ. 11፥1-5፤ 53፥4-6። ጊዜው ሲደርስም እውነተኛውን መሲሕ ጌታ ኢየሱስን ላከ፤ ገላ. 4፥4-5።

ኢየሱስ ሲያስተምር ሮማውያንን እንደሚያስወጣና ነፃነትን እንደሚያውጅላቸው ተስፋ ያደርጉ ነበር። አምስት ሺህ ሰዎችንም ከመገቡ በኋላ

ሊያነግሡት ፈልገው ነበር። ሕዝቡ «ሆሣዕና ለዳዊት ልጅ» እያሉ ምድራዊ ንጉሥ እንዲሆንላቸው ፈለጉ፤ ማቴ. 21፥9።

ይህ ተስፋ ስለነበራቸው ኢየሱስ በሕዝብ ፊት ብዙ ጊዜ «እኔ መሲሕ ነኝ» ሳይል «የሰው ልጅ» በሚለው ስሙ በመጠቀም ስለ መንግሥቱ አስተማረ። እነርሱ ግን መሲሑ ከመንገሡ በፊት አስቀድሞ በትሕትናና በብዙ መከራ ማለፍ እንደነበረበት አልተረዱም፤ ኢሳ. 52፥13-53፥12፤ ዘካ. 9፥9፤ ሉቃ. 24፥26:46-48። የሚመሠርተውም መንግሥት ምድራዊ የፖለቲካ መንግሥት ሳይሆን እስከ ዳግም ምጽአቱ መንፈሳዊ መንግሥት ሆኖ፥ በዳግም ምጽአቱ ጊዜ ደግሞ ሰማይንና ምድርን የሚጨምር መሆኑን አልተረዱም ነበር፤ ማቴ. 19፥28-30፤ 2ጴጥ. 3፥13። ክርስቶስ አሁን በአብ ቀኝ በመቀመጡ የንጉሥነት ሥልጣን አለው፤ ማቴ. 28፥18፤ ሐ.ሥ. 2፥29-33። ስለዚህ ምእመናን ብቻ ንጉሥነቱን አሁን ቢያስተውሉትም፥ በዳግም ምጽአቱ ጊዜ ግን ሁሉ ንጉሥነቱን ዐውቀው ይሰግዱለታል፤ ፊል. 2፥9-11፤ ራእ. 6፥15-17። «ቀባ» ይመ.

**መሳሳም፤** ወዳጅነትን (ዘፍ. 29፥11:13፤ ማቴ. 26፥48)፥ ፍቅርን (መ.መ. 1፥2፤ ሉቃ. 15፥20)፥ ፍትወትን (ምሳ. 7፥5:13)፥ አምልኮትንና አክብሮትን (1ነገ. 19፥18፤ ሆሴዕ 13፥2) ሊያሳይ ይችላል። በቤ.ክ. መሳሳም የተለመደ ሰላምታ ነው፤ ይህም የተቀደሰ መሆን ይገባዋል፤ ሐ.ሥ. 20፥37፤ ሮም 16፥16፤ 1ጴጥ. 5፥14።

**መሳን፤** አለመቻል፥ አቅም ማጣት፤ ዘፍ. 18፥14፤ ማቴ. 19፥26፤ ሉቃ. 1፥37።

**መሳደብ፤**

1. ሰውን መስደብ። ይህ የሰውን ክብርና ስም መንቀፍ ማለት ነው። ሰውን መስደብ ኃጢአት መሆኑ በብዙ ቦታ ተጠቅሷል፤ ማቴ. 5፥22፤ ማር. 7፥22፤ ኤፌ. 4፥31፤ ቲቶ 3፥1:2። ክርስቶስና ሐዋርያት አንዳንድ ጊዜ ኃይለ ቃል ቢናገሩም በምሳሌም ሆነ በግልጥ የሰውን ጠባይ እየገለጡ በሥልጣን አስተማሩ ወይም ገሠጹ እንጂ ተሳደቡ ማለት አይቻልም፤ ሉቃ. 13፥32፤ ሐ.ሥ. 23፥3። የእግዚአብሔር የሆነ ሁሉ አይሳደብም፤ ይሁዳ 8:9።

2. እግዚአብሔርን መሳደብ፤ የእግዚአብሔርን ክብርና ስም ወይም ሥራ መንቀፍና ማቃለል፤ መዝ. 74፥10፤ ኢሳ. 52፥5። በሙሴ ሕግ እግዚአብሔርን የሚሳደብ የሞት ፍርድ ተወስኖበት ነበር፤ ዘሌ. 24፥10-23፤ 1ነገ. 20፥10-13።

ክርስቶስ የእግዚአብሔር ልጅ ነኝ በማለት አምላክነቱን ሲያውጅ፥ የማያምኑት አይሁዳውያን እንደተሳደበ አድርገው ቈጠሩት፤ ዮሐ. 5፥17:18፤ ማቴ. 26፥64-66። በክርስቶስ ላይ የሚናገር ኃጢአቱ ሊሰረይለት ይችላል፤ ነገር ግን መንፈስ ቅዱስን የሚሰድብ አይሰረይለትም፤ ማቴ. 12፥31:32። ምክንያቱም ሰው የክርስቶስን ትስብእት ብቻ ተመልክቶ ሳያስተውል ሊሳደብ ይችላል፤ የመንፈስ ቅዱስን ሥራ ግን በመንፈሳዊ መንገድ ብቻ ማስተዋል ስለሚቻል አንድ ሰው መንፈስ ቅዱስን ቢሳደብ፥ ልቡ እልከኛ ሆኖ ንስሐ የማይገባ መሆኑን የሚያሳይ ይመስላል። ንስሐ የሚገባ ሰው መንፈስ ቅዱስን እንዳልተሳደበ ያረጋግጣል። ሰው ወደዚህ ሁኔታ የሚደርሰው እንደ ጻፎች የእግዚአብሔርን ሥራ ለሰይጣን ሰጥቶ የሰይጣንን አሳብ ሲከተል ነው፤ ማር. 3፥22-29። ሰው መንፈስ ቅዱስን ከመንቀፍ ደረጃ ሲደርስ ልቡ ይደነድናል፤ የእግዚአብሔርንም ነገር አይፈልግም፤ ዕብ. 6፥4-6። ግን አንድ ሰው ይህን ኃጢአት እንደሠራ ተሰምቶት የእግዚአብሔርን ነገር ከፈለገ ይህ ሰው መንፈስ ቅዱስን አልተሳደበም ለማለት ይቻላል። ምክንያቱም ይህን ኃጢአት ቢሠራ ኖሮ የእግዚአብሔርን ነገር ባልፈለገም ነበር።

**መሳዳ፤** ምሽግ አምባ ማለት ነው። መሳዳ የተባለው አምባ በጨው ባሕር አቅራቢያ ካለው መሬት 300 ሜትር ከፍ ይላል። ይህ አምባ በመ.ቅ. አልተጠቀሰም። ምናልባት ዳዊት ከሳኦል ሸሽቶ የኖረበት አምባ ሳይሆን አይቀርም፤ 1ሳሙ. 23፥14። ካ.5ሸ።

ዮናታን የተባለው ሊቀ ካህናት መጀመሪያ ምሽግ አደረገው። ቀጥሎም ሄሮድስ በታው በራሱ አገር በኤዶም ውስጥ ስለነበረ አስፋፋው። እንደማይደፈር ምሽግ ይቈጠር ነበር፤ ነገር ግን ሮማውያን በ72 ዓ.ም. ወደ ምሽጉ ለመድረስ ከእስራኤል የተገኙትን ብዙ ሺህ ባሪያዎች አስገድደው ከመሳዳ ሥር ባለ በአንድ ጉብታ ላይ ሰባ ሜትር ከፍታ ያለውን ክምር አስከመሩ። ሮማውያን ወደ ምሽጉ ከመግባታቸው በፊት በመሳዳ የነበሩ 967 አይሁድ ራሳቸውን ገደሉ።

**መሳፍንቱ፤** በብ.ኪ. ዘመን፥ ነገሥታት በእስራኤል ከመሾማቸው በፊት መስፍን የተባለው ከንጉሥ ዘር የሆነ ሰው ሳይሆን አገሪቱን ከጠላት ወረራ የሚያድን አዳኝ ጀግና ነበረ። የእስራኤል ሕዝብ ወደ ርስት አገራቸው ከገቡና ኢያሱ ከሞተ በኋላ እስራኤላውያን እግዚአብሔርን ትተው የአገሩን አማልክት በማምለክ በእግዚአብሔር ፊት ክፉ ሥራ ሠሩ፤ እግዚአብሔርም ተቈጣቸው፤ ወደ እርሱም ሊመልሳቸው ብሎ ለሚማርኩአቸው ወራሪዎች አሳልፎ ይሰጣቸው ነበር። ወራሪ በመጣ ቍጥር እስራኤላውያን ተጨንቀው ተጸጽተውም ወደ እግዚአብሔር ይጮኹና ይጸልዩ ነበር። በዚያን ጊዜ እግዚአብሔር ይምራቸውና መስፍንንም አስነሥቶ ከሚማርኩአቸው እጅ ያድናቸው ነበር፤ መሳ. 2፥11-19፤ 3፥9:15። እነዚህ የሚያድኑ መሳፍንት 12 ሲሆኑ ከኢያሱ መሞት ጀምሮ ሳኦል ንጉሥ ሆኖ እስኪሾም ድረስ 300 ዓመት ያህል አገሪቱን ጠበቁ። መሳፍንቱ የሚከተሉት ናቸው ፦ ጎቶንያል (3፥7-11)፥ ግራኙ ናዖድ (3፥12-30)፥ ሰሜጋር (3፥31)፥ ነቢይት ዲቦራና ባርቅ (4፥1-5፥31)፥ ጌዴዎን (6፥1-8፥35)፥ አቤሜሌክ (9፥1-57)፥ ቶላ (10፥1:2)፥ ኢያዕር (10፥3-5)፥ ዮፍታሔ (10፥6-12፥7)፥ ኢብጻን (12፥8-10)፥ ኤሎም (12፥11:12)፥ ዓብዶን (12፥13-15)፥ ሶምሶን (13፥1-16፥31)።

## መሳፍንት፥ መጽሐፈ መሳፍንት

የመሳፍንትን ታሪክ ይተርካል። መጽሐፉ በ3 ክፍል ይከፈላል ፦

1. መሳፍንት የተነሡበት ምክንያት፤ ም. 1-2።

2. የመሳፍንቱ ታሪክ፤ ም. 3-16።

3. ስለ ዳን ጭቆናና ስለ ብንያም ኃጢአት፤ ም. 17-21።

መጽሐፉን ማን እንደጻፈው፥ ምን ጊዜ እንደተጻፈ እርግጡ ባይታወቅም እንኳ የጻፈው ሳሙኤል፥ ወይም በሳሙኤል ዘመን ከነበሩት ከነቢያት ወገን አንዱ እንደሆነ ይታመናል፤ 1ሳሙ. 10፥10-12፥25።

**መስቀል**፤ «ስቅለት» ይመ.

**መስተዋት**፤ በጥንት ጊዜ ከጠራና ከነጠረ ናስ ይሠራ ነበር። ከብርጭቆ እንደሚሠራው እንደ ዛሬው መስተዋት መልክን በትክክል አያሳይም፤ ዘጸ. 38፥8፤ 1ቆሮ. 13፥12፤ ያዕ. 1፥23።

**መስቴ**፤ መጠጫ ጽዋ፤ ኤር. 48፥12።

**መስኮት**፤ በግድግዳና በግንብ ቤት ውስጥ በአራት ማዕዘን የተከበበ የብርሃንና የአየር ማስገቢያ። በጥንት ዘመን ብዙ ጊዜ የመስኮት መዝጊያ ይሠራ ነበር፤ መሳ. 5፥28፤ ሐ.ሥ. 20፥9፤ 2ቆሮ. 11፥33። በግጥም አጠቃቀም በሰማይ «መስኮቶች» ሲከፈቱ በሰቅሰቁ ውስጥ በመንጠባጠብ ፈንታ በርከት ያለ ዝናብ ወይም ሌላ ነገር ይወርዳል፤ ዘፍ. 7፥11፤ ሚል. 3፥10። «ሰቅሰቅ»፥ «ቤት» ይመ.

**መስጴጦምያ**፤ ቃሉ በሁለቱ ወንዞች መካከል ያለ ማለት ነው። መስጴጦምያ በጤግሮስና በኤፍራጥስ ወንዞች መካከል ከካራን እስከ ዑር ያለውን አገር ያመለክታል፤ ዘፍ. 24፥10፤ ዘዳ. 23፥3:4፤ 1ዜ.መ. 19፥6፤ ሐ.ሥ. 2፥9፤ 7፥2። ዛሬ መስጴጦምያ በሶርያና በኢራቅ ውስጥ ይገኛል። ካ. 1ለ።

**መስፈሪያ**፤ ዛሬ እንዳለ ሁሉ በጥንት ዘመንም ልዩ ልዩ መስፈሪያ ነበር። ከአሁኑ መስፈሪያ ጋር በትክክል ለማመዛዘን ያስቸግራል።



የደረቅ ነገር መስፈሪያዎች

1. የደረቅ ነገር መስፈሪያ፤ ቆሮስ የአህያ ጭነት መለኪያ ነው። ቆሮስን መነሻ በማድረግ የጥንት መስፈሪያዎችን መገመት ይቻላል። ኢፍ የቆሮስ ዐሥረኛ ነው፤ ሕዝ. 45፥11። ጎሞር የኢፍ ዐሥረኛ ነው፤ ዘጸ. 16፥36።

2. የፈሳሽ ነገር መስፈሪያ፤ ባዶስ። ባዶስና ኢፍ እኩል ናቸው፤ መስፈሪያው አንድ ይሆናል። ባዶስ የቆሮስ ዐሥረኛ ነው፤ ሕዝ. 45፥11:14። ኢን የባዶስ ስድስተኛ ነው። ሉግ የባዶስ ዐሥራ ሁለተኛ ነው። ብዙ ሊቃውንት ባዶስ 22 ሊትር ነው ብለው ይገምታሉ፤ አንዳንዶች 46 ሊትር ያህላል ይላሉ።



የፈሳሽ መስፈሪያ

**መስፍ**፤ አንጥረኛ ወይም ቀጥቃጭ ብረታ ብረት ከርሱ ላይ በማድረግ በመዶሻ የሚቀጠቅጥበት ከሥር ያለው ብረት ትንሹን ብረት ትልቅ፥ የታጠፈውን ብረት ዝርግና ሰፊ ለማድረግ የሚጠቀምበት መሣሪያ ነው፤ ኢሳ. 41፥7።

**መቀበል**፤ በአንድ ሌላ ወገን የሚቀርበውን ሰው፥ ሥራ፥ ስጦታ፥ አሳብ፥ አክብሮት ... ወዘተ አለመጣል፥ በእምነት፥ በአእምሮ፥ በስሜትና በፈቃድ፥ በሚገባ የራስ ማድረግ፤ ዮሐ. 1፥11-12፤ 20፥22።

**መቃ**፤ በወንዝ ዳር የሚበቅል፥ ቀርከሃን (ቀርቅሃን) የሚመስል፥ ለመጻፊያ ብዕር የሚቀረጽ፥ የቤት ማገር የሚሆን ተክል፤ ማቴ. 27፥29:30።

**መቃቢስ ዘሞዓብ**፤ ታሪኩ በግእዝ በተጻፈው በ2ኛ መቃብያን የተተረከለት ነው፤ «መቃብያን» ይመ.

**መቃቢስ ዘብንያም**፤ ታሪኩ በግእዝ በተጻፈው በ1ኛ መቃብያን የተተረከለት ነው፤ «መቃብያን» ይመ.

**መቃቢስ ዘእልዓዛር**፤ ታሪኩ በግሪክ በተጻፈው በ2ኛና በ4ኛ መቃብያን የተተረከለት ነው፤ «መቃብያን» ይመ.

**መቃብር**፤ መቅበር። ለመጀመሪያ ጊዜ መቃብር በዋሻ (ዘፍ. 23፥9)፥ በመሬት (ዘፍ. 35፥8)፥ ከዓለት በተወቀረ ድንጋይ (ማቴ. 27፥60) ይሠራ ነበር። አብርሃም በገዛው መሬት እርሱና ብዙ ቤተሰቦቹ ተቀበሩ፤ ዘፍ. 23፤ 49፥31፤ 50፥13። የመቃብር ቦታ በድንጋይ ክምር (ኢያሱ 7፥26)፥

በኖራ በተቀባ ድንጋይ በሌላም ተለይቶ ይታወቅ ነበር፤ ማቴ. 23፥27። በአንዳንድ መቃብር ላይ ምልክት አልነበረም፤ ሉቃ. 11፥44። ሰው ሲሞት ቶሎ ይቀበር ነበር። ባህሉ እንደ አገሩ፥ እንደ ዘመኑ፥ እንደ ቤተሰቡ ይሆናል። በአይሁድ መካከል ዘመዶች ሬሳውን ያጥቡት (ሐ.ሥ. 9፥37)፥ ቅባት ይቀቡት፥ ቅመም ከጨመሩ በኋላም በልብስ ይከፍኑት (ማር. 16፥1፤ ዮሐ. 19፥40)፥ በመግነዝ ይገንዙት፥ ፊቱንም በጨርቅ ይጠመጥሙት እንደነበር እናነባለን፤ ዮሐ. 11፥44። በግብጽ አገር የሀብታሞች ሬሳ እንዳይበሰብስ ባለ መድኃኒቶች ሬሳውን በሽቶ ያሹት በሳጥንም ያኖሩት ነበር፤ ዘፍ. 50፥2:3:26። ሬሳን ማቃጠል በአይሁድ ዘንድ አልተለመደም ነበር። አልፎ አልፎ ግን ሲቸገሩ ሬሳውን ያቃጥሉ ነበር፤ 1ሳሙ. 31፥12:13፤ አሞጽ 6፥10። ሰው በሚገባ ሳይቀበር ቢቀር እንደ አሳዛኝ ሁኔታ ይቈጠር ነበር፤ 1ነገ. 13፥22፤ ኤር. 16፥6። «ልቅሶ» ይመ.



ግብጻውያን ሬሳ ለቀብር ሲገንዙ

**መቃብያን**፤ መቃብያን የሚባሉ 8 መጻሕፍት አሉ፤ በግእዝ የታወቁ 4 ሲሆኑ በግሪክ የታወቁ ደግሞ 4 ናቸው።

ሀ) በግእዝ የታወቁ የመቃብያን መጻሕፍት ፦

1. መቃብያን ቀዳማዊ፥ በሞዓባውያንና በሚዶናውያን መንግሥት ብሎ የሚጀምር፥ ጺሩዳይዳን የተባለው ዐመፀኛ ንጉሥ የመቃቢስ ዘብንያምን ልጆች በእውነተኛ ሃይማኖታቸው ምክንያት እንዴት እንዳሠቃያቸው የሚተርክ መጽሐፍ ነው።

2. መቃብያን ካልእ፥ መቃቢስ የተባለው የሞዓብ ንጉሥ እስራኤላውያንን ከተዋጋ በኋላ ተጸጽቶ የእግዚአብሔርን ሕግ እንዳስተማራቸው፥ እርሱም ከሞተ በኋላ ጺሩዳይዳን የመቃቢስን ልጆች በጽኑ ሃይማኖታቸው ምክንያት እንደገደላቸው የሚተርክ መጽሐፍ ነው።

3. መቃብያን ሣልስ፥ የብ. ኪዳንን ታሪኮች እየጠቀሰ የጽድቅንና የኃጢአት፥ የትንሣኤ ሙታንን ነገር የሚያብራራ መጽሐፍ ነው። እነዚህ ሦስት መጻሕፍት በትልቁ ያማርኛ መ.ቅ. ታትመዋል።

4. መጽሐፈ ዮሴፍ ወልደ ኮርዮን፥ ከአዳም ጀምሮ በ70 ዓ.ም. እስከ ሆነው እስከ ኢየሩሳሌም ቤተ መቅደስ መቃጠል ድረስ የአይሁድን ታሪክ የሚተርክ ዜና አይሁድ ወይም መጽሐፈ ሥርው ተብሎ የሚጠራ፥ በ8 ክፍልም የተከፈለ ረጅም መጽሐፍ ነው። ፍትሐ ነገሥትም ተጨማሪ የመቃብያን መጽሐፍ ይለዋል። እነዚህንም አራት መጻሕፍት የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤ.ክ. ከብ.ኪ. መጻሕፍት ጋር ቈጥራ ትቀበላቸዋለች።

ለ) በግሪክ የታወቁ የመቃብያን መጻሕፍት ፦

1. 1ኛ መቃብያን፥ የሶርያ ንጉሥ አንጥያኮስ 169 ከክ.በ. የኢየሩሳሌምን ቤተ መቅደስ እንዳረከሰውና መቃብያን የሚባሉ የካህኑ ማታትያስ ልጆች በአርበኝነት ተነሥተውበት የአገራቸውን ነጻነት እንዴት እንደመለሱ የሚተርክ መጽሐፍ ነው።

2. 2ኛ መቃብያን፥ የመቃብያንን ታሪክ ጨምሮ የሚተርክ መጽሐፍ ነው።

3. 3ኛ መቃብያን፥ 221-204 ከክ.በ. በነገሠው በግብጽ ንጉሥ በበጥሊሞስ ዘመነ መንግሥት አይሁድ ከጥፋት እንዴት እንደዳኑ የሚተርክ መጽሐፍ ነው። ዛሬም የዓለም አብ.ክ. ከቅዱሳት መጻሕፍት ጋር አይቈጥሩትም።

4. 4ኛ መቃብያን፥ መቃብያን አርበኞች በሰማዕትነት እንዴት እንደሞቱ የሚተርክ መጽሐፍ ነው። ዛሬ የዓለም አብ.ክ. ከቅዱሳት መጻሕፍት ጋር አይቈጥሩትም።

በካቶሊክ ቤ.ክ. እምነት መሠረት ተቀባይነት ያላቸው ሁለቱ የመቃብያን መጻሕፍት ከላይ በተጻፈው ዝርዝር ውስጥ ለ) 1 እና ለ) 2 ላይ የተመለከቱት ናቸው።

**መቃን**፤ የግራና የቀኝ የቤት በር ቋሚ እንጨት። እስራኤላውያን በግብጽ አገር ሳሉ የበኵር ልጅ ሞት እንዳይደርስባቸው በፋሲካ በግ ደም የቤታቸውን መቃን ቀቡ፤ ዘጸ. 12፥7:23።

**መቃጠል፥ ማቃጠል፥ ቃጠሎ**፤ ልዩ ልዩ ነገሮች ለብርሃን፥ ለሙቀት፥ ለአምልኮትና ለፍርድ በእሳት ይቃጠላሉ፤ ዘሌ. 1፥9፤ ኢሳ. 27፥4፤ ማቴ. 3፥12፤ ሐ.ሥ. 28፥2። ሰው የጋለ ስሜት ሲኖረው ልቡ ይቃጠላል፤ ሉቃ. 24፥32፤ ዮሐ. 5፥35፤ 1ቆሮ. 7፥9።

**መቃጥን**፤ ከብረት የሚሠራ የዓሣ መያዣ አጥማጅ ትል ወይም ሥጋ ያኖርበታል፤ ዓሣው ሥጋውን ሲውጥ መቃጥኑ አፉ ውስጥ ይቀረቀራል። አጥማጁ በመቃጥን የታሰረውን ገመድ ስቦ ዓሣውን ያወጣል፤ ሕዝ. 29፥4፤ አሞጽ 4፥2፤ ማቴ. 17፥27።

**መቄዳ**፤ ከኢየሩሳሌም በምሥራቅ በኩል 25 ኪ.ሜ. ርቆ በጌት አጠገብ የሚገኝ ከተማ። ኢያሱ ያዘው፤ ኢያሱ 10፥28። በመቄዳ አጠገብ በነበረው ዋሻ የተሸሸጉትን 5 የከነዓናውያን ነገሥታትን ኢያሱ አጠፋቸው፤ ኢያሱ 10፥15-29።

**መቄዶንያ**፤ በአውሮጳ ክፍለ ዓለም ከግሪክ አገር በስተሰሜን ያለች አገር በ359 ከክ. በ. ፊልጶስ የተባለ ንጉሥ በመቄዶንያ ላይ ነገሠ። ቀጥሎም ልጁ

ታላቁ እስክንድር ነገሥ። በ168 ከክ. ቤ. የሮም ጠቅላይ ግዛት ሆነች። በአውሮጳ ውስጥ ወንጌል በመጀመሪያ በመቄዶንያ ተሰበከ፤ ፊል. 4፥15፤ ሐ.ሥ. 16፥9-12። ጳውሎስ መቄዶንያን ብዙ ጊዜ ጐበኘ። ካ. 6 ሰ። በፊልጵስዩስ፥ በተሰሎንቄ፥ በቤርያም ቤ.ክ.ን አቋቋመ፤ ሐ.ሥ. 16፥16-17፥14፤ 19፥21፤ 20፥1-3፤ 1ቆሮ. 16፥5፤ 2ቆሮ. 1፥16። ሱሲጳጥሮስ፥ አርስጥሮኮስ፥ ሲኮንዱስና አፍሮዲጡ ጳውሎስን የረዱ የመቄዶንያ አማኞች ነበሩ፤ ሐ.ሥ. 20፥4፤ ፊል. 4፥14-19። ዛሬ የግሪክ አገር ሰሜን ክፍል ናት። ስምዋም አልተለወጠም።

**መቅሠፍት፤** እግዚአብሔር በኃጢአት ምክንያት በሰው ላይ የሚያመጣው ችግርና በሽታ፤ ዘፍ. 12፥17፤ ዘኍ. 16፥46፤ 1ነገ. 8፥37-40፤ ራእ. 9፥20፤ 15፥1፤ 22፥18። ግብጻውያን እልከኞች በመሆናቸው እግዚአብሔር በዐሥር መቅሠፍቶች መታቸው። እነርሱም የውሃ ወደ ደም መለወጥ፥ ጓጕንቸር፥ ቅማል፥ የዝንብ መንጋዎች፥ ቸነፈር፥ ሻህኝ የሚያመጣ ቍስል፥ ነጐድጓድና በረዶ፥ አንበጣዎች፥ ጨለማ፥ የበኵር ልጅ ሞት ናቸው፤ ዘጸ. 7-12። «በሽታ» ይመ.

**መቅረዝ፤** የመብራት መስቀያ፤ ማቴ. 5፥15። በብ.ኪ. ከቤተ መቅደስ ዕቃዎች አንዱ ነበር። በእግዚአብሔር ማደሪያ በቅድስቱ በስተግራ በኩል ከወርቅ የተሠራ ሰባት ቅርንጫፍ ያለው መቅረዝ ነበረ፤ ዘጸ. 25፥31-40፤ 40፥24። ካህናት በወይራ ዘይት ከማታ እስከ ማለዳ ድረስ እንዲያበሩ ታዘዙ፤ ዘጸ. 27፥20:21፤ ዘሌ. 24፥2-4፤ 1ሳሙ. 3፥3። ሰሎሞን ለቤተ መቅደስ ዐሥር መቅረዞችን ሠራ፤ 1ነገ. 7፥49። የመቅረዝ ብርሃን የእግዚአብሔርን ሕዝብ አምልኮትና ምስክርነት ያሳስባል፤ ዘካ.4፤ ራእ. 1፥12-20፤ 2፥5፤ 11፥4።



ባለ ሰባት ቅርንጫፍ የቤተ መቅደስ መቅረዝ

**መቅዘፊያ፤** ከእንጨት የሚሠራ መርከብ የሚነዳበትና የሚመራበት መሣሪያ፤ ያዕ. 3፥4። «መርከብ» ይመ.

**መቅደስ፤** ሰዎች ከአምላካቸው ጋር የሚገናኙበት የተቀደሰ ቦታ (ቤት)፤ ዘጸ. 25፥8፤ መዝ. 114፥2፤ አሞጽ 7፥9። «ቤተ መቅደስ» ይመ.

**መቄፈር፤** መማስ፤ መዝ. 7፥14-16 «ጕድጓድን» ይመ.

**መበለት፤** ባልዋ የሞተባት ወይም በማናቸውም ምክንያት ያለ ባል የምትኖር ሴት፤ ዘፍ. 38፥11፤ ማር. 12፥41-44፤ ሉቃ. 7፥12። ቤ.ክ. ለመበለቶች እርዳታ አደረገች፤ ሐ.ሥ. 6፥1-4። አንድ ወንድ፥ ልጅ ሳይኖረው ቢሞት መበለት የሆነች ሚስቱ የባልዋን ወንድም እንድታገባ በሙሴ ሕግ ታዝዟል፤ ዘዳ. 25፥5:6፤ ማቴ. 22፥23-30። ጳውሎስ ባል የሞተባት ሴት እንዳታገባ ይመክራል (1ቆሮ. 7፥39:40)፥ ይህም በዕድሜ ከፍ ያለች እንደሆነ ነው፤ ቆንጆ (ወጣት) ከሆነች እንድታገባ መመሪያ ሰጥቷል፤ 1ጢሞ. 5፥11-16። «ባልቴት» ይመ.

**መባ፤** ሰው ለአምላኩ የሚያቀርበው ሁሉ መባ ይባላል። መባው ለመሥዋዕትም ሆነ ለሌላም ሊሆን ይችላል፤ ዘሌ. 1፥3፤ ዘኍ. 7፥12-17፤ ማቴ. 5፥24፤ ማር. 7፥10-12።

**መባቻ፤** ፀሐይ ልክ ስትገባ ጨረቃ ተወልዳ በከፊል የምትታይበት ቀን መባቻ ተባለ። ይህም የወር መጀመሪያ ቀን ነበረ። ቀኑም የተቀደሰ ነው፤ መዝ. 81፥3፤ ኢሳ. 1፥13፤ ቆላ. 2፥16።

**መብረቅ፤** በዝናብ ጊዜ ከደመናት የሚወጣ እሳት፤ ኤር. 10፥13። ከነጐድጓድ ጋር የተያያዘ ነው፤ ኢዮብ 37፥4። በምሳሌነት ፍጥነትን (ሕዝ. 1፥13:14፤ ሉቃ. 17፥24)፥ የክብር ሞገስን ያሳያል፤ ዳን. 10፥6፤ ማቴ. 28፥3።



መርከብ በባሕር ላይ በመቅዘፊያ አቅጣጫ ሲይዝ

**መተላለፍ፤** ሕግን፥ ትእዛዝን፥ ወግንና ሥርዓትን አለማክበር፥ አብዛኛውን ጊዜ ዐውቆ መበደል፤ ዘኍ. 14፥41፤ ማቴ. 15፥2-3፤ ሮም 4፥15፤ 5፥14፤ ያዕ. 2፥9።

**መተተኛ፤** በርኩስ መንፈስ ኃይል ልዩ ልዩ ድንቅ ነገርን የሚሠራ፤ ዘጸ. 7፥11፤ 22፥18። ኤልዛቤል መተተኛ ነበረች፤ 2ነገ. 9፥22። እስራኤል በመተት እግዚአብሔርን አስቆጣ፤ ኢሳ. 47፥9:12። «ጥንቆላ» ይመ.

**መታዘዝ፤** ትእዛዝን ተቀብሎ መፈጸም። የሚታዘዝ ይባረካል። የማይታዘዝም ይረገማል፤ ዘዳ. 11፥27-28፤ ኢሳ. 1፥19:20፤ መዝ. 1። በልማድ ብቻ መሥዋዕትን ከማቅረብ መታዘዝ ይበልጣል፤ 1ሳሙ. 15፥22። በአ.ኪ. ዋና መታዘዝ ኢየሱስን ማመንና ወንጌልንም መቀበል ነው፤ ሮም 1፥5፤ 6፥16-19፤ 2ተሰ. 1፥8፤ 1ጴጥ. 3፥1። ለኢየሱስ የሚታዘዙ ሁሉ ለዘለዓለም ይድናሉ፤ ዕብ. 5፥9። ኢየሱስ ራሱ ለአብ በመታዘዙ ሰዎችን አዳነ፤ ፊል. 2፥8፤ ዕብ. 5፥8። ምእመናን ለመንግሥት ባለ ሥልጣኖችና ለቤ.ክ. መሪዎች (ቲቶ 3፥1፤ ዕብ. 13፥17)፥ ሚስቶች ለባሎቻቸው (ቲቶ 2፥5፤ 1ጴጥ. 3፥1-6)፥ ልጆች ለወላጆቻቸው (ኤፌ. 6፥1)፥ ሠራተኞች ለአሠሪዎች (ኤፌ. 6፥5)፥ ጐበዞች ለሽማግሌዎች መታዘዝ ይገባል፤ 1ጴጥ. 5፥5። ግን የሚታዘዙለት ሰው የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ቢቃወም ለእግዚአብሔር መታዘዝ ይገባል፤ ሐ.ሥ. 5፥29።

**መታጠቢያ፤** ከናስ የተሠራ የውኃ ማስቀመጫ። በእግዚአብሔር ማደሪያ አደባባይ ይቀመጥ ነበር፤ ካህናት ወደ መገናኛው ድንኳን ከመግባታቸው በፊት እጆቻቸውንና እግሮቻቸውን ይታጠቡበት ነበር፤ ዘጸ. 30፥18-20። ሰሎሞን ዐሥር የናስ መታጠቢያዎች ለቤተ መቅደስ አሠራ፤ 1ነገ. 7፥27-45።

**መታጠብ፤** ማጠብ፥ በእስራኤላውያን ዘንድ እንግዳ ሰው ከውጭ ወደ ቤት ሲገባ እግሩን ይታጠብ ወይም ሌሎች ያጥቡት ነበር፤ ዘፍ. 18፥4፤ 24፥32፤ ዮሐ. 13፥1-10። እንደዚሁም ሰዎች ገላቸውን ይታጠቡ ነበር፤ ዘጸ. 2፥5፤ 2ሳሙ. 11፥2፤ ሩት 3፥3። ብዙ ጊዜ ግን መታጠብ ወይም ማጠብ የሕግን ሥርዓት ስለ መፈጸም፥ የፈሪሳውያንንም ወግና ልማድ ያሳስባል፤ ዘጸ. 30፥19-21፤ ዘሌ. 16፥4፤ ማር. 7፥3:4። በዚህም አንፃር መታጠብ የጥምቀትን ሥራ ይገልጣል፤ ሐ.ሥ. 22፥16።

**መትመም፤** የብዙ ድምፅ ከሩቅ መሰማት፥ የደመና ጕርምርምታ፤ ኢዮብ 37፥2። መትመም የእግዚአብሔር ክብር መገለጫ ነው፤ ሕዝ. 43፥2።

**መኃልየ መኃልይ ዘሰሎሞን፤** ማለት ከሁሉ የሚበልጥ የሰሎሞን መዝሙር ማለት ነው፥ የሁለት ፍቅረኞች ንግግር ነው። የፍቅረኞች ንግግር፥ ግጥምም ነውና አነጋገሩ ከተለመደው አነጋገር የተለየ ነው፤ ትርጕሙም ብዙ ጊዜ ያስቸግራል። በሙሽራው ዓይን ሙሽራይቱ በገጽዋ ነውር ፈጽሞ የሌለባት የውብ መጨረሻ ናት፤ 4፥1-15፤ 6፥4-10። እንደዚሁም ሙሽራይቱ ሙሽራውን ስትመለከት ፈጽሞ ያማረ፥ እኩያ የሌለው፥ ከእልፍ የተመረጠ ሆኖ ታገኘዋለች፤ 5፥9-16። ይህም ሁሉ በፍቅረኞች አነጋገር በመነገሩ አንዳንድ ሰዎች ምሥጢሩን ባለማስተዋል ይነቅፉታል፥ ሆኖም በእርግጥ ቅዱስ ምሳሌ ነው።

«ምን ዓይነት ምሳሌ ነው?» ቢሉ፥ መምህራን በመልሳቸው አልተስማሙም። አይሁድ «እግዚአብሔርና እስራኤል ናቸው» ይሉ ነበር፤ ሕዝ. 16፤ ሆሴዕ 1-3። በዘመናችን «ሰሎሞንና እረኛን የወደደችው ከሱነም አገር (ከሱላሚን) የመጣችው ልጃገረድ ናቸው» የሚሉ አሉ፤ ሌሎች ደግሞ «ሙሽሮቹ ሰሎሞንና ንግሥተ ሳባ ሲሆኑ (1፥5:6) የክርስቶስና የቤ.ክ. ምሳሌዎች ናቸው» ይላሉ። ይህም ማለታቸው ወንድዮው ሴትዮዋን እንደ ወደዳት ክርስቶስ ቤ.ክ.ን ወደደ ይወዳታልም፥ ሴትዮዋም ወንድዮውን እንደ ወደደችው ቤ.ክ. ክርስቶስን መውደድ ይገባታል ይላሉና፤ ኤፌ. 5፥25-33፤ ራእ. 19፥7፤ 21፥2:9። ብዙዎችም ዛሬ በምሳሌው የክርስቶስንና የአማኙን ኅብረት ይረዱበታል።

የዚህ መጽሐፍ አከፋፈል አስቸጋሪ ነው። ሆኖም በውስጡ ሦስት ዐይነት ሰዎች በተራ ይነጋገራሉ። ቈንጆዋ 17 ጊዜ፥ ፍቅረኛዋ የሆነው ወንዱ 11 ጊዜ፥ እንደዚሁም በመካከል የኢየሩሳሌም ቈነጃጅት 4 ጊዜ በመቀባበል ተነጋግረዋል። ይህንም አከፋፈል በ1980 የመ.ቅ. ትርጕም ይመ.። በዚህ መጽሐፍ የእግዚአብሔር ስም አንድ ጊዜ ብቻ ተጠቅሷል፤ 8፥6።

**መኃልይ፤** እንደ ለዘብና ወረብ ዓይነት በፍጥነት የሚዘመር መዝሙር፤ 1ነገ. 4፥32። ከሰሎሞን መጻሕፍት አንዱ መኃልይ ነው።

**መና፤** «ይህ ምንድን ነው?» ማለት ነው፤ ዘጸ. 16፥15። የእስራኤል ሕዝብ አርባ ዓመት በምድረ በዳ የበሉት ምግብ፤ ዘጸ. 16፥35። ጧት ጧት ጠል ካለፈ በኋላ እንደ ደቃቅ ውርጭ ያለ በምድር ላይ ይታይ ነበር። ሰዎች ያን እየለቀሙ በሉ። ለማሳደር በሞከሩ ጊዜ ገማ፤ በስድስተኛው ቀን ግን የተረፈው መና አልገማምና ለሰባተኛው ቀን ምግብ ሆነ። ለተተኪ ትውልድ ምስክር እንዲሆን አሮን ከመናው በጎሞር ውስጥ ከትቶ በቅድስተ ቅዱሳን አኖረው፤ ዘጸ. 16፥13-36፤ ዕብ. 9፥4። ከ40 ዓመት በኋላ እስራኤል በኢያሪኮ ምሥራቅ በጌልገላ ሰፍረው ሳሉ ሌላ ምግብ ስላገኙ መናው ቀረ፤ ኢያሱ 5፥10-12። እግዚአብሔር መናን ሲሰጥ እንዴት ወይም ምን እንደሆነ አይታወቅም። እግዚአብሔር መናን በመስጠቱ ሰው በዚህ ብቻ እንደማይኖር በእግዚአብሔር ቃልም እንደሚኖር (ዘዳ. 8፥3:16)፥ ሰባተኛውንም ቀን እንዲያከብር አስተማረ፤ ዘጸ. 16፥19:20:25-30፤ 20፥8-10። ክርስቶስ የእስራኤልን መና ከጠቀሰ በኋላ የሥጋው ሕይወትነት ከዚያ ይልቅ እጅግ የበለጠ መሆኑን አሳየ፤ ዮሐ. 6፥26-71።

**መናዘዝ፤** ሰው የራሱን ጥፋት ዐውቆ ለእግዚአብሔርና ለሰው መግለጥ መናገር ማለት ነው። ሰው ምሕረትን እንዲቀበል ኃጢአቱን መናዘዝ አለበት፤ ዘሌ. 5፥5፤ ምሳ. 28፥13። እግዚአብሔርን ብቻ የበደለ ለእግዚአብሔር፥ ሰውን ደግሞ የበደለ ለሰውና ለእግዚአብሔር ኃጢአቱን መናዘዝ አለበት፤ ማቴ. 5፥23-25፤ ያዕ. 5፥16፤ መዝ. 5፥4፤ ሉቃ. 15፥18፤ 1ዮሐ. 1፥9። (ሰው የሕዝቡን ኃጢአት መናዘዝ ይገባዋል፤ ዘሌ. 16፥21፤ ነህ. 1፥4-11፤ ዳን. 9፥3-19)

**መናፍስት ጠሪ፤** ርኩሳን መናፍስትንና የሞቱ ሰዎች መናፍስትን በድግምት የሚጠራና የሚጠይቅ፤ ዘዳ. 18፥11፤ 2ነገ. 23፥24። በዓይንዶር የታወቀች መናፍስት ጠሪ ነበረች፤ ሳሙኤልን ከሳኦል ጋር አነጋግራዋለች፤ 1ሳሙ. 28፥7-19፤ 1ዜ.መ. 10፥13:14። «ጥንቆላ» ይመ.

**መናፍቅ፤** በአንድ ሃይማኖት ውስጥ የተለየ ትምህርትን ተከታትሎ በመጠራጠር መለያየትን የሚፈጥርና የሚወግን፤ 2ጴጥ. 2፥1፤ ቲቶ 3፥10፤ 1ቆሮ. 11፥19። ይህም የሥጋ ሥራ ነው፤ ገላ. 5፥20። አይሁድ ክርስቲያኖችን እንደ መናፍቃን ይቈጥሩ ነበር፤ ሐ.ሥ. 24፥5።

**መንሽ፤** ሁለት ወይም ከሁለት በላይ ጣት ያለው የእህል ማበጠሪያ፤ ኢሳ. 30፥24። የእግዚአብሔር ሥልጣን ምሳሌ ነው፤ ማቴ. 3፥12።



ገበሬ በመንሽ እህል ከገለባ ሲለይ

**መንቀል፤** ከሸክላ የሚሠራ አንገታም የውኃ መያዣ ዕቃ። በብ.ኪ. በቤተ መቅደስ መገልገያ ዕቃ ነበር፤ ኤር. 52፥19።

**መንኰራኵር፤** የሠረገላ ተሽከርካሪ እግር፤ ዘጸ. 14፥25። የጥንት የእስራኤል ሰዎች በእንስሳት በሚሳብ መንኰራኵር እህላቸውን ያሄዱ ወይም ይወቁ ነበር፤ ኢሳ. 28፥27-28። ሸክላ ሠሪዎችም ገሉንና አፈሩን በመንኰራኵር እየፈጩ የሸክላ ዕቃ ይሠሩ እንደነበር ተጠቅሷል፤ ኤር. 18፥3። ሕዝቅኤል አራት እንስሳትን በመንኰራኵር ላይ አየ፤ ይህም ከምርኮ የሚመለሱበትን ጊዜ መፋጠን ያመለክት ነበር፤ ሕዝ. 1፥15-21።

**መንገድ፤** መሄጃ፥ መጓዣ። ሰው ወደ አንድ ቦታ ለመድረስ ሲፈልግ በትክክለኛው መንገድ መሄድ እንዳለበት ሁሉ፥ የእግዚአብሔርንም በረከት እንዲያገኝ በእግዚአብሔር መንገድ መሄድ ማለት እንደ እግዚአብሔር ትእዛዝ መኖር አለበት፤ ዘጸ. 32፥8፤ ዘዳ. 5፥33። የእግዚአብሔርና የሰው መንገድ የተለያየ ነው፤ ኢሳ. 55፥9፤ ሆሴዕ 14፥9። ሰው በሁለት መንገዶች ሊሄድ ይችላል፤ መድረሻው እንደ መንገዱ ይሆናል፤ መዝ. 1፥1:6፤ ማቴ. 7፥13:14። ትክክለኛው መንገድ ክርስቶስ ነው፤ ዮሐ. 14፥6። ቤ.ክ. መንገድ ትባላለች፤ ሐ.ሥ. 9፥2፤ 19፥9:23፤ 22፥4።

**መንጋ፤** ከብቶች በጎችና ፍየሎች በአንድነት፤ ከአብርሃም ጊዜ ጀምሮ የእስራኤል ሕዝብ የከብት መንጋ ይጠብቁ ነበር፤ ዘፍ. 13፥5፤ ኢዮብ 1፥3። የክርስቶስ ተከታዮች በመንጋ ተመስለዋል፤ ሉቃ. 12፥32፤ ሐ.ሥ. 20፥28፤ 1ጴጥ. 5፥2።

**መንጋጋ፤** የማኘኪያ ጥርስና ተሸካሚው አጥንት፤ አዲስ የአህያ መንጋጋ ደረቅ ባለመሆኑ ክብደት ያለውና ቶሎ የማይሰበር ይሆናል፤ መሳ. 15፥15-17።

**መንግሥተ ሰማያት፤** በወንጌላት የእግዚአብሔር መንግሥትና መንግሥተ ሰማያት አንድ ናቸው፤ ማቴ. 5፥3፤ ሉቃ. 6፥20። ክርስቶስ ስለ መንግሥተ ሰማያት አስተማረ፤ ወደ ምድር ስለ መምጣቱም ብዙ ምሳሌዎችን ተናገረ። እግዚአብሔር ከሰው በላይ ነውና መንግሥተ ሰማያት የእግዚአብሔር መንግሥት ነው። በቃሉ ግንዛቤ ላይ ልዩ ልዩ አስተሳሰብ አለ።

1. መንግሥተ ሰማያት ራሱ እግዚአብሔር ነው። ምክንያቱም እግዚአብሔር መንፈስ ነውና እርሱ ሁሉ በሁሉ ይሆናል፤ ሉቃ. 17፥20:21፤ ሐ.ሥ. 17፥27:28፤ 1ቆሮ. 15፥28።

2. መንግሥተ ሰማያት ፦ ክርስቶስ ያለበት ስፍራ ነው፤ ሉቃ. 23፥43፤ ዮሐ. 14፥2:3።

3. መንግሥተ ሰማያት ይህ ዓለም ካለፈ በኋላ በአዲስ ተፈጥሮ አዲስ ዓለም ሆኖ ይታያል፤ ሮም 8፥19-22፤ 2ጴጥ. 3፥10-13፤ ራእ. 21፥1-3። እነዚህን ሦስት አሳቦች ለማዛመድ ያስቸግር ይሆናል። ሆኖም ትንቢት ነውና ፍጻሜው ሲደርስ ብቻ ለሁሉም ግልጥ ይሆናል። «ሰማይ»፥ «የእግዚአብሔር መንግሥት» ይመ.

**መንግሥት፤** ንጉሥ የሚነግሥበት፥ ሉዓላዊ ሥልጣን ያለበት ሕዝብና አገር። በመ.ቅ. ታሪክ ዋና ዋና የዓለም መንግሥታት ግብጽ፥ ሶርያ፥ አሦር፥ ባቢሎን፥ ፋርስ፥ ሜዶን፥ ግሪክና ሮም ናቸው። በብ.ኪ. ዘመን የአብርሃም ዘር እስራኤል፥ ይሁዳና አይሁድ ተብላ የእግዚአብሔር መንግሥት ሆነች፤ ዘጸ.

19፥6፤ ማቴ. 2፥1-2። በአ.ክ. ዘመን ቤ.ክ. የእግዚአብሔር መንግሥት ሆናለች፤ ቆላ. 1፥13-14፤ 1ጴጥ. 2፥9-10። መንግሥታት በየአርእስታቸው፥ «የእግዚአብሔር መንግሥት»፥ «መንግሥተ ሰማያት»፥ «አቡነ ዘበሰማያት» ይመ.

**መንፈስ፥ መናፍስት፤** ረቂቅ የማይጨበጥና የማይዳሰስ የማይታይም።

1. እግዚአብሔር መንፈስ ነው፤ ዮሐ. 4፥24። ከሦስቱ አካላት አንዱ መንፈስ ቅዱስ ነው፤ ማቴ. 28፥19።

2. መላእክት መናፍስት ናቸው፤ ዕብ. 1፥7።

3. ሰይጣንና ተከታዮቹ፥ አጋንንትም ርኩሳን መናፍስት ይባላሉ፤ ማቴ. 8፥16:17፤ 12፥28፤ 25፥41፤ ሉቃ. 4፥36፤ ይሁዳ 6።

4. ሰው መንፈስ አለው። ይህ መንፈስ ደግሞ ነፍስ ይባላል። ሰው ሥጋና መንፈስ ነው፤ ማቴ. 10፥28፤ 1ቆሮ. 5፥5። «ነፍስ» ይመ.

5. በእግዚአብሔር ዘንድ የተሰበረ መንፈስ የተወደደ ነው፤ መዝ. 51፥17፤ ማቴ. 5፥3።

6. ብዙ ዓይነት መናፍስት ስላሉ መምህር ወይም ነቢይ በምን ዓይነት መንፈስ እንደሚናገር መለየት ያስፈልጋል፤ 1ዮሐ. 4፥1። ሰዎች በአካሄዳቸውና በትምህርታቸው ይታወቃሉ፤ ማቴ. 7፥15-20፤ 1ዮሐ. 4፥2-3። «ነቢይ» ይመ.። መናፍስትን መለየት ከመንፈስ ቅዱስ ስጦታዎች አንዱ ነው፤ 1ቆሮ. 12፥10።

**መንፈስ ቅዱስ፤** ይህ ስም ከዘለዓለም ከአብና ከወልድ ጋር ለሚኖረው ለእግዚአብሔር መንፈስ ቅዱስ የአካል የህላዌ (የመኖር) ስሙ ነው። መንፈስ ቅዱስ ከአብ የሠረጸ (የወጣ) ነው፤ በክርስቶስም ሥራ መሠረት ለምእመናን ይሰጣል። መንፈስ ቅዱስ ከአብና ከወልድ አያንስም፤ በህላዌ፥ በመለኮት፥ በክብር፥ በሥልጣን እኩል ነው፤ ማቴ. 28፥19፤ ዮሐ. 14፥16:17፤ 15፥26፤ ሐ.ሥ. 2፥33። የመ.ቅ.ን ትምህርት ስለ መንፈስ ቅዱስ በሚከተሉት ዐሥር አርእስት ለማጠቃለል ይቻላል።



1. የመንፈስ ቅዱስ ስሞችና ምሳሌዎች፤ መንፈስ ቅዱስ፥ መንፈስ (ዮሐ. 1፥32)፥ የእግዚአብሔር መንፈስ (ሮም 8፥14)፥ የጌታ የክርስቶስ መንፈስ (ሮም 8፥9፤ 2ቆሮ. 3፥17)፥ የእውነት መንፈስ (ዮሐ. 15፥26)፥ አጽናኝ (ዮሐ. 14፥26) ተብሎ ይጠራል። መንፈስ ቅዱስ በርግብ (ማቴ. 3፥16)፥ በእሳት (ማቴ. 3፥11:12፤ ሐ.ሥ. 2፥3)፥ በነፋስ (ዮሐ. 3፥8)፥ በእግዚአብሔር ጣት (ማቴ. 12፥28 እና ሉቃ. 11፥20 ያነጻጽሩ)፥ በእስትንፋስ (ኢዮብ 4፥9) ተመስሏል። መንፈስ ቅዱስ አምላክ ነውና በሁሉ ዘንድ ይገኛል (መዝ. 139፥7)፤ ቅዱስ ነውና ሁሉን ይቀድሳል፤ 1ጴጥ. 1፥1:2።

2. የመንፈስ ቅዱስ አካላዊነት (እኔ ባይነት)፤ አንዳንድ ሰዎች መንፈስ ቅዱስ አካላዊ መንፈስ ሳይሆን እንደ እሳት ሙቀት ያለ የእግዚአብሔር ኃይል ነው ይላሉ፤ መ.ቅ. ግን እንደዚህ አያስተምርም። መንፈስ ቅዱስ እግዚአብሔር ስለሆነ መንፈስ ነው፤ ሥጋና አጥንት የለውም፤ ዮሐ. 4፥24። ሆኖም መንፈስ ቅዱስ እንደ አብና እንደ ወልድ አስቦ የሚሠራ አካላዊነት ስላለው ነው። በልዩ ልዩ ነገሮች ይታያል።

(ሀ) መንፈስ ቅዱስ ከአብና ከወልድ ጋር ይጠቀሳል፤ ሆኖም በእነዚህ ጥቅሶች ከእነርሱ በአካል የተለየ መሆኑን እንረዳለን፤ ኢሳ. 48፥16፤ 61፥1፤ ማቴ. 3፥16:17፤ 28፥19፤ 2ቆሮ. 13፥14፤ 1ጴጥ. 1፥1:2።

(ለ) «ሌላ አጽናኝ» ይባላል። ኢየሱስ በምድር ሳለ የሐዋርያት አጽናኝ ነበርና መንፈስ ቅዱስም እንደ እርሱ አካላዊ መሆኑ ይታያል፤ ዮሐ. 14፥16። ክርስቶስ ከአብ እንደ ተላከ መንፈስ ቅዱስም ደግሞ ተልኳል፤ ዮሐ. 14፥26፤ 15፥26።

(ሐ) መንፈስ ቅዱስ አሳብን ይገልጣል (ዮሐ. 16፥13-15፤ ሮም 8፥16)፥ ይፈቅዳል (ሐ.ሥ. 15፥28:29፤ 16፥7፤ 1ቆሮ. 12፥11)፥ ይናገራል (ሐ.ሥ. 8፥29፤ 13፥2)፥ ይወቅሳል (ዮሐ. 16፥8)፥ የእግዚአብሔርን ጥልቅ ነገር ይመረምራል (1ቆሮ. 2፥10:11)፥ ስሜት ይሰማዋል፤ ኢሳ. 63፥10፤ ኤፌ. 4፥30። እነዚህ ሁሉ የሕያው አካል ሥራዎች ናቸው።

(መ) መንፈስ ቅዱስ ራሱ ኃይል አለው፤ ሉቃ. 1፥35፤ 4፥14፤ ሐ.ሥ. 10፥38፤ ሮም 15፥13። መንፈስ ቅዱስ እኔ ባይነት የሌለው የእግዚአብሔር ኃይል ቢሆን ኖሮ እነዚህ ጥቅሶች ትርጉም አይኖራቸውም ነበር።

3. የመንፈስ ቅዱስ አምላክነት፤ ይህም በሚከተሉት አራት ነገሮች ይታያል።

(ሀ) ከአብና ከወልድ ጋር በእኩልነት ተጠቅሷል፤ ማቴ. 28፥19፤ 2ቆሮ. 13፥14።

(ለ) በአንድ ቦታ ስለ እግዚአብሔር የተነገረው በሌላ በኩል ስለ መንፈስ ቅዱስ ይጠቀሳል፤ ዘጸ. 17፥7 እና ዕብ. 3፥7፤ ኢሳ. 6፥8-10 እና ሐ.ሥ. 28፥25-28፤ 5፥3 እና 4።

(ሐ) መንፈስ ቅዱስ በሁሉ ዘንድ ይገኛል፤ መዝ. 139፥7-10። ሁሉንም ያውቃል፤ ኢሳ. 40፥13:14፤ 1ቆሮ. 2፥10:11።

(መ) የአምላክነትን ሥራ ይሠራል፥ ይፈጥራል (ዘፍ. 1፥2:3፤ ኢዮብ 26፥13)፥ ሙታንን ያስነሣል፤ ሮም 8፥11።

4. መንፈስ ቅዱስ በብሉይ ኪዳን፤ በብ.ኪ. የመንፈስ ቅዱስ ሥራ በሚከተሉት ነገሮች ይታያል።

(ሀ) ዓለም ሲፈጠር መንፈስ ቅዱስ ምድርን ያደራጅ ነበር (ዘፍ. 1፥2:3)፥ ለሰማያት ውበትን ሰጠ (ኢዮብ 26፥13)፥ ከዚያ ወዲህም ምድርን ያድሳል፤ መዝ. 104፥30።

(ለ) በእስራኤል መሪዎች፤ መንፈስ ቅዱስ ለእነሙሴ ትንቢትን (ዘኍ. 11፥26-29)፥ ለእነባስልኤል የእጅ ሥራ ጥበብን (ዘጸ. 31፥1-5)፥ ለሰባው ሽማግሌዎች የአስተዳደር ሥልጣንን (ዘኍ. 11፥24-25)፥ ለእነገዴዎን የመሪነት ችሎታን (መሳ. 6፥34)፥ ለእነሶምሶን ኃይልን (መሳ. 14፥6) ሰጠ።

(ሐ) በምእመናን ልብ፥ መንፈስ ቅዱስ ሰውን ይቀድሳል፥ ልቡንም ይለውጣል፤ መዝ. 51፥10፤ ሕዝ. 36፥26:27። ይህም ሥራ በአ.ኪ. አዲስ ፍጥረት መሆንና ዳግም ልደት ይባላል፤ አብርሃምና ዳዊት እውነተኞች አማኞች ነበሩና ይህ መለወጥ ተሰጣቸው፤ ሮም 4፥3:6-8።

5. መንፈስ ቅዱስና ክርስቶስ፤ መንፈስ ቅዱስና ወልድ በየአካላቸው ከዘለዓለም በአንድነት ነበሩ። መንፈስ ቅዱስ ፦

(ሀ) ቅድስት ድንግል ማርያም ክርስቶስን የወለደችው በመንፈስ ቅዱስ ፀንሳ ነው፤ ማቴ. 1፥20፤ ሉቃ. 1፥35።

(ለ) ኢየሱስ ሲጠመቅ በራሱ ላይ ዐረፈ፤ ሉቃ. 3፥22።

(ሐ) ኢየሱስ በመንፈስ ቅዱስ ተሞልቶ በኃይሉ ተአምራትን አደረገ፤ አገልግሎቱንም ፈጸመ፤ ማቴ. 12፥28፤ ሉቃ. 4፥1:14:17-19፤ ዮሐ. 3፥34፤ ሐ.ሥ. 10፥38፤ ዕብ. 9፥14።

(መ) አሁንም መንፈስ ቅዱስ ስለ ክርስቶስ ይመሰክራል፤ ዮሐ. 15፥26፤ 16፥14።

6. የመንፈስ ቅዱስ መውረድ፤ ሐዋርያት በሥልጣን የወንጌልን ሥራ እንዲሠሩ ኢየሱስ «መንፈስ ቅዱስን ተቀበሉ» ብሎ እፍ አለባቸው፤ ዮሐ. 20፥22። ከዚህም በላይ በአዲስ ዓይነት በበዓለ ኀምሳ ዕለት መንፈስ ቅዱስ ወረደላቸው፤ ሐ.ሥ. 2፥1-4። መውረዱ ለሦስት ምክንያት ነው።

(ሀ) በተስፋው መሠረት፥ መንፈስ ቅዱስ እንደሚወርድ አስቀድሞ በነቢያትና በክርስቶስ ተነገረ። በፊት መንፈስ ቅዱስ በአንዳንድ መሪዎች ላይ በኃይል ይወርድ ነበር፤ አሁን ግን ምእመናን ሁሉ መንፈስ ቅዱስን ይቀበላሉ፥ ልዩ ልዩ ስጦታም ይሰጣቸዋል፤ ኢዩ. 2፥28:29፤ ዮሐ. 15፥26፤ ሐ.ሥ. 2፥33።

(ለ) በስጦታ፥ የመንፈስ ቅዱስ መውረድ በእግዚአብሔር ጸጋ ነው፤ ሐ.ሥ. 2፥38።

(ሐ) ለጥምቀት፥ መንፈስ ቅዱስ የወረደላቸው ወደ አዲስ ሁኔታ እንዲገቡ ነው፤ ሐ.ሥ. 1፥5።

መንፈስ ቅዱስ እንደዚህ በመውረዱ ክርስቶስ በክብር ያለ መሆኑን አረጋገጠላቸው (ዮሐ. 7፥39፤ ሐ.ሥ. 2፥33)፥ በክርስቶስ አንድ ማኅበር፥ አንድ አካል፥ አንዲት ቤ.ክ. አደረጋቸው (ኤፌ. 1፥21-23፤ 2፥20-22)፤ ኃይልንም ለምስክርነት ሰጣቸው፤ ሉቃ. 24፥49፤ ሐ.ሥ. 1፥8። በኋላም መንፈስ ቅዱስ በሰማርያ ሰዎች (ሐ.ሥ. 8፥14-18)፥ በአሕዛብ (ሐ.ሥ. 10፥44-48፤ 11፥15-17)፥ በኤፌሶን ሰዎች (ሐ.ሥ. 19፥1-7) ወረደ። እንደዚሁም ማንም ሰው ሲያምን መንፈስ ቅዱስን ይቀበላል፥ በመንፈስ ቅዱስ ጥምቀት የክርስቶስ አባል ይሆናል፤ ሐ.ሥ. 2፥38:39፤ 9:17፤ 1ቆሮ. 12፥13። መንፈስ ቅዱስ በብ.ኪ. ይሠራ ስለነበር በበዓለ ኃምሳ ቀን የመውረዱ አዲስነት በ3 መንገድ ይታያል ፦ ሀ) ክርስቶስ ለኃጢአት አንድ ጊዜ ለዘላለም በቂ መሥዋዕት በማቅረቡ ሥራውን ጨርሷልና በአብ ቀኝ በመቀመጡ ስለ ክብሩ መስክሯል፤ ዮሐ. 7፥39፤ ሐ.ሥ. 2፥33፤ ዕብ. 10፥12። ለ) በብ.ኪ. የክርስቶስ ጥላ በነበረው በሙሴ ሥርዓት አማካይነት ለእስራኤል ሕዝብ መጣ፥ በአ.ኪ. ግን ፍጻሜ በሆነው በአዲሱ ሥርዓት አማካይነት በቤ.ክ. ላይ መጣ፤ ኤፌ. 2፥20-22። ሐ) በብ.ኪ. የመጣው ለአገልግሎት ወደ ተጠሩ ሰዎች ብቻ ነበር፤ በአ.ኪ. ግን ለሁሉ ይመጣል፤ ዘኍ. 11፥24-29፤ ሐ.ሥ. 2፥38፤ 1ጴጥ. 4፥10።

7. መንፈስ ቅዱስና ምእመናን፤ መጀመሪያ መንፈስ ቅዱስ ሰው ንስሐ እንዲገባና በክርስቶስ እንዲያምን ልብን ይለውጣል፤ ከዚያም በኋላ ያድርበታል፤ ሮም 8፥9፤ 1ቆሮ. 6፥19:20፤ ቲቶ 3፥5-7። «መመለስ»፥ «ዳግም ልደት» ይባል። መንፈስ ቅዱስ በሰው ልብ ሆኖ ያ ሰው የእግዚአብሔር ልጅ እንደሆነ ይመሰክርለታል፤ መንግሥቱንም እንዲወርስ ያረጋግጥለታል፤ ሮም 8፥16፤ 2ቆሮ. 1፥22፤ ገላ. 4፥6፤ ኤፌ. 1፥13።

መንፈስ ቅዱስ አማኙን ሥጋውን እንዲያሸንፍ ያስችለዋል፤ በሕይወቱም ሁሉ ይመራዋል (ሮም 8፥13:14)፥ እንዲጸልይ ያግዘዋል (ሮም 8፥26፤ ኤፌ. 6፥18)፥ ስለዚህ የመንፈስ ፍሬ በሕይወቱ መታየት ይጀምራል፤ ገላ. 5፥22:23። ምእመናን እንዲያገለግሉ በመንፈስ ቅዱስ ይቀባሉ፤ 2ቆሮ. 1፥21። ምእመናን መንፈስ ቅዱስን እንዳያሳዝኑ ሁልጊዜ በእርሱ እንዲሞሉ ታዝዘዋል፤ ኤፌ. 4፥30፤ 5፥18። ይህ መሞላት ለሁልጊዜ (ሐ.ሥ. 6፥3:5) ወይም ለተወሰነ ጊዜ ለልዩ አገልግሎት የሚቀበሉትን ኃይል ሊያመለክት ይችላል፤ ሐ.ሥ. 4፥31፤ 13፥9።

8. መንፈስ ቅዱስና ማኅበረ ምእመናን (ቤተ ክርስቲያን)፤ መንፈስ ቅዱስ ምእመናን በኅብረት እንዲኖሩ ፍቅርን ይሰጣቸዋል፤ ፊል. 2፥1። ቤ.ክ. አገልግሎትዋን እንድትፈጽም ኃይልን ይሰጣታል፤ ሐ.ሥ. 1፥8። ሰዎችን ለወንጌል ሥራ ይልካል፤ ሲሄዱም ይመራቸዋል (ሐ.ሥ. 13፥2፤ 16፥6-10)፥ ስብከታቸውን ይባርካል፤ 1ተሰ. 1፥5። ለቤ.ክ. ስጦታዎችን እንደ ፈቃዱ ያካፍላል፤ ሮም 12፥1-8፤ 1ቆሮ. 12፥1-31፤ ዕብ. 2፥4።

9. መንፈስ ቅዱስና ዓለም፤ መንፈስ ቅዱስ በዚህ

ዓለም ሰዎችን ኃጢአት ከመሥራት ይገታቸዋል (ዘፍ. 6፥3)፥ ስለ ኃጢአትም ይወቅሳል (ዮሐ. 16፥8-11)፥ ነገር ግን ሰው የእግዚአብሔርን ነገር ከመንፈስ ቅዱስ ከተረዳና ካወቀ በኋላ ቢተወውና ቢንቅረው የመመለስ ተስፋ አይኖረውም፤ ማቴ. 12፥31:32፤ ዕብ. 6፥4-6።

10. መንፈስ ቅዱስና መጽሐፍ ቅዱስ፤ መንፈስ ቅዱስ የእውነት መንፈስ ነውና ሁሉን ወደ እውነት ይመራል። ነቢያት በመንፈስ ቅዱስ ተናገሩ፤ 2ጴጥ. 1፥21። ክርስቶስ ራሱ የተናገረውን ሐዋርያት እንዲገነዘቡ፥ የሚመጣውንም እንዲያውቁ መንፈስ ቅዱስ እንደሚነግራቸው ተስፋ ሰጠ፤ ዮሐ. 14፥26፤ 16፥13። መንፈስ ቅዱስ አሳባቸውን ብቻ ሳይሆን ቃላቸውንም መራ፤ 1ቆሮ. 2፥12:13። ስለዚህ የእግዚአብሔር መንፈስ ያለበት መጽሐፍ ሁሉ ለጠቅላላው የሰው ኑሮ ይጠቅማል፤ 2ጢሞ. 3፥16:17። «መጽሐፍ ቅዱስ» ይመ.

**መና**፤ ቀለብ። በእስራኤል ዘንድ የሰባተኛው ዓመት ሰብል ለእንስሳትና ለአራዊት መና እንዲሆን ታዘዘ፤ ዘሌ. 25፥7።

**መከራ**፤ ማንም ሰው ክርስቶስን ሲከተል መከራ ይደርስበታል፤ ዮሐ. 16፥33፤ ሐ.ሥ. 14፥21:22፤ 1ተሰ. 1፥6። መከራ ብዙ ጊዜ በዓለም ሰዎች ይነሣል፤ 1ተሰ. 2፥2። ሰይጣን በሰዎች ላይ መከራን ያመጣል፤ ግን በእግዚአብሔር ተወስኗል፤ ኢዮብ 1፥12፤ 2፥6፤ 2ቆሮ. 12፥7። አንዳንዱም መከራ በእግዚአብሔር ፈቃድ ሊመጣ ይችላል፤ መዝ. 39፥10፤ አሞጽ 3፥6፤ ሐ.ሥ. 2፥23። እግዚአብሔር ፍቅር ከሆነ እንዴት መከራ እንዲመጣ ይፈቅዳል የሚል ጥያቄ ይነሣ ይሆናል፤ መዝ. 73። በመ.ቅ. ውስጥ ሙሉ መልስ ባይሰጥም መከራ በዓለም ላይ በኃጢአት ምክንያት መጥቷል፤ ዘፍ. 3፥14-24። የሃይማኖት ጽንአት እንዲፈተንም መከራ ሊደርስ ይችላል (መጽሐፈ ኢዮብ ይመ.)፤ አማኝ ግን ሊታገሥ ይገባዋል፤ ዕን. 2፥2-4። ሦስቱ ወጣቶች መከራ በደረሰባቸው ጊዜ እግዚአብሔር አብሮአቸው እንደነበረ ሁሉ ዛሬም ከልጆቹ ጋር ነው፤ ዳን. 3፥25፤ ሮም 8፥31-39፤ ኢሳ. 43፥2። አማኝ ከሚመጣው ደስታ የተነሣ በመከራው ይጸናል፤ መዝ. 73፥21-26፤ ሮም 8፥18፤ 2ቆሮ. 4፥16።

መከራ ያለበት የሚከተሉትን ነገሮች ይገንዘብ ፦

1. መከራ የኃጢአት ውጤት ሊሆን ይችላል፤ ገላ. 6፥8።

2. ሰዎች ከክፋታቸው እንዲመለሱ የእግዚአብሔር ቅጣት ይሆን ይሆናል፤ ምሳ. 3፥12።

3. መከራ ሰዎች የሚፈተኑበት የሚጸኑበትም ነው፤ ሮም 5፥3፤ 1ጴጥ. 1፥7።

4. መከራ ሰዎች በይበልጥ እግዚአብሔርን እንዲያውቁ ያደርጋል፤ መዝ. 119፥67፤ ሮም 8፥35-37።

5. መከራ ግብዞችን ከእግዚአብሔር ያርቃቸዋል (ማቴ. 13፥21)፥ ለእውነተኞች ይጠቅማል፤ ሮም 8፥28።

6. ክርስቶስ እንዲያድነን መከራን ተቀበለ፤ ኢሳ. 53፥5፤ 1ጴጥ. 2፥24።

7. ምእመናን የክርስቶስ መከራ ተካፋዮች እንዲሆኑ ተጠርተዋል (ማር. 10፥39፤ ሮም 8፥17፤ ፊል. 1፥29)፥ መከራ ወደ ክብር ይመራል፤ ማቴ. 16፥24፤ ዮሐ. 12፥24-26፤ ዕብ. 12፥1:2።

8. ምእመናን መከራን በደስታ ሊቀበሉ ይገባቸዋል፤ ሐ.ሥ. 5፥41፤ 1ጴጥ. 4፥12-16። «ሥቃይ»፥ «ፈተና» ይመ.

9. ታላቁ መከራ፤ በራእ. 7፥14 ላይ «እነዚህ ከታላቁ መከራ የመጡ ናቸው» በማለት የክርስቶስ ተከታዮች ሁሉ ስለ ስሙ የሚቀበሉትን መከራ ታላቅ መከራ ይለዋል። ይህንኑ መከራ ጳውሎስ በሐ.ሥ. 14፥22 ላይ ብዙ መከራ ሲለው፥ ጌታ ራሱ ደግሞ በዮሐ. 16፥33 ላይ መከራ ይለዋል። ምእመናን በዓለም ሳሉ መከራ አለባቸው፤ 1ተሰ. 3፥3-4፤ 2ተሰ. 1፥6-7። የምእመናን የስደት መከራ የክርስቶስን መከራ መካፈል ነው፤ 2ቆሮ. 1፥5፤ 4፥10-11፤ ቆላ. 1፥24። ጌታ ሊገለጥ ሲል ይህ የስደት መከራ ይጠነክራል፤ ነገር ግን ጌታ የራሱን ሕዝብ በፍጥነት ይታደጋቸዋል፤ ማቴ. 24፥21:29-30፤ ዳን. 12፥1፤ ራእ. 20፥7-10። በ70 ዓ.ም. በኢየሩሳሌም የደረሰው መከራና በዓለም መጨረሻ የሚሆነው መከራ ይመሳሰላሉ፤ ሉቃ. 21፥20-28። «ተቃዋሚ» ይመ.

**መከር**፤ በእስራኤል አገር የገብስ አጨዳ ይቀድማል። ይህም በሚያዝያ ወር ይከናወናል፤ በግንቦት የስንዴ መከር ይቀጥላል፤ ሩት 1፥22፤ 2፥23። የስንዴ አጨዳ ሲጀመር የመከር በዓል ወይም ሰባቱ ሱባዔ ይከበራል። በዓሉ የደስታ ጊዜ ነው፤ የእስራኤልም ወንዶች ሁሉ ስለ መከሩ እግዚአብሔርን ለማመስገን በዓሉን ያከብሩት ነበር፤ ዘጸ. 34፥22፤ ዘዳ. 16፥9-12። «በዓላት» ይመ.። በአ.ኪ. መከር የዓለም ፍጻሜና የአማኞች መሰብሰብ ምሳሌ ነው፤ ማቴ. 13፥39፤ ሉቃ. 10፥2፤ ራእ. 14፥15:16።

**መከተል**፤ በእግር፥ በአርአያነት ፊት ለፊት የሚሄደውን አይቶ መራመድ፥ የሌላውን አሳብ መቀበል፤ ዘጸ. 23፥2፤ ማቴ. 4፥20:22፤ 8፥1፤ 9፥9፤ 16፥24።

**መከዳ**፤ እንደ ትራስ ያለ መደገፊያ፥ መጠጊያ። በለስላሳ ቁርበት ወይም በጨርቅ ይለበጣል፤ በውስጡም ጥጥ ወይም ሌላ ነገር ይሞላል። ሐሰተኞች ነቢያት በመከዳዎች እየጠነቆሉ ሰዎችን ያጠምዱ ነበር፤ ሕዝ. 13፥18:20።

**መካከለኛ**፤ በሁለት ወገኖች መካከል ለማስታረቅ የሚቆም። በመ.ቅ. መካከለኛነት በእግዚአብሔር ፊት ለበደለኞች የሚያማልድና ከእግዚአብሔር ምሕረትን የሚያስገኝ ነው፤ ኢዮብ 9፥33፤ 1ሳሙ. 2፥25። በብ.ኪ. ካህናትና ነቢያት በእግዚአብሔርና በሕዝቡ መካከል የመካከለኛነት ሥራ ይሠሩ ነበር፤ ዘሌ. 9፥7፤ ዘዳ. 18፥18-22፤ 28፥1፤ ዕብ. 5፥1-4። ሙሴ የብ.ኪ. መሥራች

ስለነበር የብ.ኪ. መካከለኛ ሆነ፤ ዘጸ. 19፥3-8፤ ሐ.ሥ. 7፥37-39፤ ዕብ. 9፥19-20። ሙሴ በመካከለኛነቱ ከኢየሱስ ክርስቶስ ጋር ተነጻጽሯል፤ ኢየሱስ ክርስቶስ የአ.ኪ. መካከለኛ ነው፤ ዮሐ. 1፥17፤ ዕብ. 7፥27-28፤ 8፥6፤ 9፥15:23-24፤ 10፥1፤ 12፥24። ኢየሱስ ክርስቶስ የካህናትን፥ የነቢያትንና የሙሴን መካከለኛነት በመፈጸሙ በእግዚአብሔርና በሰው መካከል ያለ መካከለኛ እርሱ ብቻ ነው፤ 1ጢሞ. 2፥5።

**መክሊት**፤ የጥንት የክብደት መለኪያ፤ 2ነገ. 18፥14። በኋላም መክሊት ገንዘብንም ያመለክት ነበር፤ ማቴ. 25፥15። «ክብደት»፥ «ገንዘብ» ይመ.

**መክብብ**፤ «መክብብ» ማለት «ሰባኪ» ወይም «አስተማሪ» ማለት ነው። በዚህም መጽሐፍ የሚሰብክ የሚያስተምር ሰሎሞን ነው። «በኢየሩሳሌም የነገሠ የዳዊት ልጅ» ተባለ (1፥1:12)፥ ጥበቡም በአያሌው ተጠቅሷል (1፥16፤ 2፥9)፥ ምሳሌዎችንም መሰብሰቡ ታውቋል፤ 12፥9፤ 1ነገ. 4፥32። «የዕብራይስጡ አጻጻፍ የኋላ ዘመን ነው እንጂ የሰሎሞን ዘመን አይደለምና ደራሲው ሌላ ነው» የሚሉ ቢኖሩም፥ ሌላ ሰው ይጻፈው እንጂ ትምህርቱ ያለ ጥርጥር የሰሎሞን ነው።

ሰሎሞን በዚህ መጽሐፍ ላይ «እግዚአብሔር የሌለበት ሕይወት ከንቱ ነው፥ አያጠግብም» ይላል። ንጉሥ ነውና ሁሉን ሊያደርግ ይችላል፥ ሀብታም ነውና የወደደውን ይገዛል፥ ጠቢብ ነውና ሁሉን ሊመረምር ይቻለዋል። ከእርሱ ይበልጥ የሚችል የለም።

የዚህ መጽሐፍ ትምህርት ከመዝ. 49 ጋር ይስማማል፤ በዮሐ. 10፥10 የተጻፈውንም በንጽጽር ያሳስባል። አከፋፈል :-

ም. 1። መክብብ የተባለው ሰው ከፀሐይ በታች ማለት በዓለም ላይ ሁሉም ዞሮ ዞሮ እንደሚመጣ፥ ፍጻሜም ነገር እንደሌለ አይቷል።

ም. 2። የዚህ ዓለም ደስታ የተባለውን ሁሉ፥ ሣቅን፥ መጠጥን፥ ጨዋታን፥ ሀብትን፥ ዕውቀትን፥ ሥልጣንን፥ ንብረትን፥ የሴቶችን ፍቅር፥ ክብርን ማናቸውንም ነገር ሁሉ ፈትኗል፤ ፈትኖም ሁሉም ከንቱ፥ ነፋስን እንደመከተል፤ የማያጠግብ መሆኑን ተገንዝቧል።

ም. 3-11። በዚህ ክፍል ሁለት አሳቦች ጐን ለጐን ይሄዳሉ።

(ሀ) እግዚአብሔር በነገሩ ከሌለ ሁሉ ከንቱ ነው። ለምሳሌ ሞት ከንቱ ነው፥ ሰው እንደሚሞቱ እንስሳዎች ብቻ ነውና፤ 3፥18-21።

(ለ) ራሲቱ ዓለም ውብ ናት የእግዚአብሔርም ፍጥረት ናት፥ ስለዚህ ሰው በዓለም ሳለ ይደሰትባት፤ ተስፋውን ግን አይመሥርትባት፤ 3፥11-13።

ም. 12። አጥጋቢ ደስታ፥ የተትረፈረፈም ሕይወት በዓለም ነገር በማናቸውም በኩል አይገኝም። የዚህ መጽሐፍ ፍሬ ነገር በም. 13-14 በአጭሩ ተገልጿል።

**መክፈቻ**፤ የጥንት ሰዎች ከእንጨት መክፈቻ ይሠሩ ነበር፤ መሳ. 3፥25። በምሳሌነት ሥልጣንንና ኃይልን ያመለክታል። ጴጥሮስ በበዓለ ኀምሳ ቀን ለአይሁድ፥ በቆርኔሌዎስ ቤት ለአሕዛብ የመንግሥተ ሰማያት መግቢያ የሆነውን የወንጌልን በር ከፈተ፤ ስለዚህም የመንግሥተ ሰማያትን መክፈቻ እንደ ተቀበለ ተነገረለት፤ ኢሳ. 22፥22፤ ማቴ. 16፥19፤ ሉቃ. 11፥52፤ ራእ. 1፥18።



ቍልፎች

**መኮስተሪያ**፤ የመብራት ጫፍ ማቅኛ፥ ክሩ ተቃጥሎ በአንድ በኩል ሲዘቀዘቅ የሚያነሣው፤ ዘጸ. 25፥38፤ 1ነገ. 7፥49።

**መውጊያ**፤ የተሳለ የችንካር ወይም የምስማር ጫፍ መሳይ። በጥንት ጊዜ ገበሬዎች በጅራፍ ፈንታ በመውጊያ በሬዎችን ያንቀሳቅሱ ነበር፤ መሳ. 3፥31። በመ.ቅ. ለልዩ ልዩ ነገሮች ምሳሌ ሆኖ ተጠቅሷል፤ መክ. 12፥11፤ ሐ.ሥ. 9፥5፤ 26፥14። ነገር ግን በ1ቆሮ. 15፥55:56 ላይ በግልጥ የኃጢአት ምሳሌ ሆኖ ተተርጕሟል።

**የመዐርግ መዝሙር**፤ ከመዝሙር 120 እስከ መዝሙር 134 የሚገኙት መዝሙሮች የመዐርግ መዝሙሮች ይባላሉ። ለመዝሙሮቹ ይህ ስያሜ የተሰጠበት ምክንያት እስራኤላውያን ለዓመት በዓል ወደ ኢየሩሳሌም ሲወጡ በመንገድ ላይ ይዘምሩአቸው ስለነበር ነው።

**መዓዛ**፤ ሽታ፤ ዘፍ. 8፥21፤ ኤፌ. 5፥2።

**መዘምራን**፤ «ዜማ» ይመ.

**መዝሙረ ዳዊት**፤ ይህ መጽሐፍ በውስጡ 150 መዝሙርና ጸሎት፥ ትምህርትና ቅኔ በአንድነት ይገኙበታል፤ 15፤ 17፤ 31፤ 56 ይመ.። ለቤ.ክ. ሆነ ለግል ጸሎት እጅግ የተወደደ መጽሐፍ ነው። በውስጡ ለየጊዜው ሁሉ፥ ማለት ለሐዘንና ለደስታ፥ ለመልካምም ሆነ ለክፉ፥ የአንድ ሰው ሁኔታ ማንኛውም ቢሆን የሚያመሰግንበት ወይም የሚተክዝበት ተስማሚ መዝሙር ወይም ጸሎት ይገኛል። በዚህ መጽሐፍ እየተጠቀመ ሰው ከእግዚአብሔር ጋር ሊገናኝ ኅብረትም ሊያደርግ፥ በመንፈስም ሊጐለምስና ሊያድግ ይችላል፤ 2ጴጥ. 3፥18። መዝሙራቱ ሁሉ ዳዊት የጻፋቸው አይደሉም፤ ሆኖም በአርእስቱ ላይ የዳዊት ስም በ82 ተጠቅሷል፤ በቀሩትም የቆሬ ልጆች ስም በ11

ተጠቅሷል (42፤ 44 ይመ.)፥ የአሳፍ በ12 ተጠቅሷል (50፤ 73 ይመ.)፥ የኤማንና የኤታን የሙሴም በ3 ተጠቅሷል፤ 88-90 ይመ.።

መዝሙራትን ማን እንደሰበሰበ አልታወቀም፤ ቢሆንም በ1ዜ.መ. 16 ላይ ዳዊት በታቦቱ ፊት የሚዘምሩ መዘምራንን እንዳደራጀ ስለምናነብ እርሱ ሥራውን ጀምሮ ይሆናል። ከእርሱ በኋላ ግን ሌላ ሰው በነገሩ ገብቷል፤ የምናውቀውም፥ ከምርኮ ዘመን በኋላ የተዘጋጁት እንደ መዝ. 74፤ 96፤ 137፤ የሐጌና የዘካርያስ እንደተባሉትም እንደ 146፤ 147፤ 148 ስለሚገኙ ነው።

«መዝሙረ ዳዊት» በ5 መጻሕፍት ተከፍሏል። እነዚህም መጻሕፍት ፦ 1ኛ፤ 1-41። 2ኛ፤ 42-72። 3ኛ፤ 73-89። 4ኛ፤ 90-106። 5ኛ፤ 107-150 ናቸው። የአንዱ መጽሐፍ ፍጻሜ የሚታወቀው «ከዘላለም እስከ ዘለዓለም እግዚአብሔር ይባረክ። አሜን አሜን (ይሁን ይሁን)» የሚሉ ቃላት ስለተጻፉበት ነው።

የመዝሙራት ቍጥር ጥንቃቄ ይጠይቃል፥ ምክንያቱም፥ በምሥራቅና በምዕራብ አብ.ክ. ዘንድ ልዩነት አለና። የምሥራቅ ቤ.ክ. 70 ሊቃውንት ሲተረጕሙት በተጠቀሙባቸው ቍጥሮች ሲሠሩ ምዕራባውያን የዕብራይስጥን ይዘዋል። ስለዚህ ከመዝ. 9፥20 እንሥቶ እስከ መዝ. 146 ድረስ ምሥራቃውያን (ለምሳሌ ኢትዮጵያውያን) በምዕራባውያን ለምሳሌ በእንግሊዝኛ ቍጥር ላይ 1 መጨመር ያስፈልጋቸዋል። እንዲሁም በአማርኛ መጽሐፍ መዝ. 22 የሆነው በእንግሊዝኛ መዝ. 23 ይሆናል፤ መዝ. 106 የሆነው ደግሞ በእንግሊዝኛ መጽሐፍ 107 ይሆናል። ይህ መጽሐፍ የዕብራይስጥን ቍጥሮች ይከተላል (በዱሮው መ.ቅ. በቅንፍ ውስጥ ያሉትን ማለት ነው)።

የመዝሙራትን ዓይነቶች መለየት አስቸጋሪ ቢሆንም ቀጥሎ የተጻፈው ስንጠረዥ ሊመራን ይችላል።

1. የምስጋና መዝሙሮች፥ ሀ) የእግዚአብሔርን ስም የሚያመሰግኑ፥ እንደ 8፤ 20፤ 30፤ 34፤ 65፤ 68፤ 75፤ 76፤ 83፤ 87፤ 88፤ 91፤ 95፤ 107፤ 136 ናቸው።

ለ) ከመከራ ማዳኑን የሚያወድሱ ፦ 18፤ 30፤ 34፤ 65፤ 75፤ 115፤ 116፤ 118፤ 138።

2. ኃጢአተኛ በኃጢአቱ የሚያዝንበት ፦ 6፤ 32፤ 38፤ 51፤ 102፤ 130፤ 143።

3. በመከራ ያለ ሰው የሚጸልይበት (የሚጽናናበት) ፦ 3፤ 5፤ 7፤ 17፤ 20፤ 30፤ 31፤ 54፤ 59፤ 142።

4. እግዚአብሔርን፥ ሕጉንና ቤቱን የሚናፍቅበት ፦ 16፤ 17፤ 19፤ 40፤ 42፤ 45፤ 63፤ 73፤ 84፤ 119፤ 122፤ 132።

5. ስለ መሲሕ የሚናገሩ ፦ 2፤ 8፤ 16፤ 22፤ 40፤ 45፤ 69፤ 72፤ 110።

6. ለትምህርት የሚሆኑ ፦ 37፤ 49፤ 50፤ 52-55፤ 60፤ 74፤ 78፤ 89፤ 104፤ 119፤ 127።

7. ካህናት የቤተ መቅደስን ደረጃዎች ሲወጡ የሚዘምሩአቸው የመዐርግ መዝሙሮች ፦ 120-134።

8. ሃሌ ሉያ ብለው የሚጀምሩት የሃሌል መዝሙሮች (የስብሐት) ፦ 111-113፤ 146፤ 148-150።

በዓለም አብ.ክ. ዘንድ እጅግ የታወቁት ፦ 23 የእረኛነት፤ 32 የይቅርታ፤ 45 የረዳትነት፤ 51 የንስሐ፤ 91 የጠባቂነት፤ 103 የምስጋና፤ 104 የፍጥረት፤ 119 የሕግ፤ 121 የመንገደኛ፤ 139 ስለ ድንቅ እውቀቱ።

በጥቂት መዝሙሮች ላይ ጸሓፊው ጠላቶቹን ሲረግምና በቀል ሲመኝባቸው ይገኛል፤ 35፤ 59፤ 69፤ 109። «ይህስ ተገቢ ነውን?» ብለን ብንጠይቅ ተገቢ አይደለም፤ ሆኖም በቅዱሳን ዘንድ እንኳ ይህ ክፉ መንፈስ በልባቸው ተደብቆ ገና እንደሚያድርና ማንም ሰው «እኔ ፍጹም ነኝ» ሊል አለመቻሉን ያስረዳናል፤ ፊል. 3፥12። ስለነዚህ መዝሙሮች አንዳንዶች እንደሚከተለው ያስባሉ። ሰዎች ምእመናንን በጽድቅ ምክንያት ቢጠሉአቸው የጽድቅና የእግዚአብሔር ጠላቶች ናቸው። በጥላቻም ጸንተው ቢቆዩ እግዚአብሔር ጽድቁን እንዲገልጽ ማለት እንዲፈርድባቸው መመኘት ትክክለኛ ስሜት ነው፤ መዝ. 139፥21-24፤ ኢሳ. 66፥24፤ ዘካ. 2፥8፤ ራእ. 6፥9:10፤ 19፥1-3። እንደዚሁም የሰይጣንንና የተከታዮቹን ውድቀት በተስፋ መጠበቅ ይገባል፤ ዘካ. 3፥2፤ ዮሐ. 12፥31:32። በዚህ አስተሳሰብ እነዚህን መዝሙሮች መዘመር ለክርስቲያን ተገቢ ነው። «ቅኔ»፥ «ግጥም» ይመ.

**የመዝሙራት አርእስት፤** በዕብራይስጡ መዝሙረ ዳዊትና በጥንታውያን ትርጕሞች በአብዛኛዎች መዝሙራት መግቢያ ላይ የተለያዩ አርእስት ይገኛሉ። ለምሳሌ ፦ ለመዘምራን አለቃ፤ በበገናዎች፤ በዋሽንት፤ ስለ ስምንተኛ፤ በሙትላቤን፤ አታጥፋ፤ 4፤ 5፤ 6፤ 9፤ 75 ... ወዘተ። አርእስት የመዝሙሩን ዓይነትና ባለ መዝሙሩን ያመለክታሉ። ስለ አሌፋት (119) «ዕብራይስጥ» ይመ.

**መዝሙር፤** ልዩ ልዩ ስልትና ቃና ባለው ድምፅ የሚዘም፥ በዜማ መሣሪያ የሚቀርብ መንፈሳዊ ማኅሌት፤ ዘጸ. 15፥20-21፤ ኤፌ. 5፥19፤ ቈላ. 3፥16። የዳዊት መጽሐፍ በሙሉ መዝሙር ይባላል፤ ሉቃ. 24፥44፤ ሐ.ሥ. 1፥20። ኢየሱስ ከደቀ መዛሙርቱ ጋር ከመጨረሻው እራት በኋላ ዘመረ፤ መዝ. 147፥1፤ ማቴ. 26፥30። «ዜማ» ይመ.

**መዝገብ፤** የተከማቸ ማንኛውም ሀብትና ንብረት፤ ምሳ. 10፥2። የምግባር ውጤትና የሃይማኖት ምሳሌ ነው፤ ማቴ. 6፥19:21፤ 13፥44። የምጽዋት ገንዘብ የሚሰበሰብበት ሣጥን ሙዳየ ምጽዋት፤ ማር. 12፥41።

**መያዣ፤** ባለዕዳ ቃሉን እስኪፈጽም ለዋስትና የሚሰጠው፤ ዘፍ. 38፥17:18። ድሆች እንዳይጐዱ ፀሐይ ሳትገባ ለመያዣ የተወሰደው ልብስ ይመለሳል፤ ዘጸ. 22፥26:27። ሰው ለዕለት የሚጠቀምበት እንደ

ወፍጮ እንደ መበለትም ልብስ ... ወዘተ መያዣ አይሆንም ነበር፤ ዘዳ. 24፥6:10:17። ምእመናን የእግዚአብሔርን ስጦታ ሁሉ እንደሚቀበሉ መንፈስ ቅዱስ መያዣቸው ነው፤ 2ቆሮ. 1፥22፤ ኤፌ. 1፥14። የመጋረጃ ሜንጦ መያዣ ተብሏል፤ ዘጸ. 26፥6:11፤ 35፥11።

**መደረቢያ**፤ ከሌላ ልብስ በላይ የሚደረብ ጋቢ፥ ካባ ወይም ኮት፤ 1ሳሙ. 2፥19።

**መደነቅ**፤ መገረም፤ ኢሳ. 52፥14። «ድንቅ» ይመ.

**መዳራት**፤ የዝሙትና የአመንዝራነት መጀመሪያ ድርጊት (ዋዜማ) ነው። ወንድና ሴት በፍትወት ተነድተው ሲጫወቱ መዳራት ይባላል (ማር. 7:22)።

**መዳብ**፤ ከልዩ ልዩ የብረታ ብረት ዓይነት ጋር የተቀላቀለ ክልስ ናስ፤ ሕዝ. 22፥18።

**መድኃኒት**፤ አዳኝ፤ በሥጋ በኩልም ሆነ በመንፈስ በኩል ከማናቸውም ክፋትና ጉዳት የሚያድን ወይም የሚጠብቅ መድኃኒት አዳኝ ታዳጊ ይባላል።

በጥንት ጊዜ ሰዎች ከልዩ ልዩ ዕፀዋት መድኃኒት እየቀመሙ በሽተኞችን ይፈውሱ ነበር፤ ኢሳ. 38፥21:22፤ ኤር. 8፥22፤ ሕዝ. 47፥12። ኩፋሌ በተባለው ተጨማሪ መጽሐፍ (10፥7) እንደተገለጠው እግዚአብሔር ለኖኅ መድኃኒትነት ያላቸውን ዕፀዋት አሳይቶታል። «ፈውስ» ይመ.

በብ.ኪ. እግዚአብሔር የእስራኤል መድኃኒት ይባላል፤ መዝ. 44፥3:7፤ ኢሳ. 43፥11፤ 45፥21፤ 60፥16። በእግዚአብሔር እየተመራ እስራኤልን ከጠላቶቻቸው እጅ ያዳነ ሰው ደግሞ አዳኝ ወይም ታዳጊ ይባል ነበር፤ መሳ. 3፥9፤ 2ነገ. 13፥5፤ ነህ. 9፥27፤ አብ. 21። እነዚህ የብ.ኪ. አዳኞች፥ መሳፍንትና ነገሥታት የእውነተኛው አዳኝ የክርስቶስ ምሳሌ ወይም ጥላ ነበሩ፤ ሁሉም በትንቢት መልክ ወደ ክርስቶስ አመለከቱ።

በአ.ኪ. መድኃኒት ሲል ስለ እግዚአብሔር አብ ወይም ስለ ክርስቶስ ብቻ እንጂ ስለ ሰው አይናገርም፤ ሉቃ. 1፥47፤ 1ጢሞ. 1፥1፤ 2፥3:4፤ ቲቶ 1፥3። ክርስቶስ ዓለምን ከኃጢአትና ከዘለዓለማዊ ሞት ስላዳነ መድኃኒት ይባላል፤ ቲቶ 1፥4፤ 2፥12:13፤ 3፥6:7፤ 2ጢሞ. 1፥10:11፤ 2ጴጥ. 1፥1:11፤ 2፥20፤ 3፥1:2:18። ክርስቶስ ሰውን ከኃጢአት እንዲያድን፥ መድኃኒትም እንዲሆን ወደ ዓለም ገባ፤ ሉቃ. 2፥11፤ ማቴ. 1፥21፤ ሉቃ. 19፥10። የክርስቶስ አዳኝነት ለሰው ሁሉ ስለሆነ ክርስቶስ የዓለም መድኃኒት (አዳኝ) ይባላል፤ ዮሐ. 4፥42፤ 1ዮሐ. 4፥14። «ደኅንነት» ይመ.

**መድረክ**፤ ሳንቃ የሚቆምበት የቤት ታችኛው ጉበን፤ 1ነገ. 7፥6፤ ሕዝ. 41፥16:17።

**መጅ**፤ የወፍጮ ልጅ። ከታች የሚሆነው ትልቁ ድንጋይ ወፍጮ ሲባል ከላይ የሚሆነው ደግሞ መጅ ይባላል። በሙሴ ሕግ መጅ በመያዣ አይወሰድም ነበር፤ ዘዳ. 24፥6። አቢሜሌክ በመጅ ተገደለ፤ መሳ. 9፥53።



ወፍጮና መጅ

**መገለጥ**፤ የተሰወረው ግልጥ መሆን። እግዚአብሔር ራሱን ባይገልጥ ኖሮ ልናውቀው አንችልም ነበር፤ ኢሳ. 55፥8፤ 1ቆሮ. 2፥14፤ 2ቆሮ. 4፥4። ግን ኃይሉንና ክብሩን ፈቃዱንም ገልጧል። ይህም ሲባል እግዚአብሔር ለሰው አስፈላጊውንና ተገቢውን እንጂ ሁሉን ገልጧል ማለት አይደለም፤ ዘዳ. 29፥29። መገለጥ በመሠረቱ ሁለት ዓይነት ነው፥ ሀ) በተፈጠሩ ነገሮችና በመጋቢነት ተግባሩ፤ ሮም 1፥19-21፤ ሐ.ሥ. 14፥17። ነገር ግን ይህ መገለጡ በቃል ጭምር ካልተደገፈ የእግዚአብሔርን ፈቃድ ሙሉ በሙሉ አይገልጥም፤ የደኅንነትንም መንገድ አያሳይም። ለ) በቃሉ፤ በመ.ቅ. የመገለጥ ቃል በብዙ መንገድ መጥቷል ፦

1. ቃልን በመናገር፤ በብ.ኪ. ዘመን ይህ ዋና መንገድ ነበር። ብዙ ጊዜ አሳቡን ለነቢያት ሰጠ። እነርሱም ለሕዝብ ተናገሩ፤ ዕብ. 1፥1።

2. በሕልምና በራእይ፤ ዘኍ. 12፥6-8። ሆኖም ሰዎች እንዲያስተውሉ ብዙ ጊዜ ትርጓሜ አስፈላጊ ነበር፤ ዳን. 2፥19:28-30።

3. ዓለምን በመፍጠሩና በመጠበቁ (መዝ. 19፤ ሮም 1፥19-21፤ ሐ.ሥ. 14፥17)፥ ተአምራትንም በማድረግ (መዝ. 78፥11)፥ ሆኖም ብዙ ጊዜ ተአምራት በእግዚአብሔር እንደተደረጉ ሰዎች በመልእክተኞች ቃል ተረዱ።

4. በልጁ፤ ዮሐ. 1፥18፤ 1ጢሞ. 3፥16፤ ዕብ. 1፥2:3።

5. መንፈስ ቅዱስን በመስጠት፤ ዮሐ. 15፥26፤ 16፥13፤ 1ቆሮ. 2፥11:12፤ ዕብ. 2፥4።

እግዚአብሔር የሃይማኖትን ትምህርት ፈጽሞ ለሐዋርያት ገልጧልና ምእመናን አሁን በዚህ ትምህርት ጸንተው መቆም እንጂ ሌላ መግለጫ መፈለግ ወይም መከታተል አይገባቸውም፤ ኤፌ. 3፥5:6፤ ይሁዳ 3፤ ራእ. 22፥18:19። የእግዚአብሔር መገለጥ በመ.ቅ. ተጽፏል። መ.ቅ.ም ጠቅላላውን የእግዚአብሔርን መገለጥ የያዘ ነው።

ዛሬም ሰዎች ራሳቸው ለግል ሕይወታቸው የእግዚአብሔርን ፈቃድ እንዲያውቁ መንፈስ ቅዱስ ይመራቸዋል፤ ሮም 8፥14፤ 1ቆሮ. 14፥26፤ ገላ. 2፥2።

በዓለም መጨረሻ ክርስቶስ ይገለጣል (ሉቃ. 17፥30፤ ቲቶ 2፥12:13)፥ ደግሞም የሰው ሥውር አሳብ ሁሉ ይገለጣል፤ ሉቃ. 12:2፤ ሮም 8፥18፤ 1ቆሮ. 3፥13።

**የመገናኛ ድንኳን፤** «የእግዚአብሔር ማደሪያ» ይመ.

**መጊዶ፤** የጦር ሠራዊት ሰፈር ማለት ነው። በቀርሜሎስ ተራራዎች ከሰሜን ወደ ደቡብ ጋዛንና ደማስቆን የሚያገናኘውን መንገድ ለመጠበቅ የተመሸገ ከተማ ነበር። እስራኤል እስከ ሰሎሞን ድረስ በከተማው አልተቀመጡም። በሰሎሞን ጊዜ ምሽጉ 200 በ300 ሜትር ገደማ ነበር፤ 1ነገ. 9፥15። በመጊዶ ብዙ ጦርነት ተደርጓል። በመጊዶ አጠገብ ዲቦራ ሲሣራን ድል አደረገች (መሳ. 5፥19)፤ ፈርዖን ኒካውም ኢዮስያስን ገደለ፤ 2ነገ. 23፥29:30። ታላቁ የዓለም መጨረሻ ጦርነት በአርማጌዶን ይደረጋል፤ አርማጌዶን ማለት የመጊዶ አምባ ማለት ነው፤ ራእ. 16፥16። ካ 4 ሀ።

**መጊዶል፤** መግደላ። በገሊላ ባሕር ዳር ያለ ከጥብርያዶስ በስተሰሜን 4 ኪ.ሜ. ርቆ የሚገኝ ምሽግና መንደር፤ ማቴ. 15፥39። በማርቆስ 8፥10 ድልማኑታ ተብሏል። የመግደላዊት ማርያም መንደር ነበር፤ ሉቃ. 8፥2።

**መጋረጃ፤** ለመገናኛ ድንኳኑና ለአደባባዩ ብዙ መጋረጃዎች ነበሩአቸው፤ ዘጸ. 26፥7-10፤ 38፥9-20። በተለይም በቅድስቱና በቅድስተ ቅዱሳኑ መካከል ለመለያ ለቅድስቱም በር መጋረጃዎች ተሠሩ፤ ዘጸ. 26፥31-34፤ 36፥35-38። ክርስቶስ በመሞቱ ወደ እግዚአብሔር የሚያደርሰውን መንገድ ስለ ከፈተ የቤተ መቅደስ መጋረጃ ተቀደደ፤ ማቴ. 27፥51፤ ዕብ. 10፥20።

**መጋቢ፤** በትልቅ ሰው ቤት በሁሉ ላይ ኀላፊ ሆኖ የሚያስተዳድርና ለሠራተኞች የሚከፍል፥ በቤ.ክ. በኀላፊነት የሚያገለግሉትም መጋቢዎች ተብለዋል፤ ዘፍ. 15፥2፤ ሉቃ. 12፥42፤ 16፥1-8፤ 1ቆሮ. 4፥1-2፤ ቲቶ 1፥7፤ 1ጴጥ. 4፥10። «የእግዚአብሔር መጋቢነት» ይመ.

**መግነዝ፤** «መቃብር፥ መቅበር» ይመ.

**መጎምጀት፤** ማናቸውም ዓይነት ምኞት፤ ማር. 7፥22።

**መጎናጸፊያ፤** ትልቅ ጋቢ፥ ቡልኮ፤ 1ነገ. 19፥13፤ ኢዮብ 1፥20።

**መጠጥ፤** የእስራኤል ሕዝብ ውኃ (ዘፍ. 24፥11-18)፥ የወይን ጠጅ (ዘፍ. 14፥18፤ ዮሐ. 2፥3) ወተትም ይጠጡ ነበር፤ መሳ. 4፥19። «ስካር» ይመ.

**የመጠጥ ቍርባን፤** ከልዩ ልዩ መሥዋዕትና ቍርባን ጋር የወይን ጠጅ ይቀርብ ነበር፤ ዘጸ. 29፥40:41።

**መጥመቂያ፤** የወይን ፍሬ መርገጫ ጉድጓድ። በእስራኤል አገር ብዙ ጊዜ በዐለታማ መሬት ላይ ይቆፈር፥ ይፈለፈል ነበር፤ ኢሳ. 63፥2:3፤ ማር. 12፥1። የጠጅ መጣያ ጋንም መጥመቂያ ይባላል፤ ኤር. 48፥33። መጥመቂያ የእግዚአብሔር ፍርድ አደባባይ ምሳሌ ነው፤ ራእ. 14፥19:20።

**መጥራት፤** ጠራ፤ ቃሉ እንደ አቀራረቡ ስም መስጠትን (ዘፍ. 1፥5)፥ መጸለይን (ዘፍ. 4፥26)፥ ለአገልግሎት መሾምን (ኢሳ. 49፥1፤ ማር. 1፥20)፥ ወንጌል መቀበልን ሊያሳይ ይችላል፤ ዕብ. 3፥1። በማቴ. 22፥14 የተጠሩ ቃሉን የሚሰሙ ሁሉ



ግብጻውያን የወይን ፍሬ ሲለቅሙ በመጥመቂያም ሲረግጡና የወይን ጠጅን በጋን ሞልተው በጥቃ ካሸጉ በኋላ በማኅተም ሲያትሙ የሚያሳይ በ1400 ዓመት ገደማ ከክ.በ. ከተሣለ ሥዕል የተገኘ

ናቸው። ጳውሎስ በዚህ ቃል ሲጠቀም ጥሪውን የሚቀበሉትን ያመለክታል፤ ሮም 8፥28-30። እግዚአብሔር ኃጢአተኞችን በወንጌል በኩል ለደኅንነት ይጠራል፤ ኢሳ. 55፥1፤ ዮሐ. 3፥16፤ ሐ.ሥ. 17፥30። የወንጌሉን ጥሪ ግን ሁሉም አይቀበሉም፤ የሚቀበሉት በልቡናቸው ልዩ የእግዚአብሔር ጥሪ ሲሰማቸው ብቻ ነው፤ ማቴ. 13፥9፤ 22፥14፤ ዮሐ. 6፥44፤ ራእ. 2፥11:29፤ 3፥22።

**መጥን**፤ አንድ ባለ ሥልጣን አገሩን ሲጐበኝ የሚዋጣ መቀበያ ምግብ፥ መሸኛ ገንዘብ፤ ዕዝ. 4፥13።

**መጭመቂያ**፤ መጥመቂያና መጭመቂያ አንድ ነው፤ ዘኊ. 18፥27:30። ገጽ 45 ይመ.

**መጻተኛ**፤ በሰው አገር የሚኖር፥ እንግዳ፥ መጤ፤ ዘዳ. 24፥19-21፤ 1ጴጥ. 2፥11። «እንግዳ» ይመ.

**መጻጻ**፤ የሚሆመጥጥ፥ የሚቆጠቁጥ ፈሳሽ ነገር። ለቍስል ይጠቅማል፤ ምሳ. 25፥20።

**መጽሐፈ ኪዳን**፤ መጻሕፍተ ኪዳን የተባሉት የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤ.ክ. ጌታችን ከትንሣኤው በኋላ፥ ከዕርገቱም በፊት ተናግሮአቸዋል ብላ ከአ.ኪ. መጻሕፍት ጋር ቈጥራ የምትቀበላቸው ሁለት መጻሕፍት ናቸው። አንደኛው በ59 አንቀጽ የተከፈለ የቤ.ክ. ሥርዓት መጽሐፍ ነው፤ ሁለተኛውም ስለ ዳግም ምጽአት የሚገልጽ መጽሐፍ ነው።

**መጽሐፍ**፤ ማናቸውንም ዓይነት ጽሑፍ ሊያመለክት ይችላል። መ.ቅ. የተጻፈበት ዘመን በወረቀት ወይም በብራና የተጻፈውን ሲያመለክት የጥቅልል መጽሐፍ እንጂ በቅጠል ላይ የተጻፈ መጽሐፍ አልነበረም፤ ዘፍ. 5፥1፤ ራእ. 22፥19። በአዲስ ኪዳን መጽሐፍ ወይም መጻሕፍት ሲል የብ.ኪዳንን መጻሕፍት ያመለክታል፤ ዮሐ. 7፥38፤ 2ጢሞ. 3፥15-17። «ጥቅልል» ይመ.

**መጽሐፍ ቅዱስ**፤ የተቀደሰ ወይም የተለየ መጽሐፍ ማለት ነው። መ.ቅ. የቅዱሳት መጻሕፍት መዝገብ ነው። የመ.ቅ. ክፍሎች ብሉይ ኪዳንና አዲስ ኪዳን ናቸው። ብ.ኪ. ከ1400-400 ከክ.ል. በልዩ ልዩ ቦታዎች አርባ በሚያህሉ ልዩ ልዩ ጸሓፊዎች እንደተጻፈ ይነገራል። አ.ኪ. ከ45-96 ዓ.ም. በስምንት ሰዎች ተጻፈ። መ.ቅ. በሙሉ ወይም በከፊል ከ2100 ቋንቋዎች በላይ ተተርጕሟል።

<u>ብሉይ ኪዳንና ኢየሱስ</u>፤

በኢየሱስ ዘመን የነበሩት አይሁድ የብ.ኪ. መጻሕፍትን ሳይጠራጠሩ እንደ እግዚአብሔር ቃል ተቀበሉአቸው፥ የሃይማኖታቸውም መሠረት አደረጉአቸው፤ ዘዳ. 4፥2፤ ዮሐ. 5፥39፤ 9፥28። እንደዚሁም ኢየሱስ የእግዚአብሔር ቃል የማይለወጥና የማይሻር መሆኑን መሰከረ፤ ሉቃ. 16፥17፤ ዮሐ. 10፥35። ብ.ኪ.ን በሚገባ ባለማወቃቸው አይሁድን ወቀሰ፤ ማር. 12፥24። የአዳምን ወይም የዘፍጥረትን ጸሓፊ ቃላት እንደ እግዚአብሔር ቃላት አከበራቸው፤ ዘፍ. 2፥24 እና ማቴ. 19፥4:5። ክርስቶስ ብ.ኪ.ን ሊፈጽም እንደመጣ አስተማረ (ማቴ. 5፥17)፥ ብ.ኪ. ስለ እርሱ እንደሚናገር አሳየ፤ ሉቃ. 18፥31፤ 24፥27:44። ሐዋርያት ኢየሱስን ተከትለው ከብ.ኪ. እየጠቀሱ ሰበኩ፥ አስተማሩም፤ ለምሳሌ ሐ.ሥ. 2፥16-35፤ ዕብ. 1። ስለዚህ የሐዋርያት ትምህርት የብ.ኪ. ትርጓሜ ነው ማለት ይቻላል።

<u>አዲስ ኪዳንና ሐዋርያት</u>፤

ኢየሱስ ቃሉን እንዲገነዘቡ፥ የሚመጣውንም እንዲያውቁ የእውነት መንፈስን እንደሚልክላቸው ለሐዋርያት ተስፋ ሰጠ፤ ዮሐ. 14፥26፤ 16፥13። ቅዱስ ጳውሎስም ከሰው ሳይሆን ከክርስቶስ ወንጌልን እንደተቀበለ ገለጠ (ገላ. 1፥11-17)፥ ሐዋርያት የእግዚአብሔርን ቃል በመጻፍ ላይ እንደነበሩ ዐወቁ። ጳውሎስ ዘዳ. 25፥4ን እና የጌታችንን ቃል በአንድነት ጠቀሰ፤ ሉቃ. 10፥7፤ 1ጢሞ. 5፥18። ጴጥሮስ ስለ ጳውሎስ መጻሕፍት ይመሰክራል፤ 2ጴጥ. 3፥15:16። ሐዋርያት ቅዱሳት መጻሕፍት በመንፈስ ቅዱስ መሪነት እንደተጻፉ ዐወቁ፤ 1ቆሮ. 2፥13፤ 2ጢሞ. 3፥15-17፤ 2ጴጥ. 1፥21።

<u>መጽሐፍ ቅዱስና ቤተ ክርስቲያን</u>፤

ከመጀመሪያ ጀምሮ ቤ.ክ. አይሁድ ያወቁአቸውን የብ.ኪ. መጻሕፍት ተቀበለች። በሐዋርያት ወይም በሐዋርያት ሥልጣን የተጻፉትን መጻሕፍት ሰብስባ እንደ እግዚአብሔር ቃል ተቀበለቻቸው። የቤ.ክ. አባቶች የአ.ኪ. መጻሕፍትን እየጠቀሱ አስተማሩ። ቅዱስ አትናቴዎስ በ367 ዓ.ም. በጻፈው በፋሲካ ዕለት ቃለ በረከት የአ.ኪ. መጻሕፍት ሃያ ሰባት ብቻ መሆናቸውን ተናግሯል። እንደዚሁም በ397 ዓ.ም በሰሜን አፍሪካ በካርታጎ (በካርቴጅ በቱኒዝያ) የተደረገው ሲኖዶስ ሃያ ሰባቱን መጻሕፍት አጸደቀ። ምእመናን ቅዱሳት መጻሕፍትን በብዙ ጥንቃቄ ይገለብጡ ነበር። ማተሚያ እስከተገኘበት ጊዜ ድረስ በሙሉ ወይም በከፊል ከአ.ኪ. 4500 የግሪክ ቅጂዎች ተገኝተዋል፤ የመጀመሪያው ግልባጭ በ150 ዓ.ም. ገደማ ተጻፈ። በዕብራይስጥ የተጻፉ ብዙ የብ.ኪ. ቅጂዎች አሉ፤ የመጀመሪያው ቅጂ በ200 ከክ.ል. ገደማ ተጻፈ። ቅዱሳት መጻሕፍት በጥንት ዘመን በጥቅልል እየተጻፉ በልዩ ልዩ ምኵራብና ቤ.ክ. ይሰበሰቡና ይነበቡ ነበር። ቅደም ተከተላቸውም ልዩ ልዩ ነበር። ለምሳሌ አትናቴዎስ ሰባቱን መልእክታት ከጳውሎስ መልእክታት አስቀድሟል። የካርታጎ ሲኖዶስ ግን የመጻሕፍቱን ተራ እንደ አሁኑ የኢትዮጵያ መ.ቅ. ተራ አድርጓል። በምዕራብ ቤ.ክ. ከጥንት ጀምሮ የያዕቆብ መልእክት ከዕብራውያን መልእክት ቀጥሎ ይገኛል። በደቂቀ ነቢያትም ቅደም ተከተል ጥቂት ልዩነት አለ፤ ሆኖም መጻሕፍቱ አንድ ናቸው። ከጥንት ጀምሮ ቅጂዎች መጻሕፍትን በክፍል፥ በምዕራፍና በቍጥር ለይተዋል። ነገር ግን እንደ ገና በ1228 ዓ.ም. በምዕራፍ በ1551 ዓ.ም. ምዕራፉ በቍጥር መከፈል ተጀመረ። አከፋፈሉ እስካሁን ድረስ ይሠራበታል። «የቅዱሳት መጻሕፍት

ዝርዝር»፥ «የቅዱሳት መጻሕፍት ትርጉም»፥ «ቃል»፥ «ትንቢት»፥ «ነቢይ»፥ «ሐዋርያ»፥ «መገለጥ»፥ «ሥልጣን»፥ «መንፈስ ቅዱስ 10»፥ «ጽሕፈት» ይመ.

**መጽናናት፤** ከሐዘን፥ ከፍርሃት መመለስና መበረታታት፥ ልባዊ ዕረፍት ማግኘት፤ ማቴ. 5፥4፤ ሉቃ. 16፥25፤ 2ቆሮ. 1፥3-6፤ 7፥4:6:7:13፤ ቆላ. 2፥2፤ 1ተሰ. 3፥7። ይስሐቅ ርብቃን በማግባቱ ከእናቱ ሞት ተጽናና፤ ዘፍ. 24፥67። ሩት በችግሯ ጊዜ ከቦዔዝ ርኅራኄንና ድጋፍን በመቀበሏ ተጽናናች፤ ሩት 2፥13። መንፈስ ቅዱስ የምእመናን አጽናኝ ወይም ጰራቅሊጦስ ነው፤ ዮሐ. 14፥16-17። «ሌላ አጽናኝ» ሲል እስካሁን ጌታ ኢየሱስ አጽናኛቸው ነበር፤ እርሱን መሳይና በእርሱ ምትክ የሚያጽናናቸው መንፈስ ቅዱስን ላከላቸው። እግዚአብሔር የምእመናን አጽናኝ ነው፤ 2ቆሮ. 1፥3-4። መጽናናት ማለት መጠናከር ሲሆን፥ ምእመን በሚገጥመው ድካም የሚያጠነክረው እግዚአብሔር ነው፤ በኃጢአቱም ብዛት የተስፋ መቍረጥ ድካም እንዳይገጥመው አጽናኙ ወይም ጠበቃው ክርስቶስ አለ፤ 1ዮሐ. 2፥1-2።

**መፋታት፤** የባልና የሚስት የጋብቻ ኪዳን መፍረስ። ባልና ሚስት እንዲለያዩ የእግዚአብሔር ፈቃድ አይደለም፤ ሚል. 2፥16፤ ማቴ. 19፥6። ነገር ግን በዝሙት ምክንያት ተፈቅዷል፤ ማቴ. 5፥31:32፤ 19፥7-9። አንድ ሰው ሚስቱ ክርስቲያን አለመሆኗን ምክንያት በማድረግ ሊፈታት አይገባውም። ግን እርሷ በፈቃድዋ ብትተወው እርሱ ሌላ ሴት ሊያገባ ይችላል። ሴትም በዚህ ዓይነት ልታገባ ትችላለች፤ 1ቆሮ. 7፥12-17።

**ሙላት፤** ፍጹም የሞላ፥ ብዙ ጊዜ ሙሉ በረከት ያለበትን ያመለክታል። ግኖስቲኮች በዚህ ቃል ተጠቅመው በምሥጢሮቻቸው ብቻ መንፈሳዊ «ሙላት» እንደሚገኝ በማስተማራቸው፥ ሐዋርያት የእግዚአብሔር «ሙላት» በክርስቶስ የሚገኝ መሆኑን በማመን አማኝ በክርስቶስ ብቻ «ሙላትን» እንደሚቀበል ያስተማሩ ይመስላል፤ ዮሐ. 1፥16፤ ኤፌ. 1፥23፤ 3፥18-19፤ 4፥12-13፤ ቆላ. 1፥19-20፤ 2፥9-10።

**ሙሴ፤** እግዚአብሔር እስራኤልን ከግብጽ ባርነት አውጥቶ እስከ ዮርዳኖስ ድረስ ለማድረስ የተጠቀመበት የእስራኤል መሪ። ይህንንም ሲያደርግ ሙሴ ሰፊ የሆነ አገልግሎት ነበረው።

1. የሕዝቡ መሪና ፈራጅ ነበረ፤ ዘጸ. 18፥13:26።

2. እግዚአብሔር በሲና ሕግን ሰጥቶ ከእስራኤል ጋር ላደረገው ቃል ኪዳን ሙሴ መካከለኛ ነበረ፤ ዘጸ. 19፥7፤ ም. 24፤ ገላ. 3፥19።

3. እንደተገለጠለትም ምሳሌ የመገናኛውን የድንኳን መቅደስ አሠራ፤ ዘጸ. ም. 25-31፤ ም. 35-40።

4. በእጁም አሮንና ልጆቹን ለክህነት የለየ፥ ለሕዝቡም የጸለየ ካህን ነበረ፤ መዝ. 99፥6፤ ዘሌ. 8 እና 9፤ ዘጸ. 32፥30-32።

5. እግዚአብሔር «አፍ ለአፍ በግልጥ» ያናገረው እግዚአብሔርንም «ፊት ለፊት» ያወቀ ነቢይ ነበረ፤ ዘኍ. 12፥6-8፤ ዘዳ. 34፥10-12።

6. አብዛኛዎቹ በእጁ ስለ ተጻፉ አምስቱ የኦሪት መጻሕፍት «የሙሴ» ተብለው ይጠራሉ፤ ሉቃ. 24፥27።

7. ለክርስቶስ ምሳሌ ሆነ፤ ነቢይ በመሆኑ (ዘዳ. 18፥15-19፤ ሐ.ሥ. 3፥22:23)፥ በታማኝነቱ (ዕብ. 3፥1-6)፥ የማደሪያውን ድንኳን በመትከሉና በማገልገሉ (ዕብ. 8 እና 9)፥ በደረሰበትም ተቃውሞ፤ ሐ.ሥ. 7፥35-40:52:53።

8. በኮሬብ በተገለጠው ክብር ፊቱ የበራ የእግዚአብሔር ሰው ሙሴ፥ በደብረ ታቦር የክርስቶስን የክብር መገለጥ አየ። ሙሴ አስቀድሞ በትንቢትና በምሳሌ ስለ ክርስቶስና ስለ ሞቱ ጻፈ (ዮሐ. 5፥46፤ 3፥15)፥ ስለ ትንቢቱም መፈጸም በታቦር ከክርስቶስ ጋር እንዲነጋገር ዕድል አገኘ፤ ሉቃ. 9፥30:31፤ ዘጸ. 34፥29-35፤ 2ቆሮ. 3፥7-18።

<u>የሙሴ ሕይወት ታሪክ</u>

ሙሴ 120 ዓመት ኖረ። ስለ ሕይወቱ ዘመን የምናነበው ከዘጸ. መጀመሪያ እስከ ዘዳ. መጨረሻ ድረስ ነው። ይህም ዘመን በሦስት ዋና ዋና ክፍሎች ይከፈላል።

1. ሙሴ ከሌዊ ነገድ በተወለደ ጊዜ የእስራኤል ሕዝብ በግብጽ በባርነት ነበሩ፤ ዘጸ. 2፥1:2። የፈርዖን ሴት ልጅ «ከውሃ አውጥቼዋለሁና» ስትል ሕፃኑን ሙሴ ብላ ሰየመችው፤ ዘጸ. 2፥10።

አስቀድሞ በእናቱ እጅ፥ በኋላም እንደ ፈርዖን የልጅ ልጅ ተቈጥሮ ሲያድግ እግዚአብሔርን እየፈራ፥ የግብጽንም ትምህርት እየተማረ «በቃሉም በሥራውም የበረታ ሆነ»፤ ከዘጸ. 2 ጋር ዕብ. 11፥23 ያነጻጽሩ። ሐ.ሥ. 7፥20-22 ይመ.

2. አርባ ዓመትም ሲሞላው ወንድሞቹን ለመርዳት አስቦ ወደ እነርሱ ወጣ። ነገር ግን አንዱን ግብጻዊ በቍጣ ተነሣሥቶ ከገደለ በኋላ ወደ ምድያም ሸሸ። ሴቶች ልጆቹንም ስለረዳቸው የምድያም ካህን በቤቱ ተቀበለው፥ ከልጆቹም አንዲቱዋን ዳረለት። ሙሴም እስከ አርባ ዓመት ድረስ የአማቱን በጎች በምድረ በዳ ሲጠብቅ ቆየ፤ ዘጸ. 2፥11-25፤ ዕብ. 11፥24-26፤ ሐ.ሥ. 7፥23-29። ዘኍ. 12፥1 ሙሴ ኢትዮጵያዊቱን አገባ ይላል። አንዳንዶች ይህች የዮቶር ልጅ ሲፓራ ናት፥ ሌሎች ከግብጽ አገር ከእስራኤል ጋር የመጣች ሌላ ሴት ናት ይላሉ።

3. በጎችንም በኮሬብ አቅራቢያ ሲጠብቅ ሳለ እግዚአብሔር ተገለጠለት፥ እስራኤልን ከባርነት እንዲያወጣ ወደ ፈርዖን ላከው፤ ወንድሙ አሮን እንዲናገርለት ፈቀደ፤ ዘጸ. ም. 3 እና 4፤ ሐ.ሥ. 7፥30-34። ፈርዖንም ሕዝቡን አልለቅም ባለ ጊዜ እግዚአብሔር በሙሴ እጅ ዐሥር መቅሠፍት በግብጽ ላይ አወረደ፤ ዘጸ. ም. 5-11። የግብጽ በኵር ልጆች ሁሉ በሞቱ ጊዜ የፋሲካን ደም በመርጨት ሙሴ ሕዝቡን በደህና ከግብጽ አወጣቸው፤ ም. 12 እና

13። ፈርዖንም ተከተላቸው፣ እግዚአብሔርም የሙሴን ጸሎት ሰምቶ የኤርትራን ባሕር በመክፈል ሕዝቡን አዳነ፤ ዘጸ. 14፥1-15፥21፤ ዕብ. 11፥27-29። በማራ፣ በኤሊም፣ በራፊዲምም በኩል ወደ ሲና ሲጓዝ፣ ሙሴ የሕዝቡን ማንጐራጐር እየታገሠ በጸሎት የሚያስፈልገውን ሁሉ ሰጣቸው፤ እጆቹንም ዘርግቶ በሚጸልይበት ጊዜ ጠላቶቻቸው በውሃ ሰጥመው ተሸነፉ፤ ዘጸ. 15፥22-18፥27።

አንድ ዓመትም በሲና ሰፍረው ሳሉ በሙሴ አማካይነት ሕግን ተቀብለው ቅዱስ ሕዝብ እንዲሆኑለት ከእግዚአብሔር ጋር ቃል ኪዳን ገቡ፤ ዘጸ. ም. 19-24። ሙሴ 40 ቀን በሲና ላይ በመቆየቱ (ዘጸ. 24፥12-31፥18) ሕዝቡ ዐምፀው ለወርቅ ጥጃ ሰገዱ። ሙሴም ተቈጥቶ ጽላቱን መሬት ላይ ጣለው፣ ጣዖቱን ሰባበረ፣ ለሕዝቡ ግን ጸለየ። እንደገና 40 ቀን በተራራው ላይ ቆየ፤ እግዚአብሔርም ይቅር በማለት ቃል ኪዳኑን እንደገና አጸናለት፤ ዘጸ. ም. 32-34። ሙሴም የመገናኛውን የድንኳን መቅደስ አሠርቶ ተከለ፤ ዘጸ. ም. 35-40። ስለ መሥዋዕትና ስለ ክህነትም ስለሚያደርጉትም ጉባኤ ሁሉ ትእዛዛትን ተቀበለ፤ አሪት ዘሌ.። ሕዝቡንም ቈጠረ፣ በየነገዳቸውም በመቅደሱ ዙሪያ እንዲሰፍሩ አደረገ፤ ለጕዞም አዘጋጃቸው፤ ዘኍ. 1፥1-10፥10። እስከ ከነዓን ደቡባዊ ዳርቻም አደረሳቸው፤ ዘኍ. 10፥11-12፥16። ከአለማመን የተነሣ፣ እንወጣም ካሉ በኋላ እንደ እግዚአብሔር ትእዛዝ እስከ 40 ዓመት ድረስ በምድረ በዳ ጠበቃቸው፤ ዘኍ. 13፥1-19፥22።

<u>የሙሴ ጠባይ</u>

ሙሴ እጅግ ትሑት ነበር፤ ግብጻዊውን በንዴት የገደለው ሙሴ፣ የእስራኤልን መቃወምና ማጕረምረም ብዙ ጊዜ ታገሠ። ራሱንም ለእነርሱ አሳልፎ ለመስጠት ዝግጁ መሆኑን በጸሎቱ በመግለጽ፣ እግዚአብሔር እንዳያጠፋቸው ለመነ፤ ዘጸ. 32፥11-14፤ ዘኍ. 11፥1-15፤ 12፥1-16፤ 14፥10-19፤ 21፥4-9። እስራኤላውያን በምድረ በዳ በሚንከራተቱባቸው ዓመታት መጨረሻ ላይ ግን አንድ ጊዜ ሙሴ ተቈጥቶ እግዚአብሔርን አሳከበረምና ወደ ከነዓን እንዳይገባ ተከለከለ፤ ዘኍ. 20፥1-13፤ መዝ. 106፥32:33።

<u>የሙሴ የመጨረሻ ተግባራት</u>

ሙሴ በኤዶምና በሞዓብ ዳርቻ በኩል እስራኤልን አዞራቸው፤ የአሞራውያንን ነገሥታትም በማሸነፍ ከዮርዳኖስ በስተ ምሥራቅ ወዳለው ሰፊ ምድር አገባቸው፤ ዘኍ. 21-32። ሁለተኛ ትውልድ የእግዚአብሔርን ቃል ኪዳን እንዲያድሱና ሕጉን እንዲጠብቁ በማለት፣ እርሱ ያደረገላቸውን ምሕረት አሳስቦ ለሕዝቡ ተናገረ (አሪት ዘዳግም)። በራሱ ምትክ ኢያሱ መሪ እንዲሆን አደረገ፤ ዘኍ. 27፥12-23። ሙሴ በግጥም/ማስጠንቀቂያ ከሰጠ በኋላ (ዘዳ. 32)፣ የእስራኤልን ነገዶች ባረከ፤ ዘዳ 33። ከዚያም በኋላ ፈስጋ በተባለው ተራራ ራስ ላይ ሆኖ የከነዓንን ምድር ካየ በኋላ ሞተ፤ ዘዳ. 34።

**ሙሽራ፤** ለመጀመሪያ የሚያገባ በልዩ ልብስ ያጌጠ፣ በሠርገኞች የታጀበ ወንድ፤ ማቴ. 25፥1-6፤ ዮሐ. 2፥9። ሙሽራ የፀሐይ (መዝ.19፥5)፣ የእግዚአብሔር አብ፣ የክርስቶስም ምሳሌ ነው፤ ኢሳ. 62፥5፤ ማቴ. 9፥15፤ ዮሐ. 3፥29። የምእመናንም ምሳሌ ነው፤ ኢሳ. 61፥10። «ጋብቻ»፣ «ሠርግ» ይመ.

**ሙሽራይቱ**(ሙሽሪት)፤ ለመጀመሪያ ጊዜ የምታገባ ሴት፤ ዮሐ. 3፥29። ለጋብቻዋ ልዩ ልብስ ትለብሳለች፤ ኤር. 2፥32። የቤተ እስራኤልና የቤ.ክ. ምሳሌ ናት፤ ኢሳ. 62፥5፤ ራእ. 21፥2:9፤ 22፥17።

**ሙሾ፤** የሐዘን ቅኔ፣ እስራኤላውያን ሰው ሲሞት ልዩ ቅኔ ይቀኙ ነበር (2ሳሙ. 1፥17)፣ እንደዚሁም አገር ሲወድቅ ሙሾ ያሞሹ ነበር፤ ሰቆቃወ ኤርምያስ ሙሾ ነው፤ 2ዜ.መ. 35፥25፤ ኤር. 7፥29፤ ሕዝ. 19፥1።

**ሙቀጫ፤** ጐድጓዳ ድንጋይ ወይም እንጨት፤ እህል፣ ወይራ፣ ቅመማ ቅመም ሁሉ ይወቀጥበታል፤ ዘጸ. 27፥20፤ ዘኍ. 11፥8።

**ሙታን፤** የሞቱ ሰዎች፤ ሉቃ. 24፥5። ሙታን 1. በሥጋ (ሮም 6፥4)፣ 2. በመንፈስ የሞቱ ማለት ነው፤ ሮም 6፥13፤ ኤፌ. 2፥1። «ሞት» ይመ.

**ሙታን ሳቢ፤** የሞቱ ሰዎች ነፍሳትን የሚጠራና የሚጠይቅ፤ ዘዳ. 18፥11። «ጥንቆላ» ይመ.

**ሙዳ፤** በየብልቱ ዓይነት የወጣ የሥጋ ቁራጭ፤ ሚክ. 3፥3።

**ሙጭልጭላ፤** «እንስሳት» ይመ.

**ሚሊዮን፤** ዐሥር መቶ ሺህ፤ 1ዜ.መ. 22፥14፤ 2ዜ.መ. 14፥9።

**ሚልካ፤** 1. የአብርሃም ወንድም የሐራን ልጅ፣ የሎጥም እኅት፤ አጎትዋን ናኮርን አገባች። ከልጆችዋም አንዱ ባቱኤል የርብቃና የላባ አባት ነበረ፤ ዘፍ. 11፥27-29፤ 22፥20-23፤ 24፥15። 2. ከምናሴ ነገድ ከነበረው ከሰለጰዓድ ልጆች አንዲቱ ሚልካ ተባለች፤ ዘኍ. 36፥11። «ሰለጰዓድ» ይመ.

**ሚልክያስ፤** «መልእክተኛዬ» ማለት ነው። ሚልክያስ የእግዚአብሔርን ቃል ተቀብሎ ትንቢትን ተናገረ። ከዚህ በቀር ስለ ነቢዩ ሌላ ነገር አልተጻፈም። ሚልክያስ የነቢይነት መጠሪያ ስም ወይም የግል ስም ሊሆን ይችላል፤ ሚል. 1፥1።

**የሚልክያስ ትንቢት፤** በ470 እና በ440 መካከል ከክ.በ. በኢየሩሳሌም ተነገረ። ይህም በዕዝራና በነህምያ ዘመን ነው፤ ሚል. 2፥10:11። ከዕዝ. 9፥1:2 እና ከነህ. 13፥23-31 ጋር ያነጻጽሩ። የትንቢቱ አሳብ እንደሚከተለው ነው። እግዚአብሔር ሕዝቡን ይወዳል፤ 1፥1-5። እስራኤል ግን የማይገባውን በመሠዋት (1፥6-8)፣ ከሌላ ወገንና

ሃይማኖት የተገኙትን በማግባት (2፥10:11)፥ በመፋታት (2፥16)፥ በከንቱ ንግግር (2፥17)፥ በጭካኔ (3፥5)፥ ዐሥራትን ባለ መስጠት (3፥6-10)፥ በጠቅላላውም እግዚአብሔርን በመናቅ (3፥14) ያጠፉ ነበር። ስለዚህ እግዚአብሔር ይፈርዳል (3፥2)፥ ከክፋት የሚመለሱትን ግን ይባርካል፤ 3፥10-12:16:17፤ 4፥2። እንግዲህ ጌታ ወደ መቅደሱ ይመጣል፥ የእግዚአብሔርም ቀን ሳይደርስ መልእክተኛውን ኤልያስን ይልካል፤ 3፥1-3፤ 4፥1-6። ሚልክያስ ይህን ከተናገረ አምስት መቶ ዓመታት ያህል በኋላ መጥምቁ ዮሐንስ ትንቢቱን ፈጸመ፤ ማር. 1፥2፤ ሉቃ. 1፥17፤ ማቴ. 11፥14።

አከፋፈል ፦

1. የእግዚአብሔር ፍቅር፤ 1፥1-5።
2. የካህናትና የሕዝብ ኃጢአት፤ 1:6-2፥17።
3. ከኃጢአት የሚያነጻ የመሚሕ መምጣት፤ 3፥1-6።
4. የተሐድሶ ጥሪ፤ 3፥7-12።
5. እግዚአብሔር ከሚነቅፉትና ከሚፈሩት መካከል ይለያል፤ 3፥13-4፥3።
6. ለእግዚአብሔር ቀን መዘጋጀት፤ 4፥4-6።

**ሚሎ**፤ የተሞላ ማለት ነው። በኢያቡስ (በኢየሩሳሌም) አንድ ቦታ ሚሎ ተባለ። ሚሎ ከምሽጉ ቅጥር አንድ ክፍል ወይም ልዩ ግንብ ሊሆን ይችላል፤ 2ሳሙ. 5፥9፤ 1ነገ. 9፥15:24፤ 2ዜ.መ. 32፥5።

**ሚስት**፤ ወንድ ለሆነ ሰው በሕይወቱ ዘመን በደስታም በመከራም አብራው እንድትኖርና እንድትረዳው የተፈጠረች የኑሮ ጓደኛ። ለባልዋም መገዛት (መታዘዝ) አለባት፤ ዘፍ.-2፥18:20፤ ምሳ. 31፥10-31፤ ኤፌ. 5፥22-33፤ 1ጴጥ. 3፥1-6። መልካም ሚስት በራስ ዘውድ ተመስላለች (ምሳ. 12፥4)፥ ከእግዚአብሔርም የሚገኝ በረከትና ስጦታ ናት፤ ምሳ. 18፥22፤ 19፥14። «ጋብቻ»፥ «ሴት» ይመ.

**ሚስያ**፤ ጢሮአዳ የሚባለው ከተማ የነበረበት በትንሹ እስያ የነበረ አገር፤ ሐ.ሥ. 16፥7:8። ካ.6ቀ።

**ሚኒት**፤ በአሞን አገር የነበረ ከተማ፤ መሳ. 11፥33፤ ሕዝ. 27፥17።

**ሚካ**፤ እናቱ ላሠራችው ምስል በዐሥር ብር ካህን የቀጠረ የኤፍሬም አገር ሰው፥ በኋላ የዳን ሰዎች ምስሉንም ካህኑንም ወሰዱበት፤ መሳ. 17 ና 18።

**ሚካኤል**፤ «እንደ እግዚአብሔር ማን ነው?» ማለት ነው። ሰይጣንን በመቃወም የእግዚአብሔርን ሕዝብ የሚጠብቅ የመላእክት አለቃ፤ ዳን. 10፥13-21፤ 12፥1፤ ይሁዳ 9፤ ራእ. 12፥7።

**ሚክያስ**፤ የስሙ ትርጉም «እንደ እግዚአብሔር ያለ ማን ነው?» ማለት ነው። 1. የይምላ ልጅ፤ በአክዓብ ዘመን መንግሥት በሰማርያ ትንቢት ይናገር ነበር። የአክዓብንም ሞት ተነበየ፤ 1ነገ. 22፥8:13-28፤ 2ዜ.መ. 18፥7-27። 2. ሞሬታዊው ሚክያስ፤ በኢዮአታምና በአካዝ በሕዝቅያስም ዘመን በይሁዳ ነቢይ ነበረ፤ ሚክ. 1፥1፤ ኤር. 26፥18:19። በአባቱ ስም ሳይሆን፥ ሞሬሼት ጌት በተባለች ከተማ ስም ይታወቃል፤ ሚክ. 1፥1:14።

**የሚክያስ ትንቢት**፤ ሚክያስ ትንቢት መናገር የጀመረው ከሰማርያ ውድቀት በፊት፥ ማለትም ከ722 ከክ.በ. ነበር። አስቀድሞ ሰማርያ (1፥6) በኋላም ኢየሩሳሌም (3፥12) እንደሚፈርስ ተነበየ። ነገር ግን እግዚአብሔር እስራኤልን እንደ መንጋ ይሰበስባል (2፥12፤ 7፥14)፥ ኢየሩሳሌምን አጽንቶ ያሠራል (4፥1)፥ አሕዛብም እግዚአብሔርን ይፈልጋሉ፤ 4፥2፤ 7፥16:17። ይህም የሚፈጸመው በክርስቶስ ነው፤ 5፥2:4።

አከፋፈል ፦

1. የሰማርያና የኢየሩሳሌም መፍረስ፤ ም. 1-3።
2. የእግዚአብሔር መንግሥት መመሥረት፤ ም. 4። ደግሞም 2፥12:13።
3. ከቤተ ልሔም የሚወጣ ገዥና እረኛ፤ ም. 5።
4. እግዚአብሔር ከሕዝቡ ጋር ያለው ክርክር፤ ም. 6።
5. ተግሣጽና ተስፋ፤ ም. 7።

**ሚዛን**፤ የክብደት መለኪያ፥ እስራኤል በእውነተኛ ሚዛን እንዲሠሩ ታዘዙ፤ ዘሌ. 19፥36፤ ሕዝ. 45፥10። ሐሰተኛ ሚዛን እጅግ አስጸያፊ ነው፤ ምሳ. 11፥1፤ አሞ. 8:5፤ ሚክ. 6፥11። የሰው አካሄድ ይመዘናል፤ ኢዮብ 31፥5:6፤ ዳን. 5፥27፤ ራእ. 6፥5። «ክብደት»፥ «መስፈሪያ» ይመ.



አንድ ግብጻዊ ወርቅ ሲመዝን፤ 1450 ዓመት ገደማ ከክ.በ. ከተገኘ ሥዕል የተገለበጠ

**ሚዜ**፤ በጋብቻ ጊዜ የሙሽራውና የሙሽራይቱ ዋና ረዳት፤ ዮሐ. 3፥29።

**ሚዳቋ**፤ «እንስሳት» ይመ.



ሚዳቋ

**ማሄጃ**፤ ጥርስ መሳይ ያለው የእህል መውቂያ መሣሪያ፤ ኢሳ. 28፥27። እስራኤል በጠላቶቹ ላይ በማሄጃ ተመሰለ፤ ኢሳ. 41፥15።



ገበሬ እህሉን በማሄጃ እያበራየ ሲወቃ

**ማለደ**፤ 1. ጧት ተነሣ፤ ማቴ. 20፥21፤ ሉቃ. 21፥38። 2. አንዱ ስለ ሌላው ለመነ፤ ሮም 8፥26:34። «ምልጃ» ይመ.

**ማልኮስ**፤ በጌቴሴማኒ ጆሮውን ጴጥሮስ የቈረጠውና ኢየሱስ የፈወሰው የሊቀ ካህናቱ ባሪያ፤ ሉቃ. 22፥49-51፤ ዮሐ. 18፥10-11።

**ማረ**፤ 1. ዕዳን ወይም ብድርን ሰረዘ፤ ቸርነት አደረገ፤ ማቴ. 5፥7፤ 9፥27፤ 18፥27:32-33። 2. ኃጢአትን ይቅር አለ፤ ማቴ. 18፥35፤ ሮም 9፥14-18፤ 11፥30-32። «ምሕረት» ይመ.

**ማረሻ**፤ በመጀመሪያ ሰዎች በሹል እንጨት ያርሱ ነበር። በሳኦል ዘመን ገበሬዎች የብረት ማረሻን ለምደው ነበር፤ 1ሳሙ. 13፥19-21። ሰይፍን ቀጥቅጦ ማረሻ ማድረግ የሰላም ምልክት ነበር (ኢሳ. 2፥4፤ ሚክ. 4፥3)፥ እንደዚሁም ማረሻን በመቀጥቀጥ ሰይፍ ማድረግ ለጦርነት የመዘጋጀት ምልክት ነበር፤ ኢዩ. 3፥10።

**ማር**፤ ጣፋጭነት ያለው የንብ ሥራ ውጤት፤ መዝ. 118፥12። ማር ከዐለት ድንጋይ (ዘዳ. 32፥13)፥ ከዛፍና ከመሬት (1ሳሙ. 14፥25:26)፥ ከምድረ በዳም ይገኛል፤ ማቴ. 3፥4። ከነዓን ወተትና ማር የምታፈስ አገር ተባለች፤ ዘጸ. 3፥8። ማር እንዲሁ ይበላ ነበር (ሉቃ. 24፥42)፥ ለምግብ ማዘጋጃም ይጠቅም ነበር፤ ዘጸ. 16፥31። ማር ጣፋጭ በመሆኑ የብዙ አስደሳች ነገር ምሳሌ ነው፤ መዝ. 19፥9:10፤ ምሳ. 5፥3፤ ሕዝ. 3፥2:3፤ ራእ. 10፥9። «ምግብ» ይመ.

**ማርቆስ**፤ ወንጌልን እንደጻፈ የቤ.ክ. አባቶች ይናገራሉ። በአይሁድ ዘንድ ስሙ ዮሐንስ ሲሆን፥ በሮማውያን ዘንድ ማርቆስ ይባላል። እናቱ ማርያም ትባላለች፤ ሐ.ሥ. 12፥12። ቤትዋ በኢየሩሳሌም ነበር። ምእመናን በቤትዋ ለጸሎት ይሰበሰቡ ነበር፤ ሐ.ሥ. 12፥12-17። አጎቱ በርናባስና ጳውሎስ ለስብከት ሥራ ሲጓዙ ማርቆስ ያገለግላቸው ነበር፤ ቆላ. 4፥10፤ ሐ.ሥ. 12፥25። ከእነርሱ ጋር እስከ ጴርጌ ደርሶ ከዚያ በኋላ ወደ ኢየሩሳሌም ተመለሰ፤ ሐ.ሥ. 13፥13። ጳውሎስና በርናባስ በእርሱ ምክንያት ሲለያዩ ማርቆስ ከበርናባስ ጋር ወደ ቆጵሮስ ሄደ፤ ሐ.ሥ. 15፥36-39። በኋላ ግን ጳውሎስ አመስግኖታል፤ ቆላ. 4፥10፤ 2ጢሞ. 4፥11፤ ፊልሞና 24። ማርቆስ ከጴጥሮስም ጋር ሠርቷል፤ 1ጴጥ. 5፥13። ብዙ ሊቃውንት በማርቆስ 14፥51-52 ላይ የተጠቀሰው ወጣት ማርቆስ ነው ይላሉ። በእስክንድርያ ቤተ ክርስቲያንን እንደመሠረተ አበው ይናገራሉ። እስካሁንም የእስክንድርያ ቤ.ክ. አባት ይባላል።

**የማርቆስ ወንጌል**፤ ጸሓፊው ማርቆስ የተባለው ዮሐንስ ነው፤ «ማርቆስ» ይመ.። የቀደሙት የቤ.ክ. አባቶች ይህ ወንጌል ለሮማውያን በ60 ዓ.ም. ገደማ በሮም ሳይጻፍ እንዳልቀረ ጠቁመዋል። የተጻፈውም ሮማውያን፥ ክርስቶስ የእግዚአብሔር ልጅ መሆኑን እንዲያምኑ ነው፤ ወንጌሉ ሮማዊ የሆነ የመቶ አለቃ እንዴት እንዳመነ ይተርካል፤ 1፥1፤ 15፥39። ብዙዎች «ማርቆስ የሐዋርያው ጴጥሮስ የመንፈስ ልጅ ነውና ይህ ወንጌል ጴጥሮስ ያስተማረው ወንጌል ነው» ይላሉ። «ወንጌል» ይመ.

የማርቆስ ወንጌል ከሌሎች ወንጌላት አጭር ነው፤ ምክንያቱም የጌታን ልደት ባለመጻፉ፥ ከብ.ኪ. ብዙ ባለመጥቀሱ፥ ብዙ የክርስቶስን ትምህርቶችና ምሳሌዎች ባለመመዝገቡና ስለ ትንሣኤውም በአጭሩ የሚተርክ በመሆኑ ነው። ሆኖም ግን የክርስቶስ ተአምራትና ሌሎች ታሪኮች በረጅሙ ሕያውነት ባለው አገላለጥ ተተርከዋል፤ ይህም ብዙ ጊዜ «ወዲያው» በሚለው ቃል ይታያል፤ 1፥12:28:29:31 ... ወዘተ። ኢየሱስ ክርስቶስ ሁልጊዜ በሥራ ላይ የሚገኝ «ሊያገለግልና ነፍሱን ለብዙዎች ቤዛ ሊሰጥ የመጣ» መሆኑ በዚህ ወንጌል

ተብራርቷል፤ 10፥45።

በዚህ ወንጌል ትኵረት የተሰጣቸው የሚከተሉት ናቸው ፦

ሀ) ክርስቶስ የእግዚአብሔር ልጅ መሆኑ፤ 1፥1:11፤ 3፥11፤ 5፥7፤ 9፥7፤ 12፥1-11፤ 13፥32፤ 15፥39። በተለይ ሮማውያን ይህን እምነው እንዲቀበሉት የኃይል ሥራው በሰፊው ተመዝግቧል።

ለ) ክርስቶስ ሰው መሆኑ፤ «የሰው ልጅ» ብሎ ራሱን ጠራ፤ የኢየሱስም ሰብአዊ ስሜቶች ተመዝግበዋል፤ 1፥41:43፤ 3፥5፤ 7፥34፤ 8፥12:33፤ 10፥14:16:21።

ሐ) ክርስቶስ ለመሞት መምጣቱ፤ የሕማማትን ሳምንት በሰፊው ይተርካል፤ ም. 11-15፤ በተጨማሪም 8፥31፤ 9፥30-32፤ 10፥33-34:38:45 ይመ.

መ) መሥዋዕትነቱና ለደቀ መዛሙርት ምሳሌ መሆኑ፤ 8፥34-38፤ 9፥33-35፤ 10፥29-31:42-45።

ሠ) ጊዜው ከመድረሱ በፊት መሲሕነቱን አለመግለጡ፤ 1፥34:44፤ 3፥12፤ 5፥43፤ 7፥36-37፤ 8፥26:30፤ 9፥9።

አከፋፈሉ እንደሚከተለው ሊሆን ይችላል ፦

1. ጌታ በገሊላ እየተመሰገነ እንዳስተማረ፤ ም. 1-6።
2. ተቃዋሚዎች እንደተነሡበት፤ ም. 7-9።
3. ጌታ ወደ ኢየሩሳሌም እንደተጓዘ፤ ም. 10።
4. በኢየሩሳሌም እንዳስተማረ፤ ም. 11-13።
5. ስለ ጌታ ሕማማትና ትንሣኤ፤ ም. 14-16።

**ማርታ፤** ከኢየሩሳሌም አጠገብ ባለው ቢታንያ በተባለው መንደር የምትኖር፥ የአልዓዛርና የማርያም እኅት። በብዙ ሥራ ስለደከመች ኢየሱስ ገሠጻት። በኋላም ወንድምዋ ሲሞት ስለ ትንሣኤ ሙታን ያላትን እምነት ገለጠች፤ ሆኖም ኢየሱስ አልዓዛርን ወዲያውኑ የሚያስነሣ አልመሰላትም ነበር፤ ሉቃ. 10፥38-41፤ ዮሐ. 11፥20-27:39 :40።

**ማርያም፤** በመ.ቅ. አያሌ ሴቶች በዚህ ስም ይጠራሉ።

1. ማርያም፤ የሙሴ እኅት። ሙሴ በወንዝ ዳር በተጣለ ጊዜ እኅቱ ማርያም በእርሱ ላይ የሚሆነውን ለማወቅ ትመለከተው ነበር። በጥበብም የፈርዖንን ልጅ አነጋገረቻትና እንድታጠባው የገዛ እናታቸውን ለሞግዚትነት ጠራች፤ ዘጸ. 2፥4-8። እስራኤላውያን የኤርትራን ባሕር ከተሻገሩ በኋላ ነቢይት ሆና ሴቶችን በመዝሙርና በምስጋና መራች፤ ዘጸ. 15፥20:21። በኋላ ግን ማርያም የሙሴን የበላይነት ካለመውደድዋ የተነሣ፥ ኢትዮጵያዊት ሚስቱን ምክንያት አድርጋ አማችው። እግዚአብሔር ግን በለምጽ ቀጣት፤ ዘኍ. 12፤ ዘዳ. 24፥9። ገና በጕዞ ሳሉ ሞተች። በቃዴስም ተቀበረች፤ ዘኍ. 20፥1።

2. ማርያም፤ የዩቴር ልጅ የዕዝራ የልጅ ልጅ፤ 1ዜ.መ. 4፥17።

3. ማርያም ቅድስት ድንግል፤ የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ እናት። ወላጆችዋ በመ.ቅ. በስማቸው አልተጠቀሱም። ሆኖም ከዳዊት ዘር ተወልዳለች። ለዮሴፍም ታጨች፤ ማቴ. 1፥1-18፤ ሮም 1፥3። በናዝሬት ሳለች መልአኩ ገብርኤል ወደ እርስዋ ተላከ። ወንድን ሳታውቅም በመንፈስ ቅዱስ ኃይል ቅዱሱን የእግዚአብሔር ልጅ በድንግልና እንደምትወልድ አበሠራት። ቃሉን አምና ወደ ዘመድዋ ወደ ኤልሳቤጥ ሄደች፤ ሉቃ. 1፥26-40። ማርያም ወደ ዘካርያስ ቤት በገባች ጊዜ ኤልሳቤጥ ማርያም ጌታን እንደምትወልድ በመንፈስ ቅዱስ ተረድታ «ከሴቶች መካከል የተባረክሽ ነሽ» አለቻት። ደግሞም ማርያም የእግዚአብሔርን ቃል በማመንዋ ብፅዕት እንደሆነች ኤልሳቤጥ ገለጠች፤ ሉቃ. 1፥40-45። ማርያምም መልሳ ብሉይ ኪዳንን እየጠቀሰች እግዚአብሔርን አመሰገነች፤ ሉቃ. 1፥46-55። ሦስት ወር ያህል በኤልሳቤጥ ዘንድ ተቀመጠች (ምናልባት ዮሐንስ እስኪወለድ ድረስ ይሆናል) ወደ ቤትዋም ተመለሰች፤ ሉቃ. 1፥56። ዮሴፍ ግን እንደ ፀነሰች አይቶ ሊተዋት አሰበ። ነገር ግን የጌታ መልአክ እርስዋን ለመውሰድ እንዳይፈራ በሕልም ነገረው። ዮሴፍም ታዝዞ እጮኛውን ማርያምን ወሰደ። በኵር ልጅዋንም እስክትወልድ ድረስ አላወቃትም፤ ማቴ. 1፥18-25።

በመንግሥት ትእዛዝ ምክንያት ዮሴፍና ማርያም ወደ ቤተ ልሔም ሄዱ በዚያም ኢየሱስን ወለደች፤ ሉቃ. 2፥1-20። በሙሴ ሕግ መሠረት ወደ ቤተ መቅደስ በሄዱ ጊዜ ስምዖን አገኛቸው፥ «... በአንቺ ደግሞ በነፍስሽ ሰይፍ ያልፋል» ብሎ የሚደርስባትን ኀዘን ተነበየ፤ ሉቃ. 2፥22-35። ሰብአ ሰገል (ጠቢባን) ከሄዱ በኋላ ከዮሴፍና ከልጅዋ ጋር ወደ ግብጽ ሸሸች። ከዚያም ወደ ናዝሬት ተመለሰች፤ ማቴ. 2፥1-23። ኢየሱስን አሳደገች። የዐሥራ ሁለት ዓመት ልጅ ሲሆንም ለፋሲካ በዓል ወደ ኢየሩሳሌም ሄደች። በዚያም ኢየሱስ የተናገረውን ምንም ባታስተውለውም በልብዋ ትጠብቀው ነበር፤ ማርያም ከቤተሰቧ ጋር በናዝሬት የታወቀች ሴት ነበረች፤ ማቴ. 13፥55፤ ማር. 6፥3፤ ሉቃ. 2፥19:41-51።

በቃና ሠርግ የነበረባቸው ሰዎች የወይን ጠጅ አልቆባቸው ሲቸገሩ፥ ማርያም ለኢየሱስ ነግራ የመጀመሪያውን ተአምር አደረገ። ከዚያም በኋላ ከኢየሱስ ጋር ወደ ቅፍርናሆም ወረደች፤ ዮሐ. 2፥1-12። ኢየሱስ ሲያስተምር ትጐበኘው ነበር፤ ማቴ. 12፥46፤ ማር. 3፥31-35፤ ሉቃ. 8፥19-21። እስከ ቀራንዮ ተከተለችው፥ ኢየሱስ በመስቀል ላይ ሳለ ወደ ቤቱ እንዲወስዳት «እነኋት እናትህ» ብሎ ለዮሐንስ ነገረው። ዮሐንስም ወደ ቤቱ ወሰዳት፤ ዮሐ. 19፥25-27። ከትንሣኤ በኋላ ከሐዋርያት ጋር ነበረች፤ ሐ.ሥ. 1፥12-14። ብፅዕናዋ (ሉቃ. 1፥28:42-45:48)፥ እምነትዋ (ሉቃ. 1፥34-38:45፤ ዮሐ. 2፥5)፥ ታዛዥነትዋ (ሉቃ. 1፥38)፥ ትሕትናዋ (ሉቃ. 1፥38)፥ ምስጋናዋ (ሉቃ. 1፥47-55)፥ የብ. ኪ. ዕውቀትዋ (ሉቃ. 1፥47-55) ተጠቅሷል።

4. ማርያም፤ የማርታና የአልዓዛር እኅት፤ ዮሐ.

11፥1። ከኢየሩሳሌም አጠገብ ባለው ቢታንያ በተባለው መንደር ትኖር ነበር፤ ኢየሱስ ወደ ቤታቸው እየሄደ ይጠይቃቸው ነበር። ወደ እርሱ ቀርባ ቃሉን በጽሞና ስለሰማች ኢየሱስ አመስገናት፤ ሉቃ. 10፥39-42። ወንድምዋ አልዓዛር ከሙታን በተነሣ ጊዜ ከኢየሱስ ጋር በሰፊው ተነጋገረች (ዮሐ. 11)፥ ማርያም ኢየሱስ እንደሚሞት ስለተረዳችና በጣም ትወደው ስለነበረ በናርዶስ ሽቱ እግሩን ቀባችው፤ ዮሐ. 12፥1-8።

5. ማርያም መግደላዊት፤ ምናልባት ከገሊላ ከተማ ከመጌዶል መጥታ ይሆናል፤ ማቴ. 15፥39። ሰባት አጋንንት ካወጣላት በኋላ ኢየሱስን ታገለግል ነበር፤ ሉቃ. 8፥2፤ ማር. 15፥40:41። ይህች ሴት ለክርስቶስ መስቀልና መቀበሩ ምስክር ነበረች፤ ማቴ. 27፥55:56:61፤ ማር. 15፥40-47፤ ዮሐ. 19፥25፤ ማቴ. 28፥1-10፤ ማር. 16፥1-8፤ ሉቃ. 24፥10። ከትንሣኤው በኋላ በአትክልት ቦታ ለብቻዋ ክርስቶስ ታያት፤ ዮሐ. 20፥1-18።

6. ማርያም የታናሹ ያዕቆብና የዮሳም እናት፤ እርሷም ለክርስቶስ ስቅለትና መቀበር ምስክር ነበረች፤ ማር. 15፥40:47፤ 16፥1፤ ሉቃ. 24፥10።

7. ማርያም፤ የቀለዮጳ ሚስት። ጌታ በተሰቀለ ጊዜ ከመስቀሉ አጠገብ ቆማ ነበር፤ ዮሐ. 19፥25። ምናልባት ይህችና በ6 ላይ የተጠቀሰችው አንድ ይሆኑ ይሆናል።

8. ማርያም፥ የማርቆስ እናት፤ ሐ.ሥ. 12፥12።

**ማርዳ**፤ ከወርቅ ከሌላም የሚሠራ በአንገት የሚደረግ ጌጥ፤ ዘጸ. 35፥22።

**ማሮን**፤ ከአሶር አጠገብ የነበረ ሐይቅ። በማሮን አጠገብ ኢያሱ ከነዓናውያንን አሸነፈ፤ ኢያሱ 11:5-7። በኋላም ሐይቁ «ሁለህ» ተብሏል። ዛሬ የእስራኤል መንግሥት ሐይቁን ወራጅ ስላደረገው አንዳንድ ኩሬዎች ብቻ ቀርተዋል።

**ማሰርና መፍታት**፤ በእስራኤል የነበሩ ሕግ አዋቂዎች በውሳኔ ታሰረ ሲሉ ተከለከለ፥ ተፈታ ሲሉ ደግሞ ተፈቀደ ማለታቸው ነበረ። በዚህ አንፃር ጴጥሮስና ሐዋርያት በክርስቶስ ያመነ ኃጢአቱ የተሰረየለት፥ ያላመነ ግን ያልተሰረየለት መሆኑን ለመግለጥ እንዲሁም በጠቅላላ የወንጌልን ትምህርት ለመወሰን ሥልጣን ተሰጣቸው፤ ማቴ. 16፥19፤ ዮሐ. 20፥23። ይህንም ወንጌልን በመስበክና በማስተማር ፈጸሙ። ቀጥሎም ማሰርና መፍታት ስለ ሰው የተሰጠውን ውሳኔ ያመለክታል። የቤ.ክ. ሰዎች ማስጠንቀቂያዎችን ከሰሙና ንገሩን ካጡ በኋላ ሰውን ከማኅበራቸው ለማስወጣት ወይም ለመቀበል ሥልጣን ተሰጥቷቸዋል፤ ማቴ. 18፥15-20፤ ዮሐ. 20፥23። «ግዝት» ይመ.

**ማሳህ**፤ ፈተና ማለት ነው። እስራኤል በራፊዲም በውሃ እጦት ምክንያት እግዚአብሔርን ስለተፈታተኑ ቦታው «ማሳህ» ተባለ፤ ዘጸ. 17፥1-7፤ ዘዳ. 6፥16፤ 9፥22፤ 33፥8።

**ማሳት**፤ ሰውን ትክክለኛ አለማድረግ ወይም ዐውቆ ማታለል፤ ዘፍ. 3፥13፤ ዮሐ. 7፥12:47፤ ራእ. 20፥10። «ሐሰተኞች» ይመ.

**ማስተስረያ**፤ የይቅርታ ማስገኛ። እግዚአብሔር ጻድቅና ቅዱስ ስለሆነ ቍጣው በኃጢአተኛው ላይ ይኖራል። ሰው ከእግዚአብሔር ጋር እንዲታረቅ፥ ኃጢአቱን የሚሸፍን፥ የእግዚአብሔርንም ቍጣ የሚመልስ ማስተስረያ ያስፈልገዋል። ይህ ማስተስረያም የእግዚአብሔርን ጽድቅ አይቃረንምና በዚህ መሠረት እግዚአብሔር ይቅር ይላል። እስከ ክርስቶስ ሞት ድረስ የሚሠዋው የእንስሳት ደም ለሰው ኃጢአት ማስተስረያ ነበር፤ ዘጸ. 30፥10፤ ዘኍ. 16፥47። በእርግጥ የእንስሳት ደም ለዚህ የዋለው በራሱ ኃይል ሳይሆን ወደፊት ሊመጣ የነበረውን የክርስቶስን ደም በጥላነት ለማመልከት ነው። ዛሬ ግን ለአማኞች የኃጢአታቸው ማስተስረያ የክርስቶስ ደም ብቻ ነው፤ ሮም 3፥25፤ ዕብ. 9፥11:12:22፤ 1ዮሐ. 2፥2፤ 4፥10። «መሥዋዕት»፥ «ደም» ይመ.

**የማስተስረያ በዓል**፤ የእስራኤል ሕዝብ በሰባተኛው ወር በዐሥረኛው ቀን (ጥቅምት 10 ቀን ገደማ) ሥራቸውን ሁሉ ትተው ይጾሙ ነበር። በዚህ ቀን ኃጢአታቸውን ይናዘዙ። ሊቀ ካህናቱም የማዕረግ ልብሱን አውልቆ ሌላ ልብስ በመልበስ መጀመሪያ ለራሱና ለካህናት፥ ቀጥሎም ለሕዝቡ መሥዋዕት ያቀርባል። በየዓመቱ በዚህ ቀን ብቻ ደሙን ይዞ ወደ ቅድስተ ቅዱሳን ይገባል። ከዚያም በታቦቱ መክደኛ ላይ ደሙን ይረጫል። ስለዚህም የታቦቱ መክደኛ የስርየት መክደኛ ይባላል። ከዚያ ወጥቶ እጆቹን በሚለቀቀው ፍየል ላይ ጭኖ የእስራኤልን ኃጢአት ያሸክመዋል። ፍየሉም ወደ ምድረ በዳ ተወስዶ ይለቀቃል፤ ዘሌ. 16፤ 23፥26-28፤ ዕብ. 9፥6-14፤ 13፥11:12። የሮም መንግሥት በ70 ዓ.ም. ቤተ መቅደስን ካፈረሰ ወዲህ አይሁድ ይህን በዓል በጸሎትና በጾም ብቻ ያከብሩታል እንጂ መሥዋዕት አያቀርቡም።

**ማስታረቅ**፤ «ዕርቅ» ይመ.

**ማቅ**፤ ከፍየል ወይም ከበግ ጠጕር የሚሠራ ልብስ። ሰዎች ሲያዝኑ (ዘፍ. 37፥34፤ 2ሳሙ. 3፥31)፥ ንስሓም ሲገቡ ማቅ ይለብሳሉ፤ 1ነገ. 20፥27፤ ነህ. 9፥1፤ ማቴ. 11፥21።

**ማቱሳላ**፤ የሄኖክ ልጅ። እርሱም የኖኅን አባት ላሜሕን ወለደ። የሕይወቱ ዘመንም ዘጠኝ መቶ ስድሳ ዘጠኝ ዓመት ነበረ፤ ዘፍ. 5፥22-27።

**ማቴዎስ**፤ ከ12ቱ ሐዋርያት አንዱ ነው። በ4ቱ የሐዋርያት ዝርዝሮች በዚህ ስም ሲታወቅ በማቴዎስ ወንጌል ብቻ «ቀራጩ» የሚል ቅጽል ተጨምሮ ተጠርቷል፤ ማቴ. 10፥3። ማርቆስና ሉቃስ ሌዊ ብለው በቤተሰቡ ስም ይጠሩታል፥ የአባቱ ስም እልፍዮስ መሆኑ ተገልጧል። አስነዋሪ በነበረው የቀራጭነት ሥራ ላይ ሳለ ኢየሱስ ሲጠራው ሁሉን ተወ፤ በቤቱም ለኢየሱስና ለቀድሞ ጓደኞቹ ታላቅ ግብዣ አደረገ፤ ማቴ. 9፥9-13፤ ማር. 2፥13-17፤ ሉቃ. 5፥27-29። ከዚህም በኋላ ኢየሱስ በቤቱ

የተገለገለ ይመስላል፤ ማቴ. 9፥28፤ 13፥1:36፤ 17፥25። የማቴዎስ ቃላት በመ.ቅ. አልተጠቀሱም። ማቴዎስ ቀራጭን እንኳ በሚመርጥ በእግዚአብሔር ጸጋ እየተደነቀ መላ ሕይወቱንና ያለውን ሁሉ ለክርስቶስ አገልግሎት የሰጠ ትሑት ሰው መሆኑ ይታያል።



ቀራጭ ቀረጥ ሲሰበስብ

እንደ ጥንት ቤ.ክ. ትውፊት የመጀመሪያውን ወንጌል የጻፈው ማቴዎስ ነው። ዛሬ አንዳንድ ሊቃውንት ይህን አሳብ ባይቀበሉትም የወንጌሉ አጻጻፍ በጥንቃቄ ከሚጽፍና ከሚሠራ፥ ወደ ወንጌላዊነት ከተለወጠ ቀራጭ አሠራር ጋር ይስማማል። የማቴዎስ ወንጌል የተጻፈባቸው ዘመናት በብዙ ሊቃውንት የተለያዩ እንደሆኑ ቢጠቀስም፥ አንዳንዶች ማቴዎስ ወንጌሉን የጻፈው ከ50 ዓ.ም. በፊት እንደሆነ ሲያመለክቱ፥ ሌሎች ግን ጸሐፊው የማርቆስን ወንጌል ተመልክቶ ኢየሩሳሌም ከወደቀችበት ከ70 ዓ.ም. በኋላ እንዳዘጋጀው ይናገራሉ።

**የማቴዎስ ወንጌል፤** ከመወለዱ ጀምሮ ታላቁን ተልእኮ እስከሚሰጥ ያለውን የክርስቶስን ታሪክ ይተርካል። ይህንም ሲያደርግ ኢየሱስ ስለ መንግሥተ ሰማያት የሰጠውን ትምህርት ከሌሎች ተግባራቱ ጋር በአምስት ታላላቅ ክፍሎች አያይዞ ያቀርባል፤ ም. 5-7፤ 10፤ 13፥1-52፤ 18፤ 24-25። «ማቴዎስ» ይመ.

ይህ ወንጌል ሲነበብ የሚከተሉት ባሕርያት ይታያሉ ፦

1. መጽሐፉ በመጀመሪያ ለአይሁድ የተጻፈ መሆኑ በሚቀጥለው ይታያል ፦ ሀ) በትውልድ ሐረግ የእስራኤል ሕዝብ ታሪክ በሦስት ሲከፈል፥ ኢየሱስ የአብርሃምና የዳዊት ልጅ ነው፥ ለ) የልደቱ ታሪክ በዳዊት ልጅ ሕጋዊ አባት በዮሴፍ በኩል ይተረካል፥ ሐ) ከብ.ኪ. ከ40 የትንቢት ቃላት በላይ ተጠቅሰው መፈጸማቸው ተብራርቶ ይገለጣል፥ መ) ኢየሱስ ከዐሥር ጊዜ በላይ የዳዊት ልጅ መሆኑ ተጠቅሷል፥ ሠ) በአይሁድ መካከል ተሰራጭቶ የነበረውን ሐሰተኛ ወሬ ይከላከላል፤ 28፥11-15።

2. ወንጌል ለዓለም ሁሉ ነው፤ ሀ) ኢየሱስ ሲወለድ አሕዛብ የተወለደበትን ስፍራ ፈልገው በማግኘት አመለኩት፥ ኢየሱስም ከሄሮድስ ሸሽቶ በአሕዛብ ምድር ኖረ፤ ም. 2። ለ) ከአሕዛብ የኢየሱስን በረከት የተቀበሉ ጥቂቶች አልነበሩም፤ 4፥12-16:24-25፤ 15፥21-28። ሐ) እስራኤል በእግዚአብሔር ዕቅድ በሌላ ሕዝብ ይተካል፤ 21፥33-41። መ) ኢየሱስ ሥልጣኑ በምድር ሁሉ እውን ሲሆን፥ ወንጌል ለአሕዛብ ሁሉ እንዲሰበክ አዘዘ፤ 28፥18-20።

3. ማቴዎስ እንደ ማርቆስና እንደ ሉቃስ ሃያ ያህል ተአምራት ሲተርክ ዋናውን ፍሬ ነገር ሳይለቅ በአጭሩ ይመዘግባቸዋል።

4. በዚህ ወንጌል ብቻ ክርስቶስ መንግሥቱን ቤተ ክርስቲያን ብሎ እንደጠራው ይታያል፤ 16፥18፤ 18፥17።

በዚህ ወንጌል ኢየሱስ ሕግንና ነቢያትን የሚፈጽም ጻድቅ፥ አዲስ ኪዳንን የሚሰጥ ሁለተኛ ሙሴ፥ በብ.ኪ. ትንቢት የተነገረለት መሲሕ፥ ለዘለዓለም የሚነግሥ ዳዊት፥ ሰይጣንንና ሞትን የሚያሸንፍ የቤ.ክ. መሥራችና በሰማይና በምድር ሥልጣን ያለው የእግዚአብሔር ልጅ መሆኑ ተገልጧል፤ 5፥17-20፤ 5፥21-22፤ 26፥27-28፤ 22፥21-45፤ 16፥18፤ 28፥18።

የማቴዎስ ወንጌል አከፋፈል እንደሚከተለው ሊሆን ይችላል ፦

መግቢያ፤ የኢየሱስ ልደትና የአገልግሎት ዝግጅት፤ 1፥1-4፥11።

1. የኢየሱስ ስብከትና አገልግሎት አጀማመር፥ ስለ መንግሥቱ አባላት፥ ሀ) ጠባይ፥ ለ) ሕግ አፈጻጸም፥ ሐ) ሃይማኖት፥ መ) ፍርድ የሰጠው ትምህርት፤ 4፥12-7፥29።

2. ኢየሱስ በተአምራቱ ሥልጣኑን ማሳየቱና ስለ መንግሥቱ አገልጋዮች አሠራር የሰጠው ትምህርት፤ 8፥1-10፥42።

3. ኢየሱስ አገልግሎቱን ሲፈጽም ያጋጠመው የፈሪሳውያን ተቃውሞና በምሳሌዎች ስለ መንግሥቱ እድገት የሰጠው ትምህርት፤ 11፥1-13፥52።

4. ኢየሱስ ደቀ መዛሙርቱን ለብቻቸው ማስተማሩና ስለ መንግሥቱ አባላት ኅብረት የሰጠው ትምህርት፤ 13፥53-18፥35።

5. ኢየሱስ ገሊላን ለቆ ወደ ኢየሩሳሌም መውጣቱና ስለ መንግሥቱ መምጣት ያስተማረው ትምህርት፤ 19፥1-25፥46።

6. የኢየሱስ አገልግሎት ፍጻሜ፤ ኢየሱስ ለደቀ መዛሙርቱ የተናገራቸው የመጨረሻ ቃላት፥ መያዙ፥ ሕማማቱና ትንሣኤው፤ 26፥1-28፥15።

መደምደሚያ፤ የታላቁ ተልእኮ አደራ፤ 28፥16-20።

**ማትረፊያ፤** ጥቅም፥ ዋጋና ክብር ማግኛ ተብሎ ሊተረጐም ይችላል፤ 1ጢሞ. 6፥4-6። አሳቡ በ1ጢሞ. 4፥7:8 ላይ በግልጥ ተብራርቷል።

**ማኅበር፤** ሕዝብ በአንድነት ሲተባበር ማኅበር ይባላል። ብዙ ጊዜ የእስራኤል ሕዝብ በጠቅላላው ማኅበር ይባላሉ፤ ዘጸ. 35፥1፤ ዘሌ. 4፥13፤ ዘኍ. 10፥2። በአ.ኪ. የእግዚአብሔር ማኅበር ቤተ ክርስቲያን በሚለው ቃል ተተርጒሟል። ይህም ስያሜ በሰማይ ላለው የቅዱሳን አንድነት መጠሪያ ሆኖ ተጠቅሷል፤ ዕብ. 12፥23።

**ማኅተም፥ ማተሚያ፤** ከወርቅ፥ ከብር፥ ከከበረ ማዕድን ወይም ከተራ ማዕድን የሚቀረጽ፥ የእንስሳ የሌላም መልክ፥ የሰው ስምና ማዕረግ የሚገኝበት። ሰዎች በአንገታቸው ያንጠለጥሉት ወይም በቀለበት መልክ አድርገው በጣታቸው ይይዙት ነበር፤ ሐጌ 2፥23። ነገሩን ለማረጋገጥ ማኅተማቸውን በሰም፥ በጭቃ፥ በሸክላ በሌላም ያትማሉ። ማኅተም ሥልጣንን (ዘፍ. 41፥42)፥ ባለቤትነትን ሊያረጋግጥ ይችላል፤ ኤር. 32፥10-14። በንጉሥ ወይም በሌላ ከፍተኛ ባለሥልጣን ማኅተም የታተመ አይለወጥም፤ አስ. 8፥8፤ ዳን. 6፥17፤ ማቴ. 27፥66። እግዚአብሔር ከዓለም ለይቶ የቃል ኪዳኑ ተካፋይ ያደረጋቸው ሕዝቡ በሚታይ ምልክት፥ ይኸውም በብ.ኪ. በግዝረት በአ.ኪ. በጥምቀት የሥላሴን ስም በላያቸው በማድረግ እንዲታተሙ አዟል፤ ዘፍ. 17፥7:10፤ ሮም 4፥11፤ ማቴ. 28፥19። የሚታየው ማኅተም ለማይታየውና ለዋናው ማኅተም፥ ማለትም በመንፈስ ቅዱስ ለመታተም ምልክት ነው፤ 2ቆሮ. 1፥22፤ ኤፌ. 1፥13፤ 4፥30። ማኅተም የእግዚአብሔር ወገኖች መሆናቸውንና ለዘለዓለም መዳናቸውን ያረጋግጥላቸዋል።



በ1400 ዓመት ከክ.በ. የተቀረጸ፥ የከነዓን ክብ ማኅተምና እትሙ

«የታተመ መጽሐፍ» ወይም «ራእይ» ሲል ገና ያልተገለጠ ምሥጢር ማለት ነው፤ ኢሳ. 29፥11፤ ዳን. 12፥9፤ ራእ. 5፥1። ጊዜው ሲደርስ ግን ትንቢቱ በማኅተም አይዘጋም፤ ራእ. 22፥10። በአ.ኪ. በምሳሌነት ማኅተም ለእምነት፥ ለልጅነት ለሌላም ማረጋገጫ ተነግሯል፤ ዮሐ. 3፥33፤ 6፥27፤ ሮም 15፥28፤ ራእ. 7፥2-8።

**ማኅፀን፤** በሴት ሆድ ውስጥ ጽንስ እስኪወለድ ድረስ የሚያድግበት የአካል ክፍል። በብ.ኪ. ዘመን ሴት ለመፅነስ ባትችል፥ ከእግዚአብሔር እንደመጣና ለሐዘን እንደ ትልቅ ምክንያት ሲቈጠር፥ እግዚአብሔር ማኅፀንዋን ሲከፍት ግን ትልቅ ደስታን ይፈጥር ነበረ፤ ዘፍ. 20፥17-18፤ 29፥31-32፤ 30፥22-24፤ 1ሳሙ. 1፥5-6፤ ሉቃ. 1፥7:13:14:58።

**ማኑሄ፤** የሶምሶን አባት። የስሙ ትርጒም «ዕረፍት» ማለት ነው፤ መሳ. 13፥2-25፤ 14፥3:4:5:10፤ 16፥31።

**ማንኰራፋት፤** በሰርን ወይም በአፍንጫ መጮኽ። ቃሉ ለፈረስ ይጠቀማል፤ ኢዮብ 39፥20።

**ማኸላት፤** ማኸላት የዕብራይስጥ ቃል ነው (መዝ. 53 እና 88 ርእስ)፥ ትርጓሜው ተረስቷል፥ ሆኖም መዝሙሮች የተዘመሩበትን የዜማ ስልት ያመለክት ይሆናል።

**ማዋቀሪያ፤** የጣራ ዋልታ መጋጠሚያ ወይም መጀመሪያ፤ መ.መ. 1፥17።

**የማዕዘን ድንጋይ፤** በሕንጻ ክፍል ሁለት ግድግዳዎች የሚገናኙበት «የማዕዘን ድንጋይ» ይባላል። ግንበኛ የማዕዘኑን ድንጋይ በጥንቃቄ ያኖረዋል። ግድግዳውም በዚያው ልክ ይሠራል። የማዕዘን ራስ ድንጋይ የሚለው በመሠረቱ ወይም በማዕዘኑ ላይ ያለው ዋና ድንጋይ ነው። በዚህ አንፃር ክርስቶስ የቤ.ክ. የማዕዘን ራስ ድንጋይ ተብሏል፤ መዝ. 118:22፤ ማቴ. 21፥42፤ ኤፌ. 2፥20፤ 1ጴጥ. 2፥5-7።

**ማዕድኖች፤** በብ.ኪ. ዘመን በማዕድን የመጠቀም ዕውቀት ተጀምሮ ነበር። ልዩ ልዩ ብረታ ብረትና ድንጋይ ከመሬት ተቈፍሮ ይወጣ ነበር፤ ዘኍ. 31፥22፤ ዘዳ. 8፥9፤ ኢዮብ 28፥1-11።

1. ብረታ ብረት። ብረት (ዘፍ. 4፥22)፥ ብር (ዘፍ. 13፥2)፥ ቆርቆሮ (ኢሳ. 1፥25)፥ ናስ (ዕዝ. 8፥27)፥ እርሳስ ወይም ዐረር (ዘካ. 5፥7፤ ዘጸ. 15፥10)፥ ወርቅ፤ ዘፍ. 2፥11።

2. ድንጋዮች። ቡላድ (ሕዝ. 3፥9)፥ ባልጩት ድንጋይ (ኢሳ. 50፥7)፥ አልባስጥሮስ (ማቴ. 26፥7)፥ ዕብነ በረድ (አስ. 1፥6) ጭንጫ ድንጋይ፤ ዘዳ. 8፥15።

3. ከመሬት የተገኘ ሌላ ዓይነት። አሸዋ (ዘዳ. 33፥19)፥ ቅጥራን (ዘፍ. 6፥14)፥ ዝፍት (ዘፍ. 14፥10)፥ ዲን (ዘፍ. 19፥24)፥ ጨው፤ 2ሳሙ. 8፥13። «የከበሩ ድንጋዮች» ይመ.

**ማዕድ፤** የምግብ ጠረጴዛ፤ 1ነገ. 2፥7። ማዕድን ማገልገል ማለት ለድሆች እርዳታን ማካፈል ማለት ነው፤ ሐ.ሥ. 6፥2። ቅዱስ ቍርባን የሚሰናዳበት የጌታ ማዕድ ይባላል፤ 1ቆሮ. 10፥21። «ገበታ» ይመ.

**ማዕጠንት፤** የዕጣን ማጠኛ፤ ዕብ. 9፥4። «ጥና»፥ «የዕጣን መሠዊያ» ይመ.

**ማዘቢያ፤** የጫማ ማሰሪያ ጠፍር ወይም ሌላ ዓይነት ገመድ፤ ኢሳ. 5፥27፤ ሉቃ. 3፥16።

**ማዛሮት**፤ የከዋክብት ስም የትኞቹ እንደሆኑ አይታወቅም፥ አንዳንድ ሰዎች ጠንቋዮች የሚጠነቍሉባቸው ዐሥራ ሁለት ከዋክብት ናቸው ይላሉ፤ ኢዮብ 38፥32።

**ማደሪያ**፤ በጥንት ዘመን እንግዳ ተቀባይነት የተለመደ እንደ መሆኑ መጠን ሰዎች መንገደኞችን በቤታቸው ተቀብለው ያሳድሩ ነበር፤ ዘጸ. 2፥20፤ ሐ.ሥ. 28፥7። ሆኖም ነጋዴዎች በሚመላለሱባቸው መንገዶች ሰውንና እንስሳትን የሚያሳድሩ ማደሪያዎች ይሠሩ ነበር፤ ኤር. 14፥8፤ ሉቃ. 10፥34:35። «የእግዚአብሔር ማደሪያ» ይመ.

**ማጀት**፤ በቤት ውስጥ የሚሠራ ክፍል (ጓዳ)። የመቃብር ምሳሌ ነው፤ ምሳ. 7፥27።

**ማጎግ**፤ 1. የያፌት ልጅ፤ ዘፍ. 10፥2። 2. ከያፌት ልጅ የተገኘ ወገን ወይም አገር። ማጎግ ከእስራኤል በስተሰሜን የኖሩ ሕዝቦች ከመሆናቸው በቀር ዛሬ እነማን እንደሆኑ ለማወቅ አይቻልም። በሕዝቅኤል አስተሳሰብ ግን በታወቀው ዓለም ዳርቻ የኖሩ ሕዝቦች ነበሩ። በትንቢቱ ቃል መሠረት በእግዚአብሔር ሕዝብ ላይ ለሚነሡ ምሳሌ ናቸው። የእግዚአብሔርን ሕዝብ ለማጥፋት ይሞክራሉ። እግዚአብሔር ግን ያጠፋቸዋል፤ ሕዝ. 38፤ 39፤ ራእ. 20፥8።

**ማጠፊያ**፤ ከወርቅ፥ ከብርና ከሌላም የሚሠራ ሳንቃ የሚዞርበት፤ 1ነገ. 7፥50። የሰነፍ ሰው ጠባይ ተገልጦበታል፤ ምሳ. 26፥14።

**ማጨብጨብ**፤ በሚገባ ወይም በማይገባ ጉዳይ ላይ እጅና እጅን በማገናኘት ደስታን መግለጥ፤ 2ነገ. 11፥12፤ ኢዮብ 34፥37፤ መዝ. 47፥1፤ 98፥8፤ ሕዝ. 25፥6፤ ናሆም 3፥17።

**ማጫ**፤ ወንድ በጋብቻ ጊዜ ለሴት ወይም ለሴቲቱ ወላጆች የሚሰጠው ስጦታ፤ ዘፍ. 34፥12። ወንድ ያልታጨች ልጃገረድ ቢደፍር ሊያገባትም ባይፈልግ ሙሉ ማጫ ይሰጥ ነበር፤ ዘጸ. 22፥16:19። «አጨ» ይመ.

**ሜልኮል**፤ የዳዊት ሚስት፥ ከሳኦል ሴቶች ልጆች ታናሺቱ። ዳዊትንም ወደደች፥ ሳኦል ለእርሱ መዳሩ ግን ወጥመድ እንድትሆነው ነበር፤ 1ሳሙ. 14፥49፤ 18፥20-28። ዳዊት ከሳኦል ሸሽቶ እንዲያመልጥ ረዳችው፤ 1ሳሙ. 19፥11-17። ዳዊት በተሰደደ ጊዜ ፈልጢ ለሚባል ሰው ተሰጠች፤ 1ሳሙ. 25፥44። ዳዊት ከነገሠ በኋላ እንደገና አስመጣት (2ሳሙ. 3፥13-16)፥ በእግዚአብሔርም ፊት በዘፈነ ጊዜ ናቀችው፥ ከዚህ የተነሣ ሳትወልድ ቀረች፤ 2ሳሙ. 6፥16-23።

**ሜምፊቦስቴ**፤ 1. የዮናታን ልጅ፥ የንጉሥ ሳኦል የልጅ ልጅ። በልጅነቱ ወድቆ አንካሳ ሆነ። ዳዊት ስለ ዮናታን ብሎ በቤቱ መንግሥቱ ተቀብሎ አከበረው፥ የሳኦልን ርስት መለሰለት፤ 2ሳሙ. 4፥4፤ 9፥1-13። ባሪያው ሲባ እርሱን ለዳዊት በማማት በደለው፤ 2ሳሙ. 16፥1-4፤ 19፥24-30። አንዳንዴ መሪበአል ይባላል፤ 1ዜ.መ. 8፥34፤ 9፥40። 2. ሪጽፋ ለሳኦል ከወለደቻቸው ሁለት ልጆች አንዱ ነበረ፤ 2ሳሙ. 21፥1-14፤ በተለይ ቍ. 8።

**ሜምፎስ**፤ በብ.ኪ. ዘመን የግብጽ መናገሻ ከተማ። ናቡከደነፆር ኢየሩሳሌምን ካፈረሰ በኋላ አያሌዎቹ አይሁድ ወደ ሜምፎስ ተጓዙ፤ ኤር. 44፥1። ነቢያት ሜምፎስ እንደሚጠፉ ተናገሩ፤ ኢሳ. 19፥13-15፤ ኤር. 46፥14:19። ሜምፎስ ከነበረበት ሠላሳ ኪ.ሜ. ርቆ ካይሮ ይገኛል። ካ. 2. ሰ።

**ሜራሪ**፤ ከሌዊ ሦስት ልጆች ታናሹ፤ ዘፍ. 46፥11። እስራኤላውያን በምድረ በዳ ሲጓዙ የሜራሪ ወገን የመገናኛውን ድንኳን ሳንቆችና ምሰሶች ይሸከሙ ነበር፤ ዘኍ. 3፥33-37፤ 7፥8። ዳዊት ታቦቱን ወደ ጽዮን ሲያወጣ ያገለግሉ ነበር፤ 1ዜ.መ. 15፥6።

**ሜሮብ**፤ ከሳኦል ሴቶች ልጆች ታላቂቱ፤ 1ሳሙ. 14፥49። ሳኦል ለዳዊት ሊድራት ተስፋ ከሰጠ በኋላ ለሌላ ሰው ሰጣት፤ 1ሳሙ. 18፥17-19። የወለደቻቸው አምስት ልጆች ተሰቀሉ፤ 2ሳሙ. 21፥1-9፥ በተለይ ቍ. 8።

**ሜሮዳክ**፤ የአማልክት ንጉሥ የተባለ የባቢሎን ዋና አምላክ፤ ኤር. 50፥2።



በ950 ዓመት ገደማ ከክ.በ. ከድንጋይ የተቀረጸ የሜሮዳክ ምስል

**ሜንጦ**፤ እንደ ትልቅ ሹካ ጣት ያለው ከድስት ውስጥ ሥጋ የሚወጣበት መጫሪያ፤ ዘጸ. 27፥3፤ 1ሳሙ. 2፥13:14።

**የሜዳ አህያ፤** «እንስሳት» ይመ.

**ሜዶን፤** ሜዶናውያን፤ ከነነዌ በስተምሥራቅ የነበረ አገርና ሕዝብ። ሜዶን መጀመሪያ በመ.ቅ. ሲጠቀስ በአሦር መንግሥት ውስጥ ነበረ፤ 2ነገ. 17፥6። ነገር ግን አሦር በደከመች ጊዜ ሜዶን ነፃነትን ለአጭር ጊዜ አገኘ፥ ኃይለኛ ሕዝብም ሆነ፤ ኢሳ. 13፥17። በኋላ በፋርስ ንጉሥ በቂሮስ ተሸንፈና ከፋርስ መንግሥት ጋር ሕጋቸውና ባህላቸው አንድ እስኪሆን ድረስ ተባበሩ፤ ዳን. 6፥8:15። ከሜዶን ዘር የነበረው ዳርዮስ በባቢሎን ንጉሥ ሆነ፤ ዳን. 5፥30-6፥28።



በ500 ዓመት ገደማ ከክ. ል. የተቀረጸ የአንድ ሜዶናዊ ቅርጽ

**ምልክት፤** የማይታየውን ነገር የሚገልጥና የሚያረጋግጥ። 1. ተአምራት፥ ጌታ ይፈጽማቸው የነበሩት ተአምራት ምልክት ተብለዋል፤ ዮሐ. 2፥11፤ 6፥14:26-27። የመንፈሳዊ ሕይወት እንጀራ መሆኑን ለመግለጥ እንጀራን አበዛ፤ ዮሐ. 6፥14:26-27። የዓለም ብርሃን መሆኑን ለመግለጥ ዕውሩን አበራ፤ ዮሐ. 9፥5-7። 2. የእግዚአብሔር የተስፋ ቃል ምልክት ፦ ቀስተ ደመና፤ ዘፍ. 9፥12። ግዝረት፤ ሮም 4፥11። 3. የእግዚአብሔርን የተስፋ ቃል የሚጠቁምና የሚያረጋግጥ፤ ኢሳ. 7፥14።

**ምልጃ፥ አማለደ፤** መሠረታዊ ትርጉሙ አንዱ ስለ ሌላው መለመን። እነሙሴ በምድር ላይ ሳሉ ስለ እስራኤል ማለዱ፤ ጸሎታቸውም ተሰማ፤ ዘኍ. 14፥19-20። ክርስቶስ ለደቀ መዛሙርቱ ለመነ፤ ሉቃ. 22፥32፤ ዕብ. 5፥7-10። ምእመናን ለሌሎች እንዲለምኑ ታዝዘዋል፤ ፊል. 4፥6፤ 1ጢሞ. 2፥1-2። ክርስቶስ «... ሊያማልድ ዘወትር በሕይወት ይኖራልና ... በእርሱ ወደ እግዚአብሔር የሚመጡትን ፈጽሞ ሊያድናቸው ይችላል።» የእርሱ ምልጃ ግን እንደ እኛ ልመና አይደለም፤ ምክንያቱም፥ ሀ) አንድ ጊዜ ራሱን መሥዋዕት አድርጎ በማቅረቡ ለምእመናን ፍጹም ደኅንነት አስገኝቶላቸዋል፥ ለ) ለዘለዓለም ሕያው ሆኖ በሰማይና በምድር ሥልጣንን ሁሉ በመቀበል በአብ ቀኝ ተቀምጧል፤ ሮም 8፥34፤ ዕብ. 7፥25፤ 1ዮሐ. 2፥1። መንፈስ ቅዱስ ደግሞ ለምእመናን ያማልዳል፥ ይህም ለድካማቸው ኃይልን ይሰጣል ማለት ነው፤ ሮም 8፥26። «ማለደ» ይመ.

**ምሕረት፤** የእግዚአብሔር የርኅራኄ ባሕርይ። ቅጣት ለሚገባው የሚሰጥ ይቅርታ (መዝ. 51፤ 130፥7:8)፤ ለደካሞች፥ ለበሽተኞች፥ ለድሆችም ቸርነትና እርዳታን ማድረግ ነው፤ ምሳ. 14፥21:31፤ ሆሴዕ 14፥3፤ ሮም 5፥6፤ ማር. 10፥46-52። እግዚአብሔር ከምሕረቱ የተነሣ ስለ እኛ ሲል በመስቀል ላይ እንዲሞት አንድ ልጁን ሰጠ፤ ኤፌ. 2፥4:5፤ 1ጴጥ. 1፥3። ምእመናን ምሕረት እንዲያደርጉ ታዝዘዋል፤ ያዕ. 2፥1-13፤ ሉቃ. 6፥36፤ ማቴ. 5፥7፤ ሮም 12፥19። እግዚአብሔር ከማናቸውም ነገር ሁሉ ይልቅ ምሕረትን ይወዳል፤ ሆሴዕ 6፥6፤ ሚክ. 6፥8፤ ማቴ. 12፥7። «መሐሪ»፥ «ማረ» ይመ.

**ምሥራቅ፤** ፀሐይ ጧት የምትታይበት አቅጣጫ። በብ.ኪ. ዋናው የቤተ መቅደስ በር በምሥራቅ ነበር፤ እግዚአብሔር በምሥራቅ በኩል ራሱን ለሕዝቅኤል በራእይ ገለጠ፤ ዘኍ. 3፥38፤ ሕዝ. 10፥19፤ 11፥23፤ 43፥2:4። የምሥራቅ ሰዎች ሲባል ከእስራኤል አገር በስተምሥራቅ አቅጣጫ የሚኖሩ ሰዎች ማለት ነው፤ ኢዮብ 1፥3፤ ማቴ. 2፥1-2። ምሥራቅ ከምዕራብ እንደሚርቅ ማለት በፍጹም የራቀና የተለየ ማለት ነው፤ መዝ. 103፥12።

**የምሥራቅ ነፋስ፤** በግብጽ፥ በእስራኤልም በኩል የሚነፍስ የሞቀ ነፋስ። ከምድረ በዳ ስለሚነፍስ ሁሉን ያደርቃል፤ ዘፍ. 41፥6፤ ሕዝ. 17፥10። በምሳሌነት ስለ እግዚአብሔር ፍርድ ይናገራል፤ ኢሳ. 27፥8፤ ኤር. 18፥17።

**ምሥጢር፤** በሰዎች ምርመራ ሳይሆን በእግዚአብሔር አንዳንድ ጊዜም በሰው ሊገለጥ የሚችል። ለሰዎች ያልተገለጠ በእግዚአብሔር ዘንድ ታውቆ ያለ ምሥጢር ይባላል፤ ዘዳ. 29፥29። አንዳንድ ጊዜ በአ.ኪ. ምሥጢር ማለት የምሳሌ ወይም የቃል ትርጉም ማለት ነው፤ ማቴ. 13፥11-13፤ 1ቆሮ. 2፥7፤ ራእ. 1፥20፤ 17፥5:7፤ ኤፌ. 5፥32። ለተመረጡት የምሥጢር መክፈቻ ተሰጣቸው፤ ማር. 4፥11።

አብዛኛውን ጊዜ ምሥጢር ሲባል ለብዙ ዘመናት ተሰውሮ የኖረ አሁን ግን በወንጌል የተገለጠ ከእግዚአብሔር የወጣ የእውነት ቃል ትምህርት ማለት ነው፤ ሮም 16፥25:26፤ 1ቆሮ. 15፥51:52፤ ቆላ. 1፥26፤ 2ተሰ. 2፥7። የወንጌል ምሥጢር እግዚአብሔር በክርስቶስ በኩል ደኅንነትን ለዓለም ሁሉ ማቅረቡ ነው፤ ኤፌ. 1፥9፤ 3፥3-6፤ 6፥19፤ ቆላ. 4፥3:4፤ 1ጢሞ. 3፥16።

**ምሬት**፤ «መራ» ይመ.

**ምራት**፤ የልጅ ሚስት። የልጅ ሚስት ምራት የምትባለው ለባልዋ አባትና እናት ብቻ ነው። ለሌሎች ግን ለምሳሌ ለባልዋ ወንድሞች ዋርሳ፥ ለእኅቶቹ አይት ትባላለች። ከምራት መድረስ ተከልክሏል፤ ዘሌ. 18፥15። ይሁዳ ከምራቱ ልጆችን ወለደ፤ ዘፍ. 38፥12-30። ክርስቶስን በማመንና ባለማመን ምክንያት ዐማትና ምራት እንደሚለያዩ ራሱ ክርስቶስ ተናገረ፤ ሉቃ. 12፥53።

**ምርኮ**፤ በጦርነት አንደኛው ወገን ሲያሸንፍ የሚወስደው ሀብት፥ እንስሳ ሰው ... ወዘተ፤ ዘዳ. 20፥14-18። አብርሃም ከምርኮው ዐሥራት ሰጠ፤ ዘፍ. 14፥20። ዳዊት ወደ ጦርነት የሄዱ ከጓዝ ጠባቂዎች ጋር ምርኮውን በአንድነት እንዲካፈሉ አዘዘ፤ 1ሳሙ. 30፥21-25። ክርስቶስ አብረውት ድል ከሚነሡ ጋር ምርኮን ይካፈላል፤ ኢሳ. 53፥12። «እርም» ይመ.

**ምርጫ**፤ ሰውም የራሱ ፈቃድ ስለሚኖረው እንደ ተፈጥሮው፥ ጠባዩና ሁኔታው ትልቅ ወይም ትንሽ ነገርን መርጦ መኖር ይችላል፤ ዘፍ. 6፥2፤ 13፥11፤ ሉቃ. 6፥13፤ 10፥42፤ 14፥7፤ ሐ.ሥ. 6፥5። «ነፃ ፈቃድ»፥ «እግዚአብሔር 6» ይመ.

**ምሳሌ**፤ አንድን ነገር ግልጥ ለማድረግ ሲፈለግ የሚቀርብ ማስረጃ፥ ማብራሪያና መግለጫ። ምሳሌ ነገር እንዳይረሳ ያደርጋል፥ በይበልጥም ያብራራል፥ ሰው እንዲያስብበት ይቀሰቅሳል። ከዘፍ. 10፥9 ጀምሮ ብዙ ምሳሌዎች ይገኛሉ። ሰሎሞን ብዙ ምሳሌዎችን ተናግሯል፤ 1ነገ. 4፥32:33። ከሁሉም በላይ ክርስቶስ አብዛኛውን ጊዜ በምሳሌ አስተማረ፤ ማቴ. 13፥35። ምሳሌዎቹም የታወቁ ናቸው፤ ማር. 4፥33:34። ምሳሌ አስተዋይን ብልህ ያደርጋል፥ የማያስተውልን ግን በድንቁርና ያጨልማል፤ ማር. 4፥10-12።

ምሳሌን ለመተርጐም ጥንቃቄ ያስፈልጋል። በተለይ ሦስት ዓይነት ምሳሌዎች አሉ፥ እንደየዓይነታቸው ይተረጐማሉ። (ሀ) እንደ ተረት ያለ አጭር ምሳሌ፥ ለምሳሌ ያህል ኢየሱስ «መልካም እረኛ እኔ ነኝ» ሲል እረኛ በጎቹን እንደሚጠብቅ ተከታዮቹን ይጠብቃል ማለት ነው። (ለ) ብዙ ድርጊት የሚገኝበት፥ ለድርጊቱም ትርጕም የሚሰጥ ምሳሌ፥ ለምሳሌ ያህል የዘሪው ምሳሌ ይህን ያሳያል፥ እያንዳንዱ ቃል ትርጕም አለው፤ ማቴ. 13፥3-9;18-23። (ሐ) ብዙ ድርጊትና አሳብ የሚገኝበት ለየድርጊቱና ለየአሳቡ ትርጕም የማይሰጥ ምሳሌ፤ ይህን ለመተርጐም ምሳሌው የተነገረበትን ምክንያት ማስተዋል ያስፈልጋል። የርኅሩኁን ሳምራዊ ምሳሌ ይመ. (ሉቃ. 10፥25-37)። ለስም የተጠቀሱ ቃላት ወይን፥ ዘይት፥ አህያ፥ ዲናር ... ወዘተ. የምንና የምን ምሳሌዎች ናቸው ብለን ብንጠይቅ የፈለግነውን ምሥጢር ልናገኝባቸው እንችላለን። ክርስቶስ ምሳሌውን የተናገረው የሕግ አዋቂውን ጥያቄ ለመመለስ ነው። እንግዲህ ይህ ታሪክ የሰው ባልንጀራ ማን እንደሆነ ያሳያል። ወይን ዘይት ... ወዘተ. የሰውዬውን ችግርነት ያሳያሉ እንጂ ለእያንዳንዳቸው ልዩ ትርጕም አይኖራቸውም።

**ምሳሌ**፤ የኢየሱስ ክርስቶስ ምሳሌዎች፤ ካስተማረባቸው መካከል ዋናዎቹ በገጽ 58 ሰንጠረዥ ላይ ይታያሉ።

**ምሳሌ፥ መጽሐፈ ምሳሌ**፤ ከጥንት ጀምሮ የያገሩ መምህራን ትምህርታቸውን በምሳሌዎች አማካይነት ሲያስተምሩ ቆይተዋል፥ በዚህ መጽሐፍ ውስጥ ጥበበኛው ሰሎሞን እግዚአብሔርን የሚፈራ ሰው እንዴት መኖር እንደሚገባው ያስተምራል። ምሳሌዎቹ የሰውን ሕይወት በየክፍሉ እየነኩ ተገቢውን አካሄድ ያመለክታሉ፤ ዋና ትምህርታቸውም እንዲህ የሚል ነው :- «ጥበብ ከእግዚአብሔር ጋር በመተባበር ዕውቀትንና ማስተዋልን አግኝቶ በሥራ ላይ ማዋል ነው።»

ይሁን እንጂ ምሳሌዎቹ ሁሉ የሰሎሞን አይደሉም። የ«ጠቢባን»፥ የአጉር፥ የልሙኤልም አሉ፤ 22፥17፤ 24፥23፤ 30፥1፤ 31፥1። ከምዕራፍ 1 አንሥቶ እስከ 9 መጨረሻ ድረስ ምክር ሰጪዋ ራስዋ ጥበብ ናት። በጐዳና ትጮኻለች፥ ከከተማይቱ ከፍተኛ ስፍራ ላይ ትጠራለች (1፥20፤ 8፥1-3፤ 9፥1-3)፥ ቢሆንም የምትሰጠው ትምህርት የሰሎሞንን ነው። ቀጥሎ ከ10-22፥ 16 እና ከ25-29፥ ራሱ ሰሎሞን የፈጠራቸው ምሳሌዎች ናቸው። ከእግዚአብሔር ዘንድ ልዩ ጥበብን እንደ ተቀበለና ሦስት ሺህ ምሳሌዎችን እንደ ተናገረ ታውቋል፤ 1ነገ. 3፥10-12፤ 4፥29-34። ከእነዚህ ምሳሌዎች ብዙዎቹ በዚህ መጽሐፍ ተጠቃለዋል፥ የይሁዳ ንጉሥ የሕዝቅያስ ሰዎች ሌሎችን ሰብስበዋል (25፥1)፤ እነዚህም በመጽሐፈ ምሳሌ በመጨረሻዎቹ 7 ምዕራፎች ያሉት ናቸው (25-31)፤ በግዕዝ «መጽሐፈ ተግሣጽ» ተብለዋል።

መጽሐፉስ መቼ ተጻፈ? ቢባል ምናልባት ሰሎሞን በዘመነ መንግሥቱ ማለትም በ950 ከክ.በ. ጀምሮት ይሆናል፥ የሕዝቅያስም ሰዎች 700 ከክ.በ. ሌሎችን ጨምረዋል፥ አይሁድ 450 ከክ.በ. ከምርኮው ሲመለሱ መጽሐፉን አጠናቀው ሳይጽፉት አልቀሩም።

መጽሐፉ የተጻፈው በግጥም መልክ ነው፤ ምክንያቱም በግጥም የተሰጠ ትምህርት በልብ ስለሚያዝ ነው።

ምሳሌዎቹ ራሳቸውን የቻሉ ናቸውና እያንዳንዱ እየተነበበ ለብቻው ይታሰብበታል እንጂ፥ የተያያዘ ታሪክ እንደሚነበብ ዓይነት ምሳሌዎቹ አይነበቡም። ይሁን እንጂ በዓይነት በዓይነቱ በአንድ ክፍል ውስጥ ተጠቃልሏልና እያንዳንዱን ምሳሌ ከተመሳሳዩ ክፍል ጋር ማንበብ ይገባል።

ክርስቶስ፥ ጴጥሮስና ጳውሎስ፥ ያዕቆብም መጽሐፈ ምሳሌን ጠቅሰውታል፤ ሉቃ. 14፥8-10 ከምሳ. 25፥6:7 ጋር፥ 1ጴጥ. 4፥18 ከምሳ. 11፥31 ጋር፥ 2ጴጥ. 2፥22 ከምሳ. 26፥11 ጋር፥ ሮም 12፥20 ከምሳ. 25፥21:22 ጋር፥ ያዕ. 4፥6 ከምሳ. 3፥34 ጋር አነጻጽሩ።

| የኢየሱስ ምሳሌዎች | ማቴዎስ | ማርቆስ | ሉቃስ |
|---|---|---|---|
| ከዕንቅብ በታች ያለ መብራት | 5÷14-15 | 4÷21-22 | 8÷16፤11÷33 |
| ልባምና ሰነፍ አናጺዎች | 7÷24-27 | | 6÷47-49 |
| በአረጀ ልብስ ላይ አዲስ እራፊ | 9÷16 | 2÷21 | 5÷36 |
| በአረጀ አቁማዳ አዲስ ወይን | 9÷17 | 2÷22 | 5÷37-38 |
| ዘሪና የመሬት ዓይነቶች | 13÷3-8:18-23 | 4÷3-8:14-20 | 8÷5-8:11-15 |
| ስንዴና እንክርዳድ | 13÷24-30:36-43 | | |
| የሰናፍጭ ቅንጣት | 13÷31-32 | 4÷30-32 | 13÷18-19 |
| የተሸሸገ እርሾ | 13÷33 | | 13÷20-21 |
| የተሰወረ ሀብት | 13÷44 | | |
| መልካም ዕንቍ | 13÷45-46 | | |
| በባሕር ላይ የተጣለ መረብ | 13÷47-50 | | |
| የቤት ባለቤት | 13÷52 | | |
| የጠፋ በግ | 18÷12-14 | | 15÷4-7 |
| ምሕረት የማያደርግ ባሪያ | 18÷23-34 | | |
| የወይን አትክልት ሠራተኞች | 20÷1-16 | | |
| ሁለት ልጆች | 21÷28-32 | | |
| የወይን አትክልት ተከራዮች | 21÷33-44 | 12÷1-11 | 20÷9-18 |
| የሰርግ ግብዣ | 22÷2-14 | | |
| የበለስ ዛፍ ምልክቶች | 24÷32-35 | 13÷28-31 | 21÷29-31 |
| ታማኝና ልባም ባሪያዎች | 24÷45-51 | | 12÷42-48 |
| ዐሥር ቈንጃጅት | 25÷1-13 | | |
| ለሦስት ባሪያዎች የተሰጡ መክሊቶች | 25÷14-30 | | |
| በጎችና ፍየሎች | 25÷31-46 | | |
| የሚያድግ ዘር | | 4÷26-29 | |
| ጌታቸውን የሚጠባበቁ ባሪያዎች | | 13÷33-37 | 12÷35-40 |
| አበዳሪና ተበዳሪዎች | | | 7÷41-43 |
| ደጉ ሳምራዊ | | | 10÷30-37 |
| ሦስት ወዳጆች | | | 11÷5-8 |
| ሞኝ ሀብታም | | | 12÷16-21 |
| የማታፈራ የበለስ ዛፍ | | | 13÷6-9 |
| የግብዣ ስፍራ | | | 14÷7-14 |
| ትልቁ ግብዣ | | | 14÷16-24 |
| የጠፋ ድሪም | | | 15÷8-10 |
| የጠፋ ልጅ | | | 15÷11-32 |
| ልባም መጋቢ | | | 16÷1-8 |
| ሀብታሙና አልዓዛር | | | 16÷19-31 |
| አሠሪ ጌታና ባሪያ | | | 17÷7-10 |
| ነዝናዣ መበለት | | | 18÷2-8 |
| ፈሪሳዊውና ቀራጩ | | | 18÷10-14 |
| ለዐሥር ባሪያዎች የተሰጡ ምናኖች | | | 19÷12-27 |

**ምስል፤** ከእንጨት ወይም ከድንጋይ የተቀረጸ፥ ወይም ከናስና ከብር፥ ከወርቅም ከሌላም በማቅለጫ የተቀረጸ፥ አረማውያን አማልክታቸውን የሚያመልኩበት፥ እስራኤል ምስልን ቀርጸው እንዳያመልኩ ተከልክለዋል። ምክንያቱም እግዚአብሔርን በተፈጠረ ነገር መመስል አይቻልምና ነው፤ ዘጸ. 20:4-6፤ 34፥17፤ ዘዳ. 4፥15-19፤ ኢሳ. 40፥18። እስራኤል ከእግዚአብሔር ሲርቁ ምስሎችን ሠሩና በምስሉ አማካይነት ሊያመልኩት ሞከሩ፤ ዘጸ. 32፥1-6፤ 1ነገ. 12፥26-29፤ 14፥9። አረማውያን በየአገራቸው ብዙ ዓይነት ምስል ይሠሩ ነበር፤ ኢሳ. 30፥22፤ 40፥20፤ ዳን. 3፥1፤ ሐ.ሥ. 19፥24። «ጣዖት» ይመ.

**ምስክር፤** 1. ቃል ኪዳን፥ ምልክት፥ መዝሙር ሌላም ምስክር ወይም መታሰቢያ ሊሆን ይችላል፤ ዘፍ. 31፥44፤ ዘዳ. 31፥19-21:26፤ ኢያሱ 24፥27:28፤ ኢሳ. 19፥19:20።

2. ሰው እውነተኛ ምስክር መሆን አለበት። ክስ በሁለት ወይም በሦስት ምስክሮች ይጸናል። ሐሰተኛ ምስክር በሌላው እንዳሰበ በራሱ ይደረግበታል፤ ዘዳ. 5፥20፤ 19፥15-21፤ 1ጢሞ. 5፥19።

3. ምእመናን የክርስቶስ ምስክሮች ናቸው (ዮሐ. 15፥27፤ ሐ.ሥ. 1፥8)፤ ባይመሰክሩ ግን ክርስቶስ አይመሰክርላቸውም፤ ማቴ. 10፥32:33።

**ምስጉን፤** የተመሰገነ ማለት ነው፤ መዝ. 1፥1።

**ምስጋና፤** እግዚአብሔርን፥ ሌሎችንም ፍጡራን ከፍ የሚያደርግና የሚያከብር ቃል ወይም ድርጊት፤ ምሳ. 27፥21፤ መሳ. 16፥24፤ ዘጸ. 15፥11። መዝሙረ ዳዊት በምስጋና የተሞላ ነው። በተለይ መዝሙር 111-117 ሃሌ ሉያ ብለው ይጀምራሉ። በአ.ኪ. እግዚአብሔር በመላእክትም በሰውም ሲመሰገን እናገኛለን፤ ሉቃ. 2፥13:14፤ ቆላ. 3፥16፤ ራእ. 7፥9-12፤ 19፥5-8። ምእመናን በሁሉ ነገር እግዚአብሔርን እንዲያመሰግኑ ታዝዘዋል፤ 1ተሰ. 5፥16-18። ምስጋና የማጉረምረም ተቃራኒ ነው፤ ዘጸ. 16፥2-3፤ ዘኁ. 14፥26-30።

**ምሽግ፤** «ከተማ» ይመ.

**ምቀኝነት፤** በሌላ ሰው ተድላ ምክንያት መበሳጨት፤ የሰው የሆነውን በናፍቆትና በምኞት መመልከት። ምቀኝነት የሥጋ ሥራ እንጂ የመንፈስ ፍሬ አይደለም፥ ለአማኞችም ይህ ጠባይ ተገቢ አይደለም፤ ማር. 7፥22፤ ገላ. 5፥21፤ ቲቶ 3፥3።

**ምትሀት፤** መስሎ የሚታይና ታይቶ የሚጠፋ ረቂቅ መንፈስ። ክርስቶስ ለደቀ መዛሙርቱ በባሕር ላይና በዝግ ቤት በታያቸው ጊዜ ምትሀት መስሏቸው ነበር፤ ማር. 6፥49፤ ሉቃ. 24፥37።

**ምቹ፤** የሚስማማ፥ ተስማሚ፤ ማር. 6፥21፤ ሉቃ. 22፥6፤ ሐ.ሥ. 24፥25፤ 1ቆሮ. 16፥12።

**ምናሔም፤** የንጉሥ ዘካርያስ ገዳይ የነበረውን ሰሎምንን የገደለና ዐሥር ዓመት በእስራኤል ላይ የነገሠ ንጉሥ። የእስራኤል 16ተኛው ንጉሥ ነበረ። ክፉም አደረገ፤ እስራኤልንም ለአሦር ንጉሥ ግብር እንዲከፍሉ አደረገ፤ 2ነገ. 15፥14-22።

**ምናምንቴ፤** የተናቀ፥ ዝቅተኛ ለቁም ነገር ይሆናል ተብሎ የማይገመት፤ መሳ. 9፥4፤ ምሳ. 6፥12-15፤ 1ቆሮ. 1፥28።

**ምናሴ፤** የስሙ ትርጉም «ማስረሻ» ማለት ነው። 1. በግብጽ አገር ዮሴፍ ከአስናት የወለደው በኵር ልጅ፤ ዘፍ. 41፥50:51። ያዕቆብ የዮሴፍን ልጆች ምናሴንና ኤፍሬምን እንደ ራሱ ልጆች ቈጥሮ ባረካቸው፤ በስሞቻቸውም ከእስራኤል ነገዶች ሁለቱ፥ ነገደ ምናሴና ነገደ ኤፍሬም ተብለው ተሰየሙ፥ የኤፍሬም ነገድ ታላቁ ሆነ፤ ዘፍ. 48። የምናሴ ነገድ እኩሌታ ከዮርዳኖስ በስተምሥራቅ ለመቀመጥ ወደደ (ዘኍ. 32፥33:39:40)፥ የቀሩት የምናሴ ልጆችም ከዮርዳኖስ በስተ ምዕራብ የርስት ድርሻን ተቀበሉ፤ ኢያሱ 17። ጌዴዎንና ዮፍታሔ የተባሉት ጀግናዎች ከምናሴ ነገድ ነበሩ፤ መሳ. 6፥11:15፤ 11፥1፤ ዕብ. 11፥32። «ነገድ» ይመ.። ካ. 3 መ. ሠ.።

2. ከይሁዳ ነገሥታት ዐሥራ አራተኛው፥ የሕዝቅያስ ልጅ፤ 2ነገ. 20፥21። ከዐሥራ ሁለተኛው ዓመቱ ጀምሮ ከ687-642 ከክ.ል. ነገሠ። ባዕድ አምልኮትን እየተከተለ ከአሞራውያን ይልቅ ክፉ አደረገ፤ በኢየሩሳሌም ላይ የእግዚአብሔር ቍጣ እንዲመጣ አደረገ፤ 2ነገ. 21፥1-18፤ 2ዜ.መ. 33፥1-10፤ ኤር. 15፥4። የአሦር ንጉሥ ወደ ባቢሎን ማረከው፤ በዚያም ጸለየ። እግዚአብሔርም ምሕረት አደረገለትና ወደ ኢየሩሳሌም ተመለሰ፤ ሕዝቡ እግዚአብሔርን እንዲያመልኩ አዘዘ፤ 2ዜ.መ. 33፥11-20።

**ምናን፤** የጥንት ክብደት መለኪያ፤ ዕዝ. 2፥69። በኋላም ምናን ገንዘብን አመለከተ፤ ሉቃ. 19፥13። «ክብደት»፥ «ገንዘብ» ይመ.

**ምንዝር፤** አመነዘረ፤ አንድ ሰው ከሌላው ሰው የኑሮ ጓደኛ ጋር ቢገናኝ አመነዘረ ይባላል። በብ.ኪ. የሞት ፍርድ ሊፈረድበት ይቻል ነበር፤ ዘሌ. 20፥10። ሰዎች እግዚአብሔርን ትተው ሌላ አምላክ ሲያመልኩ አመንዝራዎች ይባላሉ፤ ኤር. 3፥9፤ ማቴ. 12፥39። ኢየሱስም ሴትን በማይገባ መመልከት ምንዝር እንደሆነ አስተማረ፤ ማቴ. 5፥27-30። «ዝሙት» ይመ.

**ምንደኛ፤** በተወሰነ ደመወዝ የተቀጠረ ሠራተኛ፤ ዘዳ. 24፥14:15፤ ኢዮብ 7፥1፤ ሚል. 3፥5።

**ምንዳ፤** ደመወዝ፤ ዘፍ. 29፥15።

**ምኞት፤** ከፍ ባለ ስሜት አንድ ነገርን መሻትና መፈለግ፥ መውደድ። ምኞት ሁለት ዓይነት ነው። 1. የማይገባ ምኞት፤ ዘጸ. 20፥17፤ ምሳ. 21፥26፤ ኤፌ. 4፥19፤ 5፥5፤ 1ጢሞ. 6፥9። ክፉ ምኞት የኃጢአት ምንጭ ነው፤ ያዕ. 1፥14:15። 2. የሚገባ

መልካም ምኞት፤ 1ጴጥ. 2፥2-3፤ ማቴ. 13፥17።

**ምክር፤** ስለ አካሄድ ለሰው የሚሰጥ አሳብ፤ ዘኁ. 31፥16፤ መሳ. 20፥7፤ 1ነገ. 1፥11-12። እግዚአብሔር ሁሉን የሚያውቅ ስለሆነ አማካሪ አያስፈልገውም፤ ኢሳ. 40፥13-14። በነገሥታት ዘመን አማካሪዎች በቤተ መንግሥት ልዩ ማዕረግ ነበራቸው፤ 2ሳሙ. 15፥12፤ 16፥23፤ 17፥5:14። የአርማትያሱ ዮሴፍ አማካሪ ነበረ፤ ማር. 15፥43። በቤተ ክርስቲያን የአንዳንድ ሰዎች አገልግሎት በተለይ ምክር መስጠት ነው፤ ሮም 12፥8።

**ምኩራብ፤** የአይሁድ የጸሎት ቤት። በብ.ኪ. ዘመን የአይሁድ አምልኮ በኢየሩሳሌም በነበረው ቤተ መቅደስና በሥርዓቱ የተመሠረተ ነበር። ናቡከደነፆር ግን ቤተ መቅደሱን አፈረሰ፥ ሕዝቡንም ወደ ባቢሎን አፈለሰ። ከዚያም ጊዜ ጀምሮ አይሁድ በሚገኙባቸው ስፍራዎች ሁሉ ለጸሎትና ለማኅበረተኛነት ልዩ ቤት ሊሠሩ እንደጀመሩ ይገመታል፤ ሕዝ. 11፥16። በዚህም ሆነ በሌላ በክርስቶስ ጊዜ በእስራኤል አገር በየቦታው በኢየሩሳሌምም ብዙ ምኩራቦች ነበሩ። ሐዋርያትም አይሁዶች በተበተኑባቸው ቦታዎች ሲዘዋወሩ አስቀድመው ወደ ምኩራቦች ገብተው ወንጌልን ያስተምሩ ነበር፤ ማቴ. 4፥23፤ ሐ.ሥ. 6፥9፤ 9፥2፤ 13፥5:14፤ 14፥1፤ 17፥1:10:17፤ 18፥4፤ 19፥8። ዐሥር የጐለመሱ ወንዶች ሲገኙ ምኩራብን መሥራት ይፈቀድላቸው ነበር፥ ቤቱም ትልቅ ወይም ትንሽ ሊሆን ይችላል።



ምኩራብ ከውጭ ሲታይ

በየምኩራቡ ውስጥ ሕግና ነቢያት የተጻፉባቸው የብራና ጥቅልሎች በአንድ ሣጥን ውስጥ (ታቦት) ይቀመጣሉ። የእግዚአብሔር ቃል ሲነበብ እንባቢው እንዲሰማ በተዘጋጀው ከፍተኛ ቦታ ይቆም ነበር። የክብር ወንበሮች ከዚህ ቦታ ፊት ለፊት ነበሩ፤ ማቴ. 23፥6። ወንዶችና ሴቶች ለየብቻቸው ይቀመጡ ነበር። ምኩራብ ለአምልኮና ለትምህርት ለኅብረተሰብም መገልገያ ይውል ነበር። ምኩራቡ በአለቆቹ ይመራ ነበር፤ ማር. 5፥22፤ ሐ.ሥ. 13፥15፤ 18፥8። ጉባኤውንም የሚመሩ አለቆች ነበሩ (ሐ.ሥ. 13፥15)፥ ጥፋተኛውን እስከ ሠላሳ ዘጠኝ ግርፋት በመግረፍ ወይም ከምኩራብ በማስወጣት ሊቀጡ ሥልጣን ነበራቸው፤ ዮሐ. 9፥34፤ 2ቆሮ. 11፥24። የምኩራቡ አገልጋይ ልጆችን ያስተምራል፥ ጥቅልሎችን ያቀርባል፥ ጥፋተኞችን ይገርፋል፥ ሌላውንም የአለቆች ትእዛዝ ይፈጽማል፤ ሉቃ. 4፥20። በየሰንበቱ ሕዝቡ ሁሉ በምኩራብ ይሰበሰቡ ነበር፤ ሉቃ. 4፥16፤ ሐ.ሥ. 15፥21። በዚያን ጊዜ በአምልኮታቸው ውስጥ ጸሎት ከሕግና ከነቢያት ንባብ፥ የዳዊትን መዝሙራት መዘመር፥ ስብከትና ቡራኬም ነበረ።



በምኩራብ ውስጥ ብ.ኪ. ሲነበብ

**ምዋርተኛ፤** ጋኔን በመጥራት የእንስሳትን ደምና ብልቶች በማየት፥ በአራዊት ጩኸት ወይም ሌላ ነገር በመመልከት የሆነውን ወይም የሚመጣውን ነገር እገልጣለሁ የሚል ጠንቋይ፤ ዘዳ. 18፥10፤ 1ሳሙ. 6፥2፤ 2ነገ. 17፥17፤ ኢሳ. 44፥25፤ ሆሴዕ 4፥12፤ ሐ.ሥ. 16፥16-18። «ጥንቆላ» ይመ.

**ምዕራፍ፤** 1. የመጽሐፍ ክፍል። 2. የርቀት መለኪያ፤ ሉቃ. 24፥13። አንድ ምዕራፍ የኪሎ ሜትር አምስተኛ ነው። «ርዝመት» ይመ.

**ምዝምዝ፤** እንደ ዘንግና እንደ ገመድ ዓይነት ሆኖ የተነጠረ የወርቅ ሽቦ፤ ምሳ. 8፥19፤ መ.መ. 5፥11:15።

**ምድረ በዳ፤** ደረቅ አገር። የእስራኤል ሕዝብ በምድረ በዳ አርባ ዓመት ኖሩ፤ ዘዳ. 32፥10። ክርስቶስ በምድረ በዳ ተፈተነ፤ ሉቃ. 4፥1-2። ሰው የማይገኝበት ገለልተኛ ቦታንም ያመለክታል፤ ማር. 6፥35:36።

**ምድር፤** ባሕር የሌለበት የብስ፤ ዘፍ. 1፥10። ከዚህም ሌላ ቃሉ ከሰማይ በታች ያለውን ሁሉ (ዘፍ. 1፥1)፥ መሬትን (ዘፍ. 2፥7)፥ አገርን (ዘፍ. 45፥18)፥ የዓለም ሰዎችን ሁሉ (ዘፍ. 6፥11) ሊያመለክት ይችላል። ምድር ለመኖሪያ እንድትሆን እንጂ ለከንቱ አልተፈጠረችም፤ እንዲሁም አዲስ

ሰማይና አዲስ ምድር እስከሚተኩ ድረስ የአሁኗ ምድር ጸንታ እንደምትኖር ተጠቅሷል፤ ኢሳ. 45፥18፤ መክ. 1፥4፤ ራእ. 21፥1።

**የምድር መናወጥ፤** መ.ቅ. ልዩ ልዩ የምድር መናወጥን ይጠቅሳል፥ አንዳንድ ጊዜ ዘመን ይቈጥርባቸዋል፤ አሞጽ 1፥1፤ ዘካ. 14፥5። እግዚአብሔር ለእስራኤል ለኤልያስም ራሱን በገለጠ ጊዜ ምድር ተናወጠ (ዘጸ. 19፥18፤ 1ነገ. 19፥11)፥ ኢየሱስ ከሞት በተነሣም ጊዜ ምድር ተናወጠ፤ ማቴ. 27፥51-53፤ 28፥2። የምድር መናወጥ የእግዚአብሔር የፍርድ ቀን ምሳሌ ሊሆን ይችላል፤ መሳ. 5፥4፤ መዝ. 77፥18፤ ኢሳ. 29፥6።

**ምድያም፤** አብርሃም ከኬጡራ የወለደው የአምስት ወገን አባት። አብርሃም ከከነዓን ወደ ምሥራቅ ላከው፤ ዘፍ. 25፥1-6። የምድያም ዘሮች በአባታቸው ስም ታወቁ፤ ከዮርዳኖስ በስተምሥራቅና ከከነዓን በስተደቡብ በምድረ በዳ ኖሩ፤ ከእስማኤላውያን ጋር ተባበሩ። ዮሴፍ ለምድያም ነጋዴዎች ተሸጠ፤ ዘፍ. 37፥28:36። ሙሴ የምድያምን ልጅ ገረድ አገባ፤ ዘጸ. 2፥21፤ 3፥1። የምድያምን ሰው በምድረ በዳ እንዲመራው ጠየቀ፤ ዘኍ. 10፥29-32። የምድያም ሽማግሌዎች ከሞዓብና ከሴዎን ጋር እስራኤልን ተቃወሙ፤ ዘኍ. 22፥4፤ ኢያሱ 13፥21። በመሳፍንት ዘመን ምድያማውያን በጌዴዎን ተሸነፉ፤ መሳ. 6፥1-8፥21፤ መዝ. 83፥9።



የምድያም ነጋዴዎች

**ምድጃ፤** በድንጋይ ይሠራል፤ በጭቃም ይለሰናል፤ በላዩ ምጣድ ተጥዶ ዳቦ ይጋገርበታል ወይም ማዕድናት ይቀልጡበታል። ምድጃ ሁለት ዓይነት ነው። ምድጃው በእሳት ከሞቀ በኋላ ጋጋሪው እሳቱን አውጥቶ ሊጡን በላዩ ያስቀምጣል። ወይም የምድጃው ታችኛው ክፍል ለእሳት፥ ላይኛው ደግሞ ለሊጥ ይሆናል፤ ሆሴዕ 7፥4-7፤ ኤር. 11፥3-4። «እቶን» ይመ.

**ምግብ፤** በመጀመሪያ ሰው ማናቸውንም ዓይነት የእህልና የዛፍ ፍሬ አታክልትም ለመብላት ተፈቀደለት፤ ዘፍ. 1፥29። ከጥፋት ውሃ በኋላ ሥጋን መብላት ጀመረ፤ ዘፍ. 9፥3። በሙሴ ሕግ ለምግብ የሚሆን የሥጋ ዓይነት ተወሰነ፤ ዘሌ. 11። የምግብ ዓይነትና አቀራረብ እንደ አገሩና እንደ ኑብረተ ሰቡ ልዩ ልዩ ነበር። ነገሥታት ትልቅና ሰፊ ግብዣ ያደርጉ ነበር (አስ. 1፥2-5)፥ ብዙ ሰዎች ከማዕዳቸው ይበሉ ነበር፤ 2ሳሙ. 9፥7፤ 1ነገ. 4፥22:23፤ 18፥19፤ ነህ. 5፥17-19።



ሴቶች ዳቦ ሲጋግሩ

**የማዕድ ሰዓት፤** በግብጽ ዋናው የምግብ ጊዜ እኩለ ቀን ላይ ነበር፤ ዘፍ. 43፥16። በእስራኤል ግን ተራው ሕዝብ ትንሽ ምግብ ይዞ ወደ ሥራው ይሄድ (ሩት 2፥14)፥ ማታም እንደ አቅሙ እራት ይበላ ነበር፤ ሩት 3፥7። በክርስቶስ ጊዜ አይሁድ በቀን ሁለት ጊዜ መብላት ለምደው ነበር፤ ሉቃ. 14፥12። ወንዶችና ሴቶች በአንድነት ይበሉ (ኢዮብ 1፥4)፥ ብዙ ጊዜም አንድ ዓይነት ምግብ ብቻ ያዘጋጁ ነበር፤ ሉቃ. 10፥38-42።

**በማዕድ ጊዜ አቀማመጥ፤** በአብርሃም ዘመን ሰዎች በመሬት ላይ ተቀምጠው ይበሉ ነበር (ዘፍ. 18፥8፤ 37፥25)፤ በኋላም ዕብራውያን በጠረጴዛ አጠገብ ተቀምጠው መብላት ጀመሩ፤ 1ነገ. 13፥20። በግሪክ ዓለም ታላላቅ ሰዎች በአልጋ ተጋድመው ይበሉ ነበር፤ አስ. 7፥8። ሰዎች በግብዣ ጊዜ በአጭር ማዕድ በሦስት አቅጣጫ በተዘረጉ ፍራሾች ላይ ጋደም ብለው ይበሉ ነበር። በአንድ ፍራሽ ከ3-5 ሰዎች ሊቀመጡ ይችላሉ። በማዕድ ላይ ካለው ወጭት በቀኝ እጅ ያጠቅሳሉ። ቁርሶ ማጕረስ የአክብሮት መግለጫ ነበር፤ ዮሐ. 13፥22-26። «ቅዱስ ቍርባን» ይመ. በግብዣ ላይ ለተጋባዦች እንደ ማዕረጋቸው ቦታ ይሰጣቸው ነበር። በስተግራ መቀመጥ የተከበረ ነበር፤ እንደዚሁም አሽከሮች ከሚገቡበት በስተቀኝ የተከበረ ወንበር ነበር፤ ዘፍ. 43፥33፤ ሉቃ. 14፥8-11።

**የማዕድ ሥርዓቶች፤** ከምግብ በፊት የተጋባዦን እግርና እጅ አለማስታጠብ እንደ ጕድለት ይቈጠር ነበር፤ ማር. 7፥3፤ ሉቃ. 7፥44። አይሁድ ከምግብ በፊት እግዚአብሔርን ያመሰግናሉ። ጋባዦም ምግቡን ያካፍላል፤ 1ሳሙ. 9፥23:24፤ ማቴ. 15፥36፤ ሉቃ. 24፥30። ከበሉም በኋላ እግዚአብሔርን ይባርካሉ፤ ዘዳ. 8፥10።

የምግብ ዓይነቶች፤ ሰዎች ስለ ምግብና መጠጥ ሲያስቡ ዋና ዋና ነገሮች እህል፥ ወይንና ዘይት ነበሩ፤ ዘዳ. 7፥13፤ ነህ. 5፥11፤ ሆሴዕ 2፥10። የምግብን ዓይነት በአምስት አርእስት ለማጠቃለል እንችላለን።

1. እህል፤ ዘፍ. 26፥12፤ 37፥7። በመ.ቅ. ውስጥ ምስር (ዘፍ. 25፥34)፥ ስንዴ (ዘፍ. 30፥14)፥ ሽንብራ፥ ባቄላ፥ ገብስ (2ሳሙ. 17፥28:29) ጤፍ፥ አጃ (ሕዝ. 4፥9) ተጠቅሰዋል። ከእነዚህም እንጀራ (ዘፍ. 21፥14)፥ ቂጣ (ዘጸ. 12፥8)፥ እንጐቻም (መሳ. 7፥13)፥ ተዘጋጅቶ ይበላል። ቆሎው ተቆልቶ ወይም ጥሬውን ወይም በእሸትነቱ የሚበላ እህልም አለ፤ ኢያሱ 5፥11፤ ዳን. 1፥16፤ ማቴ. 12፥1።

2. አታክልት፤ ዘፍ. 1፥29። ቀይና ነጭ ሽንኩርት፥ በጢሕ፥ ኩራት፥ ዱባ (ዘኁ. 11፥5) ጉመንም ተጠቅሰዋል (ምሳ. 15፥17)።

3. ፍራፍሬ፤ ዘፍ. 1፥29። ለውዝ፥ በለስ፥ ተምር፤ ዘፍ. 43፥11። ሮማን፥ ወይን (ዘኁ. 13፥23)፥ ወይራ (ዘጸ. 23፥11)፥ እንኮይም ተጠቅሰዋል፤ ምሳ. 25፥11። የወይን ዘቢብም የታወቀ ነው፤ 1ሳሙ. 25፥18።

4. ሥጋና ከእንስሳ የሚገኝ። ሥጋን በመጥበስና በመቀቀል (1ሳሙ. 2፥15)፥ በተቀመመ መረቅም ይበሉ ነበር፤ ሕዝ. 24፥10። ይስሐቅ የታደነ የእንስሳ ሥጋ ይበላ ነበር፤ ዘፍ. 27፥3። በእስራኤል ዘንድ በሬ፥ በግ፥ ፍየል፥ አጋዘን፥ አጭ፥ በራይሌ፥ ድኩላ፥ ንጹሕ ወፍና ዓሣ ይበሉ ነበር፤ ዘዳ. 14፥3-20። ልዩ ዓይነት የሆኑ አራት አንበጣዎች ለመብላት ተፈቅደዋል፤ ዘሌ. 11፥20-23፤ ማቴ. 3፥4። ለልዩ ግብዣ የሰባ ጥጃ (ዘፍ. 18፥7)፥ ፍሪዳም ይዘጋጁ ነበር፤ ሉቃ. 15፥23። ወተት ይጠጣ ነበር፥ ከወተትም እርጎ (ዘፍ. 18፥8)፥ ቅቤ (ዘዳ. 32፥14)፥ አይብም ለጥቅም ይውል ነበር፤ 1ሳሙ. 17፥18። ኢዮብ እንቁላል ይበላ እንደነበር ይገመታል (ኢዮብ 6፥6)፥ ማርም የተወደደ ነበር፤ ዘፍ. 43፥11።

5. ቅመማ ቅመም። ምግብ በጨው (ኢዮብ 6፥6)፥ በማር (ዘሌ. 2፥11)፥ በቅመም ይጣፍጣል። የተጠቀሱ ቅመሞች ሰናፍጭ (ማቴ. 13፥31)፥ አዝሙድ፥ እንስላል፥ ከሙን (ኢሳ. 28፥25-27፤ ማቴ. 23፥23)፥ ጤና አዳም (ሉቃ. 11፥42)፥ ድንብላልም ናቸው፤ ዘጸ. 16፥31። የቀደሙ ሰዎች እንደ ወጥ የሚጠቀሙበት የእንጀራ ማጥቀሻ ነበራቸው፤ ዮሐ. 13፥26። በሆምጣጤም ተጠቅመዋል፤ ሩት 2፥14። የምስር ወጥም የተለመደ ነበር፤ ዘፍ. 25፥30-34።

**ምጽራይም፤** የካም ሁለተኛ ልጅ፤ ዘፍ. 10፥6። ስድስት ልጆች ወለደ፤ 1ዜ.መ. 1፥8:11። የግብጾች አባት እንደሆነ ይነገራል፤ አገሩ በምጽራይም ቋንቋ ምስር ተብሎ ይጠራል።

**ምጽዋት፤** ለተቸገሩ አዝኖ መስጠት። ድሆችን በልግስና መርዳት ታዝዟል፤ ዘዳ. 15፥11። ሰው ሲመጸውት እግዚአብሔር ያያል፥ ይባርካልም። ግን ለታይታና ውለታን በማሰብ ቢደረግ አይጠቅምም፤ ማቴ. 6፥1-4። ምጽዋት በእግዚአብሔር መንግሥት ዋጋ እንዳለው ጌታችን አስተማረ፤ ሉቃ. 16፥9። ምጽዋት በዚህ ዓለም ለሕይወትና ለበደል ማስወገጃ ይሆናል፤ ዳን. 4፥27። በኢየሩሳሌም ምእመናን ሀብታቸውን ለድሆች ያካፍሉ ነበር (ሐ.ሥ. 4፥32፤ 6፥1-6)፥ ጳውሎስ ለድሆች በየቤ.ክ. ገንዘብ ሰበሰበ፥ የሚነግዱትም ከሚያተርፉት እንዲሰጡ አስተማረ፤ ሮም 15፥25-27፤ 1ቆሮ. 16፥1-4፤ 2ቆሮ. 9።

**ምጽጳ (መሴፋ)፤** የጠባቂ ግንብ ማለት ነው። በዚህ ስም ብዙ ቦታዎች ተጠርተዋል። ከእነርሱም የታወቀው ከኢየሩሳሌም በስተሰሜን ስምንት ኪ.ሜ. ርቆ የሚገኘው የከነዓናውያን ምሽግ ነው፤ ኢያሱ 15፥38። በዚህ ቦታ ንጉሥ ሳኦል ተመረጠ (1ሳሙ. 10፥17-27)፥ በባቢሎን ንጉሥ የተሾመው የኢየሩሳሌም ገዥ ጎዶልያስ በዚህ ስፍራ ተገደለ፤ ኤር. 40፥9-41፥3።

**ሞሎክ፤** አሞናውያንና ሌሎችም ነገዶች ልጆችን አቃጥለው በመሠዋት ያመለኩት ጣዖት፤ ዘሌ. 18፥21፤ 20፥1-5። ሰሎሞን ለሚስቶቹ የሞሎክን መስገጃ ሠራ፤ 1ነገ. 11፥7።

ምናሴ ለሞሎክ ልጆቹን በእሳት አሳለፈ፥ ኢዮስያስ ግን መስገጃውን አፈረሰ፤ 2ዜ.መ. 33፥6፤ 2ነገ. 23፥10። ነቢያት የሞሎክን አምልኮት ተቃወሙ፤ ኤር. 7፥29-34፤ 19፥1-13፤ ሕዝ. 20፥26-39፤ አሞጽ 5፥26።

**ሞሪያ፤** አብርሃም ይስሐቅን ለመሠዋት የሄደበት ተራራ፤ ዘፍ. 22፥2። ሰሎሞን ቤተ መቅደስን በሞሪያ ሠራ፤ 2ዜ.መ. 3፥1። ነገር ግን በታው አንድ መሆኑንና አለመሆኑን ለማረጋገጥ አንችልም።

**ሞራ ገላጭ፤** ለወደፊት የሚሆነውን ነገር ለማወቅ የእንስሳትን የሆድ ዕቃ በተለይ ጉበትንና ሞራን የሚመረምር ጠንቋይ፤ ዘዳ. 18፥10፤ ዘሌ. 19፥26፤ 2ነገ. 21፥6፤ ሕዝ. 21፥21። «ጥንቆላ» ይመ.

**ሞሳሕ፤** 1. የያፌት ልጅ፤ ዘፍ. 10፥2። 2. ከያፌት ልጅ ከሞሳሕ የተገኘ ወገን። ከእስራኤል በስተሰሜን በኩል ይኖሩ ነበር፤ ሕዝ. 27፥13፤ 38፥2:3።

**ሞት፤** የነፍስና የሥጋ መለየት ወይም ሕይወትን ማጣት። ይህም በሥጋዊም በመንፈሳዊም ሊሆን ይችላል፤ ማቴ. 8፥22። በአዳም አለመታዘዝ ምክንያት ሞት ወደ ዓለም ገባ፤ ሞት የኃጢአት ውጤት ነውና፤ ሮም 5፥12፤ 6፥23። አዳም ትሞታለህ በተባለው መሠረት ወዲያው በሥጋ አልሞተም፥ ነገር ግን ከእግዚአብሔር በመንፈስ ተለየ፤ ዘፍ. 2፥17፤ 3፥8:19:22-24። ከክርስቶስ ውጭ ያሉ ሰዎች ሙታን ናቸው፤ ሉቃ. 1፥79፤ ኤፌ. 2፥1፤ 1ዮሐ. 3፥14። መ.ቅ. በአንዳንድ ቦታ ከሞት በኋላ ስላለው የሰው ሁኔታ ከባድ ጥያቄ ይጠይቃል፤ ኢዮብ 14፥10-12፤ መክ. 3፥20-22።

እንደገናም የተረጋገጠ ማስረጃ ይሰጣል፥ ይህም እንደሚከተለው ነው። ሰው በሥጋ ሲሞት ነፍሱ ከሥጋው ከተለየ በኋላ ወደ እግዚአብሔር ይመለሳል፥ ፍርድንም ይቀበላል፤ መክ. 12፥7፤ 2ቆሮ. 5፥1-5፤ ፊል. 1፥21-23፤ ዕብ. 9፥27፤ ያዕ. 2፥26። ከሞት በኋላ ትንሣኤ ስላለ ሞት እንቅልፍ በሚል ቃል ተገልጧል፤ 1ነገ. 2፥10፤ ሐ.ሥ. 7፥60። ሰው ሲሞት ነፍሱ አያንቀላፋም፤ ሉቃ. 16፥23-24፤ ፊል. 1፥21-23፤ ራእ. 6፥9-11፤ 20፥4። ኃጢአተኞች በፍርድ ዕለት ለዘለዓለም ከእግዚአብሔር ፊት በእሳት ባሕር ይጣላሉ፤ ይህም ሁለተኛ ሞት ይባላል። ሥቃያቸውም አያልቅም፤ ኤር. 20፥11፤ ዳን. 12፥2፤ ማር. 9፥45፤ 2ተሰ. 1፥9፤ ይሁዳ 7፤ ራእ. 14፥11፤ 20፥6:14።

ክርስቶስ ግን በሞቱ ሞትን ሽሮአል፥ የሞትን ፍርሃትና መውጊያ አስወግዷል፤ 1ቆሮ. 15፥53-57፤ 2ጢሞ. 1፥10:11፤ ዕብ. 2፥9:14:15፤ ራእ. 1፥18። ክርስቶስን አምነው የሞቱ ለዘለዓለም ከእርሱ ጋር ይኖራሉ፤ ኢሳ. 35፥10፤ 45፥17፤ ዳን. 7፥14፤ 12፥2፤ ሉቃ. 23፥43፤ ዮሐ. 5፥24፤ 1ተሰ. 4፥13-18። ምእመናን በክርስቶስ ዕረፍትን ስለሚያገኙ ሞታቸው ዕረፍት ነው፤ ራእ. 14፥13።

**ሞዓብ፤** ሎጥ ከታላቅ ሴት ልጁ የወለደው የሞዓባውያን አባት፤ ዘፍ. 19፥37። ሞዓባውያን ከጨው ባሕር በስተምሥራቅ ስለሚኖሩ አገራቸው «ሞዓብ» ተባለ። ካ. 2 ረ።

እስራኤል ወደ ከነዓን ሲጓዙ በአገራቸው እንዲያልፉ አልፈቀዱም፤ መሳ. 11፥17:18። እስራኤልን እንዲረግም በለዓምን ቀጠሩ፤ ዘኍ. 22-24። በሞዓብና በእስራኤል መካከል ብዙ ጊዜ ጦርነት ነበረ፤ መሳ. 3፥12-30፤ 1ሳሙ. 14፥47፤ 2ሳሙ. 8፥2፤ 2ዜ.መ. 20፥1-30። በባዕድ አምልኮታቸው በተለይ በጣዖታቸው በካሞሽ ለእስራኤል እንቅፋት ሆነዋል፤ ዘኍ. 25፤ 1ነገ. 11፥7:33፤ ዕዝ. 9፥1። ነቢያት ተነበዩባቸው፤ ኢሳ. 15-16፤ ኤር. 9፥26፤ ሕዝ. 25፥9-11፤ አሞጽ 2፥1-2፤ ሶፎ. 2፥8-11። ሩት ሞዓባዊት ነበረች፤ ሩት 1፥4። ሞዓባውያን ወደ እግዚአብሔር ጉባኤ እንዳይገቡ እስከ ዐሥር ትውልድ ድረስ ተወግዘው ነበር፤ ዘዳ. 23፥3-6።

**ሞኝ፤** የልባም ተቃራኒ። እግዚአብሔር የለም የሚሉ በዚህ ቃል ተጠርተዋል፤ መዝ. 14፥1። የዓለም ጥበበኞች ወንጌልን እንደ ሞኝነትና ወንጌልን የሚሰብኩትን ደግሞ እንደ ሞኞች ይቈጥራሉ፤ 1ቆሮ. 1፥18-27፤ 2፥14፤ 3፥18-20፤ 4፥10፤ 2ጢሞ. 3፥9። ጳውሎስ በቤ.ክ. ከሚቃወሙት ጋር ሲከራከር አንዳንድ ጊዜ በምጸት አነጋገር ራሱን እንደ «ሞኝ» አድርጎ ተናግሯል፤ 2ቆሮ. 11፥16-21፤ 12፥6:11።

**ሞያተኛ፤** በተወሰነ ደመወዝ የተቀጠረ የቀን ሠራተኛ፤ ሉቃ. 15፥19፤ ዮሐ. 10፥12:13።

**ሞገስ፤** የእግዚአብሔር ወይም የሰው መልካም አመለካከት፤ ዘፍ. 6፥8፤ 18፥3፤ 39፥4፤ መዝ. 84፥11፤ ሉቃ. 2፥52፤ ሐ.ሥ. 2፥47። በአ.ኪ. ብዙ ጊዜ ሞገስ የሚለው ቃል አሳብ «ጸጋ» በሚለው ይጠቃለላል።

**ሠለስቱ ደቂቅ፤** ሦስቱ ወጣቶች።

**የሠለስቱ ደቂቅ መዝሙር፤** ሲድራቅ ሚሳቅና አብደናጎ በእሳት ውስጥ ተጥለው የዘመሩት መዝሙር። በትልቁ ያማርኛ መ.ቅ. ከዳንኤል 3፥23 ቀጥሎ ታትሟል።

**ሠመረ፤** ተወደደ፥ መልካም ሆነ፥ አማረ። ለመሥዋዕት ይነገራል፤ ዘሌ. 1፥3:4።

**ሠረገላ፤** ባለ ሁለት መንኰራኲር፥ በፈረስና በሌላም ዓይነት እንስሳት የሚሳብ፥ ለጭነት፥ ለሰልፍ ለጦርነት የሚጠቅም እንደ ጋሪ ያለ ተጐታች፤ ዘፍ. 41፥43፤ 46፥29፤ 1ሳሙ. 6፥7-16፤ 1ነገ. 22፥34፤ 2ነገ. 5፥9፤ ሐ.ሥ. 8፥28። የእስራኤል



የጭነት ሠረገላ በፈረስ ሲጐተት

ጠላቶች ብዙ ጊዜ በሠረገላዎች ይጠቀሙ ነበር፤ መሳ. 1፥19፤ 2ነገ. 6፥15። እስራኤላውያን ግን እስከ ዳዊት ጊዜ ድረስ ሠረገላ አልነበራቸውም፤ 1ዜ.መ. 18፥4። ኤልያስ በእሳት ሠረገላ ዐረገ፥ ይህም



የጦር ሠረገላ

የእግዚአብሔርን ኃይል የሚያመለክት ምሳሌ ነው፤ 2ነገ. 2፥11:12፤ 13፥14። ከዚህም ሌላ የቤት ዐምድ ተሸካሚ አግዳሚ እንጨት ሠረገላ ይባላል፤ 1ነገ. 7፥2፤ 2ዜ.መ. 3፥7። ገጽ 64 ይመ.



የጭነት ሠረገላ በበሬ ሲጐተት

**ሠራዊት**፤ ጭፍራ። ቃሉ ሰማያዊ ፍጥረትን ሁሉ (ዘፍ. 2፥1፤ ዘዳ. 4፥19)፥ ወታደሮችን (ዘፍ. 21፥22)፥ መላእክትን (ኢያሱ 5፥14፤ መዝ. 103፥21) ሊያመለክት ይችላል።

**የሠራዊት ጌታ**፤ የሁሉ ገዥ እግዚአብሔር የሚጠራበት ስም። የእግዚአብሔር ሠራዊት ትእዛዙን ለመፈጸም የተዘጋጁ ሁሉ ናቸው። ስሙ እግዚአብሔር ሕዝቡን እንደሚጠብቅ ያሳያል፤ 1ሳሙ. 1፥3፤ 17፥45፤ መዝ. 46፥7:11፤ ኤር. 11፥17፤ 30፥8-9። «ጸባዖት» ይመ.

**ሠርክ**፤ ማታ፥ ምሽት፥ የቀን መጨረሻ፥ የሌሊት መግቢያ። በዚህ ጊዜ መሥዋዕት ይቀርብ ነበር፤ ዘጸ. 29፥39-42፤ 1ነገ. 18፥29፤ መዝ. 141፥2።

**ሣራ**፤ ሦራ፤ ሣራ ልዕልት፥ ሦራ ልዕልቴ ማለት ነው። የአብርሃም ሚስት የይስሐቅ እናት፤ ዘፍ. 11፥29፤ 21፥2:3። መካን ነበረች ነገር ግን እግዚአብሔር ቃል ኪዳኑ በእርስዋ እንዲፈጸም ወሰነ። አብርሃም ሰዎች ስለ ውበትዋ ብለው እንዳይገድሉት ፈራ። ስለዚህም በራብ ምክንያት ወደ ግብጽ በተሰደደ ጊዜ እኅቴ ናት አለ። እርስዋም እኅቱ ነኝ በማለትዋ ነገሥታት ሊወስዱአት ሁለት ጊዜ ሲዘጋጁ እግዚአብሔር አዳናት፤ ዘፍ. 12፥10-20፤ 20፥1-18። አብርሃም ልጅ እንዲያገኝ ገረድዋን አጋርን ሰጠችው። በኋላ ግን አሠቃየቻት፤ ዘፍ. 16። ቃል ኪዳኑ በአጋር ልጅ በእስማኤል እንዲፈጸም የእግዚአብሔር ፈቃድ አልነበረም። እግዚአብሔር ከፍ ያለ የክብር ስም ለሣራ ሰጣት፤ ዘፍ. 17፥15-21። ሣራ እንደምትወልድ ስትሰማ ተጠራጥራ ሳቀች፤ ግን መሳቅዋን ካደች፤ ዘፍ. 18፥1-15። በእምነት በርትታ ፀነሰች፥ ይስሐቅንም ወለደች። ከወለደች በኋላ አጋርንና እስማኤልን አባረረች፤ ዘፍ. 21፥1-14። በኬብሮን ተቀበረች፤ ዘፍ. 23። በእምነትዋና በታዛዥነትዋ ተመሰገነች፤ ኢሳ. 51፥1:2፤ ዕብ. 11፥11፤ 1ጴጥ. 3፥6።

**ሣር**፤ ብዙ ዓይነት ያለው ልምላሜ። ከፍጥረቱ በሦስተኛው ቀን ተገኘ፤ ዘፍ. 1፥11። እስራኤል ለእግዚአብሔር ሲታዘዙ እግዚአብሔር ለከብቶቻቸው ሣርን ይሰጥ ነበር፤ ዘዳ. 11፥13-15። ከዝናም ወራት በኋላ ሣር በቶሎ ስለሚደርቅ ለሰው ሕይወትና ክብር ምሳሌ ሆኖ ይነገራል፤ መዝ. 103፥15፤ ኢሳ. 40፥6:7፤ ያዕ. 1፥9-11።

**ሥሉሴ**፤ በሦስት ዓይነት የሚጐነጐን የበቅሎ፥ የፈረስና የግመል የአንገት ጌጥ፤ መሳ. 8፥21:26።

**ሥላሴ**፤ ሦስትነት ማለት ነው። ከቃሉ ምሥጢር በቀር በመ.ቅ. አይገኝም። እውነተኛና ሕያው የሆነ አንድ አምላክ ብቻ አለ። ይህ አንዱ አምላክ በሦስት አካላት ስለሚኖር ሥላሴ የሚለው ቃል የአንዱን አምላክ የአካል፥ የስምና የግብር ሦስትነት ያመለክታል። በብ.ኪ. ለእግዚአብሔር አካላት ብዛት መሠረት የሚሆኑ ብዙ ጥቅሶች ይገኛሉ፤ ዘፍ. 1፥2:26፤ 2፥18፤ 11፥7፤ መዝ. 33፥6፤ ኢሳ. 6፥8። ሆኖም የብ.ኪ. ሰዎች እነዚህና ሌሎችም ጥቅሶች ስለ ሦስት አካላት እንደሚገልጡ አላስተዋሉም ነበር። አ.ኪ. ግን በእግዚአብሔር ዘንድ ሦስት አካላት እንዳሉ ስማቸውም አብ፥ ወልድ፥ መንፈስ ቅዱስ መሆኑን ይገልጣል። እያንዳንዱ ፍጹም አካል አለው። ይህም ማለት እግዚአብሔር በሦስት ዓይነት መልክ እየተለዋወጠ ራሱን ገለጧል ማለት ሳይሆን በባሕርይና በመለኮት አንድ የሆኑ ሦስት ፍጹማን አካላት አሉ ማለት ነው። እንግዲህ በእግዚአብሔር ዘንድ «እኔ፥ አንተ፥ እርሱ» የሚል አባባል አለ። «አካል» ሲባል ሌላ ትርጒም ቢኖረውም ከዚህ ላይ ግን ፍጹም ምሉእና ቋሚ እኔ ባይ ማለት ነው። ኢየሱስ «አባቴ» በማለት ራሱን ከአብ ጋር አስተካከለ፥ ከአብ ልዩ አካል መሆኑንም ገለጠ፤ ዮሐ. 5፥17:18። እንደዚሁም ኢየሱስ «ሌላ አጽናኝ ይሰጣችኋል» በማለቱ መንፈስ ቅዱስ እንደርሱ ያለ፥ ከእርሱም በአካል የተለየ መሆኑን አረጋገጠ፤ ዮሐ. 14፥15:16። በጥምቀት በቡራኬ በሌላም ጊዜ የሦስቱን ስም እንጠራለን፤ ማቴ. 28፥19፤ 1ቆሮ. 12፥4-6፤ 2ቆሮ. 13፥14፤ ኤፌ. 2፥20-22፤ 1ጴጥ. 1፥1:2። ሦስቱ አካላት የግል ግብር አላቸው፤ አብ የወልድ አባት ሲሆን፥ ወልድም የአብ ልጅ ነው። መንፈስ ቅዱስ ደግሞ የአብና የወልድ መንፈስ ነው፤ ዮሐ. 15፥26፤ ገላ. 4፥6። «እግዚአብሔር አብ»፥ «ኢየሱስ»፥ «መንፈስ ቅዱስ» ይመ.

**ሥልጣን**፤ በነገር ሁሉ የመምራት፥ የመፍረድ፥ የመግዛት ማንኛውንም ነገር የማድረግ ሙሉ መብት።

1. የእግዚአብሔር ሥልጣን፤ ሥልጣን ሁሉ የእግዚአብሔር ነው። ሰው ባለ ሥልጣን ቢባልም ከራሱ ሳይሆን ከእግዚአብሔር ሥልጣን ይቀበላል፤ ሮም 13፥1።

2. የክርስቶስ ሥልጣን፤ ክርስቶስ በልጅነቱ ከአብ ጋር እኩል ሥልጣን አለው። ራሱን ዝቅ አድርጎ ሰው ሆኖ ሲመጣ የመሲሕነት ሥልጣን ተሰጠው፤ በእግዚአብሔርና በሰው መካከል መካከለኛ ሆነ፤ ፊል. 2፥6-7፤ 1ጢሞ. 2፥5፤ ማቴ. 28፥18። ጌታችን በሥልጣን አስተማረ (ማቴ. 7፥29)፥ በሥልጣን አጋንንትን አወጣ (ሉቃ. 4፥36)፥ ኃጢአትን አስተሰረየ (ማር. 2፥10)፥ ለተከታዮቹ ሥልጣንን ሰጠ፤ ማር. 3፥15፤ ሉቃ. 10፥19። በሰማይና

በምድር ሁሉ ሥልጣን የእርሱ ነው፤ ማቴ. 28፥18፤ ዮሐ. 5፥27።

3. የሐዋርያት ሥልጣን፤ ከክርስቶስ ስለተላኩ የክርስቶስ ሥልጣን ነበራቸው፤ ማቴ. 10፥1፤ 28፥18-20፤ ዮሐ. 20፥21። ስለዚህም ቤ.ክ.ን ለማዘዝ የቤ.ክ.ም ትምህርትና ሥርዓት ለመወሰን መብት ነበራቸው፤ 2ቆሮ. 10፥8፤ 13፥10፤ 1ቆሮ. 5፥3-5፤ 11፥34፤ 14፥37።

4. የቤተ ክርስቲያን ሥልጣን፤ ክርስቶስ በሰጣት ሹሞችዋ አማካይነት መንፈሳዊ ሥልጣን አላት። በሥልጣን ወንጌልን ትሰብካለች፤ የቅዱሳት ምሥጢራትን አገልግሎት ትፈጽማለች፤ ምእመናንን ታስተዳድራለች፤ ማቴ. 16፥19፤ 28፥19-20፤ 1ቆሮ. 5፥5:12-13።

5. የአማኝ ሥልጣን፤ የእግዚአብሔር ልጅ በመሆን ሥልጣን አለው፤ ዮሐ. 1፥12።

6. የቤተሰብ ሥልጣን፤ ክርስቶስ የቤ.ክ. ራስ እንደሆነ ባል የሚስቱ ራስ ነው። በጭቆና እንዲገዛት ሳይሆን ክርስቶስ ቤ.ክ.ን እንደሚንከባከብና እንደሚመግብ በፍቅሩም እንደሚያስተዳድር ባሎች ሚስቶቻቸውን በእኩልነት እያከበሩ ማስተዳደር አለባቸው፤ 1ቆሮ. 7፥4፤ 11፥3:11፤ ገላ. 3፥28፤ 1ጴጥ. 3፥7። ወላጆች በልጆቻቸው ላይ ሥልጣን አላቸው (1ጢሞ. 3፥4:12)፤ ስለዚህ ሚስቶች ለባሎቻቸው (ኤፌ. 5፥22፤ 1ጴጥ. 3፥1-6)፥ ልጆች ለወላጆቻቸው መታዘዝ ይገባቸዋል፤ ኤፌ. 6፥1-3።

7. የመንግሥት ሥልጣን፤ ቢያስተውሉም ባያስተውሉም ባለሥልጣናት ሁሉ ሹመታቸውን ከእግዚአብሔር ተቀብለዋልና ሰዎች ሁሉ ሊታዘዙላቸው ይገባል፤ ዮሐ. 19፥11፤ ሮም 13፥1-7፤ ማቴ. 22፥17-21። ሆኖም ይህ ሊሆን የሚቻለው የባለሥልጣኑ ትእዛዝ ከእግዚአብሔር ትእዛዛት ጋር ሲስማማ ነው፤ ሐ.ሥ. 4፥19፤ 5፥29።

8. የሰይጣን ሥልጣን፤ በኤፌ. 6፥12 እና በ2ቆሮ. 4፥4 ላይ ሰይጣን ባለሥልጣን እንደሆነ ተገልጧል። የተሰጠውን ሥልጣን ግን ያለ አግባብ ተጠቅሞበታል፤ ሉቃ. 4፥6፤ 22፥53፤ ኤፌ. 2፥1-2፤ ቆላ. 1፥13-14። ሰይጣን የተወሰነ ሥልጣን እንዲኖረው እግዚአብሔር ፈቅዶለታል፤ 1ነገ. 22፥20-23፤ ኢዮብ 1፥12፤ 2፥6። በዓለም መጨረሻ ግን ፈጽሞ ይወድቃል፤ ማቴ. 25፥41።

**ሥራ**፤ በመጀመሪያ እግዚአብሔር ሥራ ሠራ፤ ዘፍ. 1፥1፤ 2፥2፤ መዝ. 111። እግዚአብሔር ሰውን ለሥራ ፈጠረ፤ ዘፍ. 2፥15። በኃጢአት ምክንያት ሥራ አድካሚና ከባድ ሆነ፤ ዘፍ. 3፥19:23። ሰው ሥራ እንዲሠራ የእግዚአብሔር ትእዛዝ ነው፤ ዘጸ. 20፥9፤ መዝ. 104፥23፤ ኤፌ. 4፥28። ሰው በሙሉ ኃይሉ ለጌታ ብሎ መሥራት ይገባዋል፤ መክ. 9፥10፤ ቆላ. 3፥17:23፤ 1ተሰ. 4፥10-12። በሥራውም ሊደሰት ይችላል፤ መክ. 5፥18-20፤ መዝ. 128፥2። ክርስቲያን በሥራው መልካም አርአያን ማሳየት ይገባዋል፥ ሰውም ለመሥራት ባይወድ አይብላ ተብሏል፤ 2ተሰ. 3፥8-10።

ሰው የሚሠራው ሁሉ በሁለት ሊከፈል ይችላል። ይኸውም ክፉ ሥራና መልካም ሥራ ነው። ማንኛውም ክፉ ሥራ ኃጢአት ነው። ክፉ ሥራ ሰውን ወይም እግዚአብሔርን መበደል ነው፤ መዝ. 141፥4፤ 101፥7፤ ሚክ. 2፥1፤ ሮም 13፥12፤ ቆላ. 1፥21:22። ክፉ ሥራ የሥጋ ሥራ ይባላል፤ ገላ. 5፥19-21። ከልብ ይወጣል፤ ማር. 7፥21-23።

መልካም ሥራ ለእግዚአብሔር ሕግ መታዘዝ፥ የእግዚአብሔርን ፈቃድ መፈጸምና የእግዚአብሔርን ሥራ መሥራት ነው፤ ይህም የእግዚአብሔር ሰው ያሰኛል፤ ማቴ. 5፥16፤ ዮሐ. 4፥34፤ 6፥28-29፤ 8፥39፤ 10፥32፤ 14፥12። ሰው ያለ እምነት እግዚአብሔርን ማስደሰት አይችልም፤ ዕብ. 11፥6። ይልቁንም ሰው በክርስቶስ ሲያምን የተለወጠ ልብ ስለሚኖረው መልካም ሥራ ይሠራል፤ ለዚህም ሥራ ይመሰገናል፤ ዋጋውንም በመንግሥተ ሰማያት ይቀበላል፤ ማቴ. 25፥21:23:34-40፤ 2ቆሮ. 5፥10፤ ራእ. 20፥12።

ነገር ግን ፈሪሳውያን እንደሚያደርጉት ሰው በሥራው ሊመካ አይገባውም፤ ሉቃ. 17፥10፤ 18፥9-14፤ ኤፌ. 2፥9። ምክንያቱም መልካም ሥራ የሰውን ክፋት ሊደመስስ አይችልም፤ ያዕ. 2፥10-11። ሰው ከዳነ በኋላም እንኳ ክፉ ሥራ ሊሠራ ይችላል፤ 1ዮሐ. 1፥8-2፥1። በሌላ አንጻር ደግሞ አንዳንድ «አማኞች» ሥራ የሌለበት እውነተኛ እምነት ይኖራል ብለው እንደሚያስቡት ማሰብ አይገባም፤ ያዕ. 2፥18-26። የሰው ሥራ በመጽደቅና በመዳን ውስጥ ምን ስፍራ እንዳለው ሐዋርያው ጳውሎስ በሮም 3፥20:28፤ ገላ. 2፥16፤ ኤፌ. 2፥8-10፤ 2ጢሞ. 1፥9፤ ቲቶ 3፥5 ላይ ጽፏል። «እምነት»፥ «ጻድቅ»፥ «ጽድቅ» ይመ.

ከኃጢአት የምንድነው ክርስቶስ በመስቀል ላይ በፈጸመልን ሥራ ነው፤ ዮሐ. 19፥30፤ 6፥29። በክርስቶስ እምነን ከኃጢአት ከዳንን አዲስ ሕይወት ይኖረናል፤ 2ቆሮ. 5፥17። ይህን አዲስ ሕይወት እንደተቀበልን ለማሳየት መንፈስ ቅዱስ በውስጣችን ሆኖ በእኛ በኩል መልካም ሥራ እንድንሠራ ያደርጋል፤ ገላ. 5፥22:23። እምነታችን በመልካም ሥራችን ይገለጣል፥ መልካም ሥራ የእምነት ፍሬ ነው። እምነት መልካም ሥራን ያስከትላል፤ ያዕ. 2፥18፤ ኤፌ. 2፥10፤ ማቴ. 5፥16፤ 2ተሰ. 2፥16:17፤ 1ጴጥ. 2፥12።

**ሥራይ**፤ መርዝ ያለበት፥ ሊገድል የሚችል መድኃኒት፤ ዘዳ. 32፥33።

**ሥርዓተ ጽዮን**፤ 30 ቀኖና (አንቀጽ) ያለበት የሲኖዶስ መጽሐፍ ክፍል። «ሲኖዶስ» ይመ.

**ሥርዓት**፤ የመንግሥት፥ የቤ.ክ.፥ የሕዝብ ወይም የአንድ ድርጅት የአስተዳደር፥ የአመራር ወይም የአካሄድ ሕግ፥ ደንብ፥ ብያኔ፤ ምሳ. 30፥27፤ 1ቆሮ. 14፥40፤ ገላ. 1፥14።

**ሥቃይ**፤ ዓለም መልካም ሆኖ ከተፈጠረ በኋላ ሥቃይ በኃጢአት ምክንያት ገባ፤ ዘፍ. 1፥31፤

3:15-19። በዚህ ዓለም ሥቃይ በብዙ ዓይነት መንገድ ይገለጣል። ከሚመጣው ዓለም ክብር ጋር ግን አይመዛዘንም፤ ሮም 8፥18። በክርስቶስ ያላመኑ በሚመጣው ዓለም ለዘለዓለም ይሠቃያሉ፤ ማር. 9፥42-48፤ ራእ. 14፥9-11። ስለ ኃጢአታቸው በሞተው በክርስቶስ የሚያምኑ ግን በሚመጣው ዓለም ሥቃይን አያዩም፤ ኢሳ. 53፥5፤ ራእ. 21፥4። «መከራ» ይመ.

**ሥጋ፤** ልዩ ልዩ ነገርን ያመለክታል።

1. ከአጥንት በቀር የሰው ወይም የእንስሳ ክፍል፤ ዘፍ. 40፥19።

2. ጠቅላላው ግዙፍ የሰው አቅዋም፤ ያዕ. 2፥26።

3. የሰው ሁለንተና (መዝ. 16፥9፤ ዮሐ. 1፥14፤ 1ዮሐ. 4፥2)፥ ይህም ደካማ ነው፤ ማቴ. 26፥41፤ ሮም 6፥19።

4. ሰዎች ሁሉ፤ ዮሐ. 17፥1-2።

5. ሕያዋን ሁሉ፤ ዘፍ. 6፥17።

6. ያለ መንፈስ ቅዱስ የሚኖር፥ በኃጢአት የሚመራ የሰው ባሕርይ፤ ይህም ረቂቅ የሆነ በኃጢአተኛው ውስጥ ያለ የኃጢአት ሕግ እንጂ ግዙፍ ክፍል አይደለም (ሮም 7፥14:23፤ 8፥2:5-9)፤ ሥጋ መንፈስን ይቃወማል፥ ሥራውም ግልጥ ነው፤ ገላ. 5፥16-21። ምእመን በክርስቶስ ስለሆነ ሥጋንና ምኞቱን ከጺልና ለሥጋ ማሰብ አይገባውም፤ ገላ. 5፥24፤ ሮም 6፥6፤ 8፥13፤ 13፥14።

**ሦራ፤** «ሣራ» ይመ.

**ሦስተኛ፤** በዘጸ. 14፥7፤ 15፥4 መሠረት የሦስተኛ ክፍለ ጦር ሠራዊት አለቃ ማለት ነው።

**ረባት፤** የአሞን ዋና ከተማ፤ ዘዳ. 3፥11፤ ኢያሱ 13፥25። በአ.ኪ. ዘመን ዐሥሩ ከተሞች ከተባሉት አንደኛው ከተማ። ዛሬ ስሙ ተለውጦ የዮርዳኖስ መንግሥት ዋና ከተማ አማን ተብሏል። ከተማው ከዮርዳኖስ በስተምሥራቅ 35 ኪ.ሜ. ያህል ርቆ በኢያሪኮ ፊት ለፊት ይገኛል።

**ረአሶን፤** በይሁዳ ንጉሥ በአካዝ ዘመን የነበረ የሶርያ ንጉሥ። ከእስራኤል ንጉሥ ከፋቁሔ ጋር ተባብሮ በኢየሩሳሌም ላይ ወጣ። አካዝም የአሦርን ንጉሥ፥ አድነኝ ብሎ ለመነው። የአሦር ንጉሥ ሶርያን አሸንፎ ረአሶንን ገደለ፤ 2ነገ. 15፥37-16፥9፤ ኢሳ. 7፥1-9።

**ረዋት፤** የውሃ መያዣ እርኮት፤ ከቁርበት ይሠራል፤ በምሳሌ ደመናን ያመለክታል፤ ኢዮብ 38፥37:38።

**ረዓብ፤** 1. የእስራኤልን ሰላዮች የሸሸገች በኢያሪኮ ትኖር የነበረች ጋለሞታ። እስራኤል በእግዚአብሔር ኃይል ከነዓንን እንደሚይዙ አመነች፤ ከቤተሰብዋም ጋር ዳነች፤ ኢያሱ 2፥1-21፤ 6፥17-25፤ ዕብ. 11፥31፤ ያዕ. 2፥25። ብዙ ሊቃውንት የዳዊት ቅድመ አያት ራኬብ ረዓብ ናት ይላሉ፤ ማቴ. 1፥5። 2. በአፈ ታሪክ የጥልቅ ባሕር አውሬ፤ የእግዚአብሔር ጠላት፤ ኢዮብ 26፥12፤ መዝ. 89፥10። 3. ግብጽን ሊያመለክት ይችላል፤ መዝ. 87፥4፤ ኢሳ. 30፥7፤ 51፥9።

**ረዓድ፤** መንቀጥቀጥ ያለበት ፍርሃት። በፍጹም ልብ ለእግዚአብሔር መገዛትን ያሳያል፤ መዝ. 2፥11።

**ረዳት፤** ጥሪውን ወይም ሥራውን እንዲፈጽም አንድን ሰው የሚረዳ ሌላ ሰው፤ ዘፍ. 2፥18። እግዚአብሔር «ረዳቴ» በመባሉ ረዳቱ ከሚረዳው ጋር እንደየሁኔታው ምን ዓይነት ግንኙነት እንዳለው መለየት ያስፈልጋል፤ መዝ. 30፥10፤ 121፥1-2። «እርዳታ» ይመ.

**ሩሃማ፤** ትርጉሙ «ምሕረት» ማለት ነው፤ ሆሴዕ 2፥3። «ሎሩሃማ» ይመ.

**ሩት፤** በመሳፍንት ዘመን የነበረች የኑኃሚንን ልጅ ማሕሎንን ያገባች ሞዓባዊት። ኑኃሚንና ባልዋ በረሃብ ምክንያት ከልጆቻቸው ጋር ከኤፍራታ አገር ተነሥተው ወደ ሞዓብ ሄዱ። ልጃቸው ማሕሎን ሩት የተባለችውን የሞዓብ ሴት አገባ። ኑኃሚን ባልዋና ልጆችዋ ከሞቱ በኋላ ወደ አገርዋ ለመመለስ አሰበች፤ ሩትም በእግዚአብሔር ታምና ከእርስዋ ጋር ለመሄድ ወሰነች። ሩት ኑኃሚንን እያገለገለች የቤተ ልሔምን በዔዝን ለማግባት በቃች። ተጋብተውም ኢዮቤድን ወለዱ፥ ኢዮቤድ የእሴይ አባት ነበር። ታሪኩ በመጽሐፈ ሩት ተጽፏል።

**የሩት መጽሐፍ፤** መጽሐፉ እግዚአብሔር ከእሕዛብ ወገን የነበረችውን ሩትን በእምነትዋ ምክንያት እንደተቀበላት (1፥16:17)፥ የዳዊት ቅድመ አያትም እንደሆነች ያሳያል፤ 4፥13-17፤ ማቴ. 1፥5። እንደዚሁም የንጉሥ ዳዊትን ቅድመ አያቶች በመዘርዘር መጽሐፈ መሳፍንትና መጽሐፈ ሳሙኤልን ያያይዛል።

አከፋፈል ፦

ም. 1.፤ ሩት ከኑኃሚን ጋር ወደ ቤተልሔም እንደሄደች፥

ም. 2.፤ በኑኃሚን ሀብታም ዘመድ በበዔዝ እርሻ እንደቃረመች፥

ም. 3.፤ ሩት እንዲያገባት በዔዝን እንደጠየቀች፥

ም. 4.፤ ሩት በዔዝን አግብታ የክርስቶስን ቅድመ አያት ኢዮቤድን እንደወለደች።

**ሩጫ፤** በተለይ በግሪክ አገር ሩጫ የተወደደ ጨዋታ ነበር። የክርስቲያን ሕይወት በሩጫ ይመሰላል፤ 1ቆሮ. 9፥24፤ 2ጢሞ. 4፥7፤ ዕብ. 12፥1-2። «ጨዋታ» ይመ.

**ራሔል፤** ከላባ ሁለት ሴቶች ልጆች ታናሺቱ፤ ዘፍ. 29፥16። ያዕቆብን አግብታ (ዘፍ. 29፥28)፥ አያሌ ዓመታት መካን ሆና ከኖረች በኋላ ዮሴፍንና ብንያምን ወለደች፤ ዘፍ. 29፥31፤ 30፥22-24፤ 35፥16-18። ያዕቆብ ሁለቱን የዮሴፍ ልጆች እንደ ራሱ ልጆች ስላደረገ ራሔል ከእስራኤል ነገዶች የሦስቱ፥ የኤፍሬም፥ የምናሴና የብንያም እናት ሆነች፤

ዘፍ. 48፥5፤ ዘኍ. 1፥4:9:10፤ ሩት 4፥11።

ያዕቆብ የአክስትዋ የርብቃ ልጅ ሲሆን በአባቱ በኩል ደግሞ ከሚስቱ ከራሔል ጋር ዝምድና ነበረው፤ ዘፍ. 24፥15። ካያት ጊዜ ጀምሮ ወደዳት፤ በጠቅላላው 14 ዓመት ስለ እርስዋ አባትዋን አገለገለ፤ ዘፍ. 29፥4-30። ላባም ያዕቆብን በማታለል አስቀድሞ ልያን ስለ ዳረለት፥ ሁለቱ እኅትማማች እርስ በርሳቸው ተቀናኑ፤ ዘፍ. 30፥ 1-24። ሁለቱም ከያዕቆብ ጋር ወደ ከነዓን ለመሄድ ተስማሙ፤ ዘፍ. 31፥4-20። ራሔል የአባትዋን ጣዖታት ሰረቀችና አታለለችው፤ ዘፍ. 31፥30-35። በኋላ ለያዕቆብ ሰጠቻቸው፥ እርሱም ቀበራቸው፤ ዘፍ. 35፥2-4። እስከ መጨረሻ ወደዳት (ዘፍ. 33፥2)፤ በኤፍራታ አቅራቢያ በሞተች ጊዜ ያዕቆብ በመቃብርዋ ላይ ሐውልት አቆመ፤ ዘፍ. 35፥19:20፤ 48፥7፤ 1ሳሙ. 10፥2። ራሔል ለእስራኤል እናቶች ሁሉ ተጠሪ ምሳሌ ሆና ተጠቅሳለች፤ ኤር. 31፥15፤ ማቴ. 2፥17:18።

**የራሔል መቃብር፤** ከቤተ ልሔም አንድ ኪ.ሜ. ርቆ ይገኛል፤ ዘፍ. 35፥16-20። እስከ ዛሬም ድረስ ይታያል።

**ራማ፤** ከፍታ ማለት ነው። አንዳንድ ከተማዎች ራማ ተብለዋል፤ ከእነርሱም የታወቀው በገባዖንና በጊብዓ አጠገብ የነበረ ከተማ ነው፤ ኢያሱ 18፥25፤ መሳ. 19፥13። ይህ የዲቦራ አገር ነበር፤ መሳ. 4፥5። ኤርምያስ ታስሮ ከኢየሩሳሌም ከተወሰደ በኋላ ከራማ ተለቀቀ። ግን ይህ ራማ የትኛው እንደሆነ አልታወቀም፤ ኤር. 40፥1። ራሔል በራማ አጠገብ ተቀበረች፤ ስለዚህም የሐዘን ቦታ ሆነ፤ ኤር. 31፥15፤ ማቴ. 2፥18። «አርማቴም» ይመ.

**ራሞት፤** በጋድ አገር የነበረ የመማፀኛ ከተማ፤ ኢያሱ 20፥8፤ 1ነገ. 22፥1-37፤ ካ. 3ሠ።

**ራስ፤** በምሳሌነት ራስ የሥልጣንን ብልጫና የኃይልን ምንጭ ያሳያል፤ መሳ. 11፥11። ክርስቶስ የቤ.ክ. (ቆላ. 1፥17-19)፥ የወንድ (1ቆሮ. 11፥3)፥ የዓለም ሁሉ (ኤፌ. 1፥22)፥ የመንፈስም ሁሉ፥ (ቆላ. 2፥10) ራስ ነው። ወንድ የሴት ራስ ነው፤ 1ቆሮ. 11፥3፤ ኤፌ. 5፥23። እግዚአብሔር (አብ) የክርስቶስ ራስ ነው ሲል የባሕርይ አባትነቱን ያሳያል፤ 1ቆሮ. 11፥3። ራስነት ሁልጊዜ የባሕርይ የበላይነትን አያሳይም፤ እንዲሁም ወንድ የሴት ራስ ነው ሲል አስተዳደርን እንጂ የባሕርይን የበላይነት አያመለክትም።

**የራስ ቍር፤** ከናስ ወይም ከቆዳ የተሠራ በራስ ላይ የሚደፋ የጦር መጣሪያ መከላከያ፤ 1ሳሙ. 17፥5:38፤ 2ዜ.መ. 26፥14። የመዳን ምሳሌ ነው፤ ኤፌ. 6፥17። «የጦር መሣሪያ» ይመ.

**ራስን መሸፈን፤** በዱሮ ዘመን በግሪክ አገር ከጋለሞቶች በቀር ሴቶች ሁሉ ራሳቸውን ይከናነቡ ነበር። ሴቶች ምእመናትም ወንጌል እንዳይሰደብ ባህሉንም ለመጠበቅ ራሳቸውን ይከናነቡ ነበር፤ 1ቆሮ. 11፥6።

**ራስን መግዛት፤** የሥጋን ምኞትና አሳብን መቈጣጠርና መግታት ማለት ነው። ይህም ስለ ርኵሰት፥ ስለ መስከር፥ ስለ ቍጣም ሊሆን ይችላል፤ ሐ.ሥ. 24፥25። ራስን መግዛት የሚቻለው ለመንፈስ ቅዱስ ስንገዛ ነው፥ የመንፈስ ፍሬ ነውና፤ ገላ. 5፥22። አማኝ ራሱን መግዛት ይኖርበታል፤ 2ጢሞ. 1፥6፤ 1ቆሮ. 9፥25። የእግዚአብሔር ሰዎች በብዙ ቦታ ራሳቸውን ሲገዙ ይታያሉ፤ 2ሳሙ. 16፥5-13፤ ሉቃ. 23፥8-11።

**ራቁት፤** «ዕራቁት» ይመ.

**ራብ፤** (ረሃብ)፤ በእስራኤል አገር ከድርቅ፥ ከዐውሎ ነፋስ፥ ከቸነፈር፥ ከአንበጣ፥ ከጦርነትም የተነሣ ብዙ ጊዜ ራብ ነበር፤ ዘፍ. 12፥10፤ 41፥56፤ 1ነገ. 17፥1፤ 18፥2፤ 2ነገ. 6፥25። በሰው ኃጢአት ምክንያት መሬት ተረገመ (ዘፍ. 3፥17)፤ ራብ የአለመታዘዝ ውጤት ስለመሆኑ ተደጋግሞ ተገልጧል፤ ዘዳ. 28፥15-24፤ ኤር. 14፥10-18፤ አሞጽ 4፥6-10። ራብ የእግዚአብሔርን ቃል ያለመስማት ምሳሌ ሆኖ ተነግሯል፤ አሞጽ 8፥11።

**ራእይ፤** ሰው ሳያንቀላፋ በተመስጦ የሚያየውና የእግዚአብሔር ቃል የሚገለጥበት። ራእይ ከሕልም የተለየ ነው። ራእይ እግዚአብሔርን ለሚያውቁ፥ የእግዚአብሔር መንፈስ ላደረባቸው ይሰጣል፤ ዘኍ. 12፥6፤ ሐ.ሥ. 2፥17። በብ.ኪ. ዘመን ራእይ የታያቸው ነቢያት ብዙዎች ናቸው። በተለይም ሕዝቅኤልና ዳንኤል ብዙ ራእይ አይተዋል። በአ.ኪ.ም የእግዚአብሔር ፈቃድ ለዘካርያስ (ሉቃ. 1፥22)፥ ለሐናንያ (ሐ.ሥ. 9፥10)፥ ለቆርኔሌዎስ (ሐ.ሥ. 10፥3)፥ ለጴጥሮስ (ሐ.ሥ. 10፥9-17፤ 11፥5)፥ ለጳውሎስ (ሐ.ሥ. 18፥9)፥ ለዮሐንስም (ራእ. 1፥17-19፤ 4፥1)፤ በራእይ ተገለጠ። «ነቢይ» ይመ.

**ራጉኤል፤** «ዮቶር» ይመ.

**ራፊዲም፤** የእስራኤል ሕዝብ ወደ ደብረ ሲና ከመድረሳቸው በፊት ለመጨረሻ ጊዜ የሰፈሩበት ቦታ። በዚያ ሙሴ በበትሩ ዐለትን መትቶ ውሃ አወጣ። እጆቹንም ዘርግቶ ሲጸልይ ሳለ እስራኤል በኢያሱ መሪነት አማሌቃውያንን ለማሸነፍ ቻሉ። ቦታው ማሳህና መሪባ ተባለ፤ ዘጸ. 17፥1-16፤ 19፥2።

**ራፋስቂስ፤** እንደ ተርታንና እንደ ራፌስ የአሦር የማዕርግ ስም ነበረ እንጂ የመጠሪያ ስም አልነበረም። ትርጕሙ «የባላባቶች አለቃ» ማለት ይመስላል። የአሦር ንጉሥ ሰናክሬም ከታላላቆቹ አለቆች እነዚህን ሦስት ሰዎች ወደ ሕዝቅያስ ወደ ኢየሩሳሌም ላካቸው። ራፋስቂስ የተባለው ተናጋሪ ሆኖ በአይሁድ ላይ ዛተባቸው፤ እነርሱም ዝም አሉት፤ 2ነገ. 18፥17:19:26-28:37፤ 19፥4:8፤ ኢሳ. 36፥2:4:11-13:22፤ 37፥4:8።

**ራፋይም፤** 1. በከነዓን የነበሩ ረጃጅም ኃያላን ሕዝቦች፤ ዘፍ. 14፥5፤ ዘዳ. 2፥20:21፤ ኢያሱ 17፥15። 2. ከኢየሩሳሌም በደቡብ በኩል ከቤተ

ልሔም 5 ኪ.ሜ. ርቆ የሚገኝ ሸለቆ። ዳዊት ሁለት ጊዜ ፍልስጥኤማውያንን በዚህ ሸለቆ አሸነፈ፤ 2ሳሙ. 5፥17-25።

**ራፌስ፤** በአሦርና በባቢሎን መንግሥት የማዕርግ ስም፤ 2ነገ. 18፥17።

**ሬካባውያን፤** የሬካብ ዘሮች፥ ወገኖችና ተከታዮች። የሬካብ ልጅ ኢዮናዳብ ለእግዚአብሔር አምልኮት ቅንዓት ስለነበረው የበዓልን አምልኮት ለማጥፋት ከኢዩ ጋር ተባበረ፤ 2ነገ. 10፥15-31። እስራኤል በምድረ በዳ እግዚአብሔርን እንደተከተሉ የእርሱ ዘሮችም ከእግዚአብሔር እንዳይርቁ አዘዛቸው። ዘሮቹ እስከ ኤርምያስ ዘመን ድረስ ታዘዙና እግዚአብሔር ተስፋ ሰጣቸው፤ ኤር. 35፤ ነህ. 3፥14።

**ሬፋን፤** የሬፋን ኮከብ። ሬፋን ከአሕዛብ አማልክት አንዱ ሲሆን፥ አምላኪዎቹ ብሩህ ለሆነ ዘዋሪ ኮከብ (ፕላኔት) እየሰገዱ ያመልኩት ነበር። ስለዚህ የኮከቡ ስም «የሬፋን ኮከብ» ተባለ፤ አሞጽ 5፥26፤ ሐ.ሥ. 7፥43።

**ርስት፤** የከነዓን ምድር ለአብርሃምና ለዘሩ ርስት ሆኖ ተሰጠ፤ ዘፍ. 15፥8:18። ኢያሱ ምድሩን ለእስራኤል ሕዝብ አካፈለ። ይህን ርስት ከእግዚአብሔር እንደተቀበሉት ስላመኑ ለሌላ አይሸጡትም ነበር፤ ዘሌ. 25፥23፤ 1ነገ. 20፥3። «በኵር»፥ «ዋርሳ» ይመ.። እስራኤል ራሱ የእግዚአብሔር ርስት ይባላል፤ ዘዳ. 4፥20። ምእመናን የእግዚአብሔር ልጆች በመሆናቸው የርስቱ ተካፋዮች ናቸው፤ ሮም 8፥17፤ ገላ. 3፥29። በከነዓን የተመሰለውን በረከት ሁሉ ምእመናን ያገኛሉ፤ ዕብ. 11፥13-16። በተለይ ምእመናን የእግዚአብሔርን መንግሥትና በረከቱን ይቀበላሉ፤ ማቴ. 25፥34፤ 1ቆሮ. 6፥9:10፤ 15፥50። ምድርን (ማቴ. 5፥5)፤ መዳንን (ዕብ. 1፥14)፤ ክብርን (ሮም 8፥17:18) ይወርሳሉ። ርስታቸው ተጠብቆላቸዋልና መንፈስ ቅዱስ የርስታቸው መያዣ ነው፤ ኤፌ. 1፥14፤ 1ጴጥ. 1፥3-5።

**ርብቃ፤** የአብርሃም ወንድም፥ የናኮር የልጅ ልጅ፥ የላባ እኅት፤ ዘፍ. 22፥23፤ 24፥15:29። የይስሐቅ ሚስት ሆነች፤ ዘፍ. 24። በመጀመሪያ መካን ነበረች። ባልዋ ከጸለየላት በኋላ ያዕቆብንና ዔሳውን ወለደች፤ ዘፍ. 25፥20-26፤ ሮም 9፥10። መልከ መልካም፥ ትጉ፥ ልበ ቈራጥም ነበረች፤ ዘፍ. 24፥16:19:20:58፤ 26፥6-11። ያዕቆብን ስለ ወደደች አባቱን በማታለል በረከትን እንዲያገኝ አደረገች፤ ዘፍ. 25፥28፤ 27፥5-17። ከዔሳው ቍጣ ለመሸሽ፥ ከዘመዶችዋ ሚስትን ለመፈለግ አስባ ወደ ላባ እንዲሄድ አደረገች፤ ዘፍ. 27፥42-28፥5። አብርሃም ለመቃብር በገዛው ቦታ ተቀበረች፤ ዘፍ. 49፥31።

**ርኅራኄ፤** ምሕረት፥ ቸርነት፥ ለተጨነቀ ወይም ለተቸገረ ማዘንና ርዳታን መስጠት። እግዚአብሔር ርኅሩኅ ነው፤ መዝ. 103፥13፤ ኢሳ. 63፥9፤ ዮናስ 4፥11፤ ያዕ. 5፥11። አማኞችም ርኅሩኅ መሆን ያስፈልጋቸዋል፤ ኢሳ. 1፥17፤ ማቴ. 18፥23-35፤ ኤፌ. 4፥32፤ 1ጴጥ. 3፥8፤ 1ዮሐ. 3፥17።

**ርኩስ፤** መርከስ፤ ነውረኛ፥ አስጸያፊ መሆን፥ ግንኙነትን የሚያፈርስ። ኖኅ ከጥፋት ውሃ በኋላ ከንጹሐን እንስሳትና ወፎች ሁሉ ወስዶ መሥዋዕትን አቀረበ፤ ዘፍ. 8፥20። እግዚአብሔር ለኖኅ ተንቀሳቃሽ ሁሉ መብል እንዲሆንለት ሰጠው፤ ዘፍ. 9፥3። ከፍጥረት እስከ ሙሴ ድረስ ለመሥዋዕት ካልሆነ በቀር ንጹሕና ርኩስ ብሎ መለየት ያልነበረ ይመስላል። ነገር ግን በሙሴ ሕግ ሰው የሞተውን ሰው በድን በመንካት (ዘኁ. 19፥11)፥ እንደ ለምጽ ባሉት በሽታዎች (ዘሌ. 15)፥ ልጅ በመውለድ ወራት አርባና ሰማንያ ቀኖች (ዘሌ. 12፥1-5)፥ ከሥጋ ፈሳሽ ነገር ወይም ዘር ቢወጣ (ዘሌ. 15) ርኩስ ይባል እንደነበር ተጽፏል። አንድ ሰው ርኩስ በተባለበት ወራት ወደ ቤተ መቅደስ አይገባም ነበር፤ ዘሌ. 15፥31። በዚህ አንጻር ደግሞ ኃጢአት ሰውን እንደሚያረክስ ተነገረ፤ ኢሳ. 6፥5፤ ሕዝ. 18፥10-13። በአ.ኪ. ዘመን ግን ማናቸውም ነገር በራሱ ርኩስ አይባልም፤ ማር. 7፥19፤ ሮም 14፥14:20፤ 1ጢሞ. 4፥4። ከሰው ልብ የሚወጣ ኃጢአት እንጂ መብል፥ አንዳች ነገርን መንካት፥ በሽታ ወዘተ. ...አያረክስም፤ ማር. 7፥14-23፤ 1፥40:41። «ንጹሕ»፥ «ለምጽ» ይመ.



ርኩሳን እንስሳት

**ርኩስ መንፈስ፤** «ጋኔን» ይመ.

**ርኵሰት፤** የጥፋት ርኵሰት፤ አሳቡ አንጥያኮስ የኢየሩሳሌምን ቤተ መቅደስ በ165 ከክ.ል. ከማርከሱ ጋር ይያያዛል፤ ታሪኩ በዮሴፍ ወልደ ኮርዮን ተጽፏል፤ ዳን. 11፥31፤ 12፥11፤ ማቴ. 24፥15፤ ማር. 13፥14። በተጨማሪም የካቶሊክን 2ኛ መቃብያን 5፥11-6፥11 ይመ.። ክሊቃውንት አንዳንዶቹ የሮማውያን ወታደሮች የቄሣርን ባንዲራ ይዘው በ70 ዓ.ም. ወደ ቤተ መቅደስ በገቡ ጊዜ ይህ ትንቢት እንደተፈጸመ ያስተምራሉ። ሌሎች ደግሞ ትንቢቱ የዐመፅን ሰው (ሐሳዊ መሲሕን) እንደሚያመለክት ያስተምራሉ፤ 2ተሰ. 2፥1-4።

**ርዝመት፤** ዕብራውያን በዘንግ፥ በክንድ፥ በስንዝር፥ በጋት በሌላም የሰው አካል ይለኩ ነበር። በግሪክ አንድ ሰው ክንዶቹን ግራና ቀኝ ሲዘረጋ አርጊያ ይባላል፤ ይህንም መሠረታዊ መለኪያ አደረጉት። አንድ አርጊያና አራት ክንድ እኩል ናቸው። አንድ ምዕራፍ መቶ አርጊያ ነው። መቶ ሰማንያ ሜትር ይሆናል።

**ርግብ፤** ትንሽ ወፍ። ኖኅ የጥፋትን ውሃ መጕደል በርግብ አረጋገጠ፤ ዘፍ. 8፥8-12። ርግብ የውበት (መ.መ. 1፥15)፥ የኀዘን (ኢሳ. 59፥11)፥ የየዋህነት ምሳሌ ናት (ማቴ. 10፥16)። መንፈስ ቅዱስ በርግብ አምሳል በክርስቶስ ራስ ላይ አረፈ፤ ማቴ. 3፥16። «ወፎች» ይመ.



የሮማን ዛፍና ፍሬው

**ሮማን፤** አበባውና ፍሬው ቀይ፥ የፍሬው ጭማቂ ብዙ የሆነ፥ ቅርፊቱ ለመድኃኒት የሚጠቅም አንድ ዓይነት ዛፍ፤ ዘጸ. 28፥33፤ መ.መ. 6፥11። በሮማን ቅርጽ የቤተ መቅደስ መርበብ ተሠርቶ ነበር፤ 1ነገ. 7፥42።

**ሮማዊ፤** ሮም ገናና መንግሥት በነበረችበት ጊዜ አንድ ሮማዊ ዜግነት ያለው ሰው በሮም መንግሥት ውስጥ ልዩ መብት ነበረው። ሮማዊ ሲመረመር በጅራፍ አይገረፍም፥ የሞት ፍርድ ሲፈረድበት ይሰየፋል እንጂ አይሰቀልም ነበር፥ ለቄሣርም ይግባኝ የማለት መብት ነበረው። አንድ ሰው በሮማዊ ቤት በመወለድ፥ ዜግነትን በገንዘብ በመግዛት ወይም መንግሥቱን በማገልገል ሮማዊ ሊሆን ይችል ነበር። ጳውሎስ በሮማዊ መብቱ ተጠቅሟል፤ ሐ.ሥ. 16፥37-39፤ 22፥25-29፤ 23፥27፤ 25፥10-12።

**ሮማይስጥ፤** የሮማውያን ቋንቋ ማለት ነው፤ ጌታችን በምድር ሳለ የመንግሥት ቋንቋ ስለነበረ፥ በጌታችን መስቀል ላይ የተጻፈው ጽሕፈት በሮማይስጥ ቋንቋ ነበር፤ ሉቃ. 23፥38፤ ዮሐ. 19፥20። ፊደሉ የእንግሊዝኛን ፊደል ይመስላል። ብዙዎች የሮማይስጥ ቃላት በትውስት መልክ ወደ ግሪክ ገብተው በአ.ኪ. ይገኛሉ፤ ጥቂቶችም ከግሪክ ወደ ግእዝና ወደ አማርኛ ገብተዋል። ለምሳሌ ዲናር የሮማይስጥ ቃል ነው።

**ሮም፤** የሮም መንግሥት፤ በአ.ኪ. ዘመን «ሮም» ትባል የነበረችው ከተማ ዛሬ «ሮማ» ትባላለች። ከተማይቱ 753 ከክ.ል. እንደተቈረቈረች ይነገራል። የሮም መንግሥት መናገሻ ከተማ ነበረች። የሮም መንግሥት እየተስፋፋ ሄዶ ክርስቶስ በምድር በነበረበት ጊዜ ከእንግሊዝ አገር አንሥቶ እስራኤልን በመጨመር እስከ ዓረብ አገር ድረስ በዚያን ጊዜ የታወቀውን ዓለም ገዛ። ክርስቶስ ጲላጦስ ፊት የቀረበውና ጳውሎስም ወደ ቄሣር ይግባኝ ያለው እስራኤል ከሮም ግዛት አንድዋ በመሆንዋ ነበር፤ ማቴ. 27፥1:2፤ ሐ.ሥ. 25፥11።

በጳውሎስ ዘመን ሮም አንድ ሚሊዮን የሚያህሉ ነዋሪዎች የሚገኙባት በብዙ ትልልቅ ሕንጻዎች ያጌጠች ከተማ ነበረች። የሮም መንግሥት ጸጥታንና ፍርድን ለብዙ ሕዝብ ስለሰጠ ተወዳጅ ነበር (ሐ.ሥ. 17፥7)፥ ክርስቶስና ሐዋርያት ለሮም መንግሥት



የሮም መንግሥት የከተማ ኑሮ

አክብሮት ያሳዩ ነበር፤ ሉቃ. 20፥25፤ ሐ.ሥ. 24፥10፤ ሮም 13፥1-7፤ 1ጴጥ. 2፥13:14። ሆኖም ምእመናን ከቄሣር ይልቅ እግዚአብሔርን ስላከበሩ በሮም መንግሥት ስደት ደረሰባቸው፤ ብዙ ምእመናን በግፍ ተገደሉ። እንደ ቤ.ክ. ታሪክ ከሆነ በኔሮ ዘመነ መንግሥት በጳውሎስና በጴጥሮስ ላይ በሮም ከተማ የሞት ፍርድ ተፈረደባቸው።

በ395 ዓ.ም. ቴዎዶስዮስ የሚባል የሮም ንጉሠ ነገሥት በሞተ ጊዜ መንግሥቱ በምሥራቅና በምዕራብ ክፍሎች ተከፈለ። በ410 ዓ.ም. አላሪክ የሚባል የጠላት መሪ ሮምን ወግቶ አሸነፋት፥ ሥልጣንዋንም ሻረ። ከተማይቱ ግን እስከ ዛሬ ድረስ አለች፥ ዛሬም የኢጣሊያ ዋና ከተማ ናት። «ቄሣር»፥ «ገዥ» ይመ. ኀ. 7 ሀ።

**የሮም ቤተ ክርስቲያን፤** የሮምን ቤ.ክ. ያቋቋማት ማን እንደሆነ አልታወቀም። ሐዋርያው ጳውሎስ ነው ለማለት በቂ ማስረጃ የለም፤ ሮም 15፥20-24። ጴጥሮስ ሆነ ሌላም ሐዋርያ ያቋቋማት አይመስልም። መንፈስ ቅዱስ በጰንጠቆስጤ ቀን ሲወርድ የሮም ሰዎች በኢየሩሳሌም እንደነበሩ ተገልጧል፤ ሐ.ሥ. 2፥10። ከጴጥሮስ ስብከት ወንጌልን ሰምተው ወደ ሮም ያደረሱትና ቤተ ክርስቲያንን ያቋቋሙ እነርሱ ሳይሆኑ አይቀርም። እርግጡ ግን አልታወቀም።



የሮም መቅደስና የሮም ወታደሮች አርማ

**የሮም መልእክት፤** ይህ መልእክት ሐዋርያው ጳውሎስ በሮም ከተማ ለሚኖሩ ክርስቲያኖች የጻፈው ነው። በ58 ዓ.ም. ገደማ ተጻፈ። የተላከውም ከቆሮንቶስ ከተማ ነው። ጳውሎስ ወደ ሮም ሄዶ አያውቅም ነበር፤ እዚያም የነበረውን የክርስቲያን ማኅበር ያቋቋመ እርሱ አልነበረም፤ 15፥20-22። ወደ እስፔን ለመሄድ አሳብ ስለነበረው ሮም ከመድረሱ በፊት የሚያስተምረውን ወንጌል ሊገልጥላቸው ወደደ። በሮም ቤ.ክ. አይሁድና አሕዛብ አብረው ሲኖሩ የእስራኤል ሕዝብ ወንጌልን ባለመቀበላቸው በእግዚአብሔር ዕቅድ ላይ ብዙ ጥያቄ እንደተነሣ የሚጠቁሙ በመልእክቱ የሚገኙ ፍንጮች ጥቂቶች አይደሉም፤ በተለይ በም. 9-11። ይህ መልእክት ከሌሎች የጳውሎስ መልእክቶች የበለጠ ስለ ክርስቶስ ወንጌል ሰፋ ያለ ማብራሪያ ይሰጣል። ሆኖም ስለ ቤ.ክ.ና ስለ ዳግም ምጽአት ብዙ አሳብ አይገኝበትም።

«ጻድቅ በእምነት ይኖራል» የሚለው ዕንባቆም የተናገረው ቃል የዚህ መልእክት መሠረታዊ ጥቅስ ነው፤ 1፥17። ሰው በራሱ ጥረት ጻድቅ ስለማይሆን፥ ለኃጢአተኛ ጽድቅ ሆኖ የሚቈጠረው የእግዚአብሔር ጽድቅ ነው። ይህም ጽድቅ በክርስቶስ መሥዋዕትነት ለሚያምኑ ሁሉ ይሰጣል፤ 3፥11:24-25:28፤ 4፥3-5፤ 5፥1:8-9። ሰው በአዳም እንደሚሞት ሁሉ አማኝም በክርስቶስ ጻድቅና ሕያው ነው፤ 5፥19። አማኝ ከክርስቶስ ጋር አንድ እንዲሆን ተጠምቋልና አዲስ ሕይወት አለው፤ ከኃጢአት፥ ከሕግና ከሞት ኃይል ወጥቶ በአዲስ መንፈስ ይኖራል፤ 6፥3-5:14፤ 7፥6፤ 8፥2:14። እግዚአብሔር አማኙን አስቀድሞ ስላወቀው፥ ስለወሰነው፥ ስለጠራው፥ ስላጸደቀውና ስላከበረው አሁን ለአማኙ ተስፋ፥ ዋስትናና አለኝታ አለው፤ 8፥15-17:28-30:38-39። እግዚአብሔር ይህን ሁሉ ለክርስቲያኖች ካደረገ «ሕዝቡን (እስራኤላውያንን) ጥሏልን? የተሰናከሉ እስኪወድቁ ድረስ ነውን?» የሚሉት ጥያቄዎች ተነሥተዋል። መልሱ፥ 1ኛ. እግዚአብሔር ስለ ፍትሑ የማይጠየቅ፥ 2ኛ. እስራኤልን ባለማመናቸው የሚቈርጥ፥ 3ኛ. እንደ ምሥጢራዊ ዕቅዱ የአሕዛብንም ሆነ የእስራኤልን «ሙላት» (በእግዚአብሔር የተመረጡትን ሁሉ) የሚያድን ነው፤ 9፥20፤ 10፥1-4፤ 11፥5:12:15:25-26። አማኝ ይህን ሁሉ ተረድቶ ራሱን ለእግዚአብሔር እንዲያቀርብና የዓለምን አስተሳሰብና አካሄድ ትቶ በአእምሮ በመታደስ የተለወጠ ጠባይ እንዲኖረው ታዝዟል፤ 12፥1-2።

የሐዋርያው ዋና አሳብ የእግዚአብሔርን ጽድቅ የሚመለከት ሲሆን፥ ስለ እግዚአብሔር ልዕልናና ባሕርይ፥ ስለ ክርስቶስ ማንነትና ሥራ፥ ስለ መንፈስ ቅዱስ አካላዊነትና አሠራር፥ ስለ አይሁድና አሕዛብ፥ ስለ ጸጋና ሕግ፥ ስለ እምነትና ሥራ፥ ስለ መንፈስና ሥጋ የሰጠው ትምህርት በልዩ ልዩ አንቀጽ ድንገት ብቅ ሲል ይታያል። የመጽሐፉ አቀራረብ እንደ ትልቅ ወንዝ ውሃ ተያይዞ የሚፈስ ቢሆንም በመግቢያውና በመደምደሚያው መካከል 5 ታላላቅ ክፍሎችን ልናይ እንችላለን ፦

<u>መግቢያ</u>፤ የጳውሎስ ጥሪ፥ ወንጌልና ከሮም ቤ.ክ. ጋር የነበረው ግንኙነት፤ የመልእክቱ ዋና አሳብ፤ 1፥1-17።

<u>1. እግዚአብሔር ሰውን በቍጣ ኰነነ (ወይም ሰው በእግዚአብሔር ቍጣ ተኰነነ)፤</u> 1፥18-3፥20። አረማውያን(1፥18-32)፥ አይሁድ(ም.2)፥ ሰዎችም ሁሉ በኃጢአታቸው ምክንያት ከእግዚአብሔር ቍጣ በታች ናቸው፤ 3፥1-20።

<u>2. እግዚአብሔር ሰውን በጸጋ አጸደቀው (ወይም ሰው በእግዚአብሔር ጸጋ ጸደቀ)፤</u> 3፥21-7፥25። የእግዚአብሔር ጽድቅ፥ ሀ) በክርስቶስ ሞት ተገልጧል (3፥21-26)፥ ለ) በእምነት መንገድ ይሰጣል (3፥27-31)፥ ሐ) ለኃጢአተኛ ይቈጠርለታል (4፥1-12)፥ መ) በእምነት አማካይነት ይቈጠርለታል (4፥13-25)፥ ሠ) አማኞችን ወደ ብፅዕና ያደርሳል

(5፥1-11)፥ ረ) ከአዳም ፍርድ ነፃ ያወጣል (5፥12-21)፥ ሰ) ከኃጢአት ኃይል አርነት ያወጣል (ም. 6)፥ ሸ) ከሕግ ሥልጣን ይፈታል (ም.7)።

<u>3. እግዚአብሔር ሰውን በፍቅር አከበረው (ወይም ሰው በእግዚአብሔር ፍቅር ተከበረ)</u)፤ 8፥1-39። አማኝ ከኵነኔ ወጥቶ በመንፈስ ቅዱስ ኃይል በአዲስ ሕይወት ይኖራል (8፥1-17)፥ የማይጠፋውም ተስፋ ሲኖረው በአለኝታው መበረታታት ይገባዋል፤ 8፥18-39።

<u>4. እግዚአብሔር ሰውን በምሕረት መረጠው (ወይም ሰው በእግዚአብሔር ምሕረት ተመረጠ)</u>፤

9፥1-11፥36። እስራኤል ቢወድቅም የእግዚአብሔር ቃል አልተሻረም። እግዚአብሔር «የሚወደውን ይምረዋል፥ የሚወደውንም እልከኛ ያደርገዋል» (9፥18) የሚለውን የምዕራፍ 9ን የማጠቃለያ አሳብ ብናገኝም፥ እስራኤል ላለማመናቸው ኀላፊነት ያለባቸው ሲሆን ቤ.ክ. ግን ወንጌልን ለሁሉ ማብሠር አለባት፤ ም. 10። ከእስራኤል ውድቀት የተነሣ አሕዛብ ወደ ደኅንነት ደርሰዋልና መዳናቸው ለወደቁት እስራኤል የመዳን መንገድ ይሆናል። ስለዚህ የእግዚአብሔር ዕቅድ ለእስራኤልም ሆነ ለአሕዛብ ይፈጸማል፤ ም. 11።

5. <u>እግዚአብሔር ሰውን በልዕልና አደፋፈረው (ወይም ሰው በእግዚአብሔር ልዕልና ተደፋፈረ)</u>፤

12፥1-15፥13። ከክርስቶስ ወንጌል የተነሣ አማኝ፥ ሀ) በራሱ ሕይወት (12፥1-2)፥ ለ) በቤ.ክ. (12፥3-8)፥ ሐ) ከአማኞችና ከማያምኑት ጋር ባለው አኗኗር (12፥9-21)፥ መ) ባለ ሥልጣናትን በማክበር (ም. 13)፥ ሠ) የደከሙትን በመርዳት (14፥1-15፥13) አዲስ ሕይወትን መኖር አለበት።

<u>መደምደሚያ</u>፤ ጳውሎስ የተሰጠውን ተግባር ዓላማ ካሳየ በኋላ ኢየሩሳሌምን እንደሚጐበኝና ወደ እስፓን ለመሄድ በማቀዱ የሮም ቤ.ክ. በጕዞው እንደምትተባበር ተስፋ ያለው መሆኑን ገለጠ። ሰላምታ ለብዙ ሰዎች ካቀረበና ስለ ሐሰተኞች ማስጠንቀቂያ ከሰጠ በኋላ እግዚአብሔርን በመወደስ መልእክቱን ደመደመ፤ 15፥14-16፥27።

**ሮቤል፥ ሩቤን**፤ የስሙ ትርጕም «እነሆ ወንድ ልጅ!» ማለት ነው። ልያ ለያዕቆብ የወለደችለት በኵር ልጅ፤ ዘፍ. 29፥31:32። ከእስራኤል ነገዶች የአንዱ አባት ሆነ፥ በስሙ ነገደ ሮቤል ተብሎ ተሰየመ፤ ዘፍ. 46፥8:9፤ ዘኍ. 1፥4:5። ወደ ያዕቆብ ቁባት በመግባቱ አባቱን አሳዘነው፤ ዘፍ. 35፥22፤ 49፥3:4። ከዚህም የተነሣ ብኵርናው ለዮሴፍ ልጆች፥ ለኤፍሬምና ለምናሴ ተሰጠ፤ 1ዜ.መ. 5፥1፤ ዘፍ. 48፥5።

ሮቤል ለዮሴፍ ራራለት፤ ዘፍ. 37፥21:22:29:30። የሮቤል ነገድ እንደ ጋድ ነገድና እንደ ምናሴ ነገድ እኩሌታ፥ ከሙሴ እንደሰሙት ከዮርዳኖስ በስተምሥራቅ ርስት ተቀብለው ኖሩ፤ ዘኍ. 32። ካ. 3 ሸ። «ነገድ» ይመ.

**ሮብዓም**፤ የስሙ ትርጕም «ሕዝብ ይብዛ» ማለት ነው። የሰሎሞን ልጅ ነበረ፤ እናቱ አሞናዊቷ ናዕማ ነበረች። አባቱ ከሞተ በኋላ በኢየሩሳሌም ነገሠ፤ የእስራኤል ነገዶች ሁሉ እንዲያነግሡት በሴኬም ተሰበሰቡ። ሮብዓም ግን፥ አባቴ በጫንባችሁ ቀንበር ላይ እጨምራለሁ እንጂ አላቃልለውም ባላቸው ጊዜ አሥሩ ነገዶች የናባጥን ልጅ ኢዮርብዓምን በላያቸው አነገሡ፤ የሮብዓምን አስገባሪ ገደሉት። ሮብዓም ጦር ሠራዊቱን ሰበሰበ፤ ነቢዩ ሳማያ (ሸማያ) ግን፥ ይህ ነገር ከእግዚአብሔር ዘንድ ነውና አትውጡ አለ፤ 1ነገ. 11፥43-12፥24፤ 2ዜ.መ. 9፥31-11፥4። ሮብዓም በይሁዳና በብንያም ነገዶች ላይ ከ931-913 ከክ.በ. 17 ዓመት ነገሠ። መጀመሪያ ሲነግሥ በእግዚአብሔር መንገድ ሄደ በኋላ ግን ክፉ አደረገ፤ በአምስተኛው ዓመት የግብጽ ንጉሥ ሺሻቅ መጣበት፥ መዝገቡን ሁሉ ወሰደበት። ሮብዓም በእግዚአብሔር ፊት ሰውነቱን ካዋረደ በኋላ ሺሻቅ ሄደለት፤ 2ዜ.መ. 11፥5-12፥16፤ 1ነገ. 14፥21-31።

**ሰለባ**፤ ገዳይ ሰውን ከገደለ በኋላ ለማሳየት የሚወስደው ምልክት። መሣሪያ ገፍፎ ወይም ከሟቹ አካል አንድ ዓይነት ክፍል ቈርጦ ሲወስድ ሰለባ ይባላል፤ 1ሳሙ. 18፥25:27።

**ሰለጰዓድ**፤ አምስት ሴቶች ልጆች የነበሩት የምናሴ ነገድ ሰው፤ ዘኍ. 26፥33፤ ኢያሱ 17፥3፤ 1ዜ.መ. 7፥15። ሴቶች ልጆቹ ርስት እንውረስ ብለው ሙሴን ለመኑ፤ ተሰጣቸውም፤ ዘኍ. 27፥1-11፤ 36፥2-12።

**ሰሊሆም**፤ ለመጠመቂያ የሚሆን ውሃ የተጠራቀመበት ኵሬ። ከኢየሩሳሌም በደቡብ በኩል ያፌል በተባለው ጎጥ ሥር ይገኛል። ሕዝቅያስ ውሃውን ከግዮን ምንጭ በቦይ ወደዚህ አስገብቶታል። በፊት በኢየሩሳሌም ቅጥር ውስጥ ነበር። ዛሬ ግን በኋላ ከተሠራው ቅጥር ውጭ ነው፤ ኢሳ. 22፥9-11፤ «ግዮን» ይመ.። ሰሊሆም ማለት የተላከ ማለት ነው። ኢየሱስ የዕውሩን ዓይን በጭቃ ከቀባ በኋላ «ሂድና ታጠብ» ብሎ ወደ ሰሊሆም ላከው፤ ዮሐ. 9፥6-7። ካ. 8ሀ።

**ሰላም**፤ በስምምነትና በአንድነት አብሮ መኖር ማለት ነው። ደግሞ የዕረፍት ስሜት ነው። ሰዎች ሲገናኙ የሚለዋወጡት የሰላምታ ቃል፥ ወይም የንግግር መክፈቻ ቃል ነው፤ ዮሐ. 20፥19። እውነተኛ ሰላም የሚገኘው ሰው በክርስቶስ አምኖ፥ ከኃጢአቱ ነጽቶ፥ ከእግዚአብሔር ጋር ሲታረቅ ነው፤ ሮም 5፥1፤ ኤፌ. 2፥14-17። ሰላም የመንፈስ ፍሬ ነው፤ ገላ. 5፥22። እግዚአብሔር ለሚታመኑበት የራሱን ሰላም ይሰጣቸዋል፤ ኢሳ. 26፥3:4፤ ዮሐ. 14፥27፤ ፊል. 4፥6:7። አማኞች ከሰዎች ጋር በሰላም እንዲኖሩ ታዝዘዋል፤ ሮም 12፥18፤ 1ጴጥ. 3፥11። ክርስቶስ ሲመጣ ሰላም ይሰፍናል፤ ኢሳ. 9፥6:7፤ 11፥6-9። ሰላም የእግዚአብሔር መንግሥት ራሱ ነው፤ ሮም 14፥17። ክርስቶስ የሰላም አለቃ ይባላል፤ ኢሳ. 9፥6።

በስሕተት ትምህርት ምክንያት የቤ.ክ. ሰላም ይደፈርሳል፤ ነገር ግን እውነትን ለመደገፍ ሲባል ሐሰትን በመቃወም የመለያየት ሁኔታ ሊያጋጥም

ይችላል፤ 1ቆሮ. 11፥18-19። በክርስቲያኖች መካከል የሚፈጠር አለመግባባትም ሰላምን ከሚያደፈርሱ ምክንያቶች አንዱ ነው፤ 1ቆሮ. 1፥10-17።

**ሰላምታ**፤ የመገናኘትን ስሜት መግለጫ ቃል። ሰላምታ ብዙ ዓይነት አለው፤ ነህ. 2፥3፤ ማቴ. 10፥12፤ ማር. 12፥38፤ ሉቃ. 1፥29:41:44፤ ዮሐ. 20፥19። ሐዋርያት መልእክት ሲጽፉ በሰላምታ ጀመሩ፥ የሌሎችንም ሰዎች ሰላምታ አቀረቡ፤ ሮም 1፥1-7፤ 16፥21-23። ጉዳዩ አስቸኳይ ሲሆን (2ነገ. 4፥29፤ ሉቃ. 10፥4)፥ ወይም ከአንዳንድ ስሕተት ለመራቅ ሰላምታ አለመስጠት ይቻላል፤ 2ዮሐ. 10:11። ሰላምታ በመሳሳም (ማቴ. 26፥49፤ ሮም 16፥16)፤ እጅ ለእጅ በመጨባበጥ (ገላ. 2፥9) ይሰጣል።

**ሰላጢን**፤ እንደ እንካሴ ያለ ረዥም ሹል መውጊያ፤ ኢዮብ 39፥23፤ 41፥21።

**ሰልማን**፤ ምናልባት የአሦር ንጉሥ ሰልምናሶር ይሆናል፤ ሆሴዕ 10፥14።

**ሰሎሜ**፤ የክርስቶስን ስቅለት ከተመለከቱትና በትንሣኤው ዕለት ወደ መቃብሩ ከሄዱት ሦስት ሴቶች አንድዋ፤ ማር. 15፥40፤ 16፥1።

**ሰሎም**፤ 1. ከኢዩ ዘሮች መካከል ከነገሡት የመጨረሻው፥ ዘካርያን ገድሎ በሰማርያ የነገሠ 16ኛው የእስራኤል ንጉሥ። በግምት 745 ከክ. ል. አንድ ወር ከነገሠ በኋላ ተገደለ፤ 2ነገ. 15፥10-15። 2. የይሁዳ ንጉሥ ኢዮአክስ በዚህ ስም ተጠርቷል፤ 1ዜ.መ. 3፥15፤ ኤር. 22፥11።

**ሰሎሞን**፤ ሰላማዊ ማለት ነው። ከተባበረው የእስራኤል መንግሥት ሦስተኛና የመጨረሻ ንጉሥ፥ የዳዊትና የቤርሳቤህ ልጅ፤ 2ሳሙ. 12፥24። ዳዊት በሸመገለ ጊዜ ንጉሥ ለመሆን ተቀባ፤ 1ነገ. 1። አብያታርን፥ ሳሚን፥ አዶንያስንና ኢዮአብን ተበቀላቸው፤ 1ነገ. 2። የፈርዖንን ልጅ አገባ፤ 1ነገ. 3፥1። አስተዋይ ልቡና እንዲያገኝ ለመነ፥ በጥበቡም የታወቀ ሆነ፤ 1ነገ. 3፥5-28፤ 10፥1-10፤ 2ዜ.መ. 1፥3-12። በጢሮስ ንጉሥ በኪራም እርዳታ ቤተ መቅደስንና ቤተ መንግሥቱን አነጸ፤ 1ነገ. 5-8፤ 2ዜ.መ. 2-7። ለሕንጻ ሥራዎች ሠራተኞችን መለመለ፤ 1ነገ. 5፥13-17፤ 9፥19-21። ስፊ በሆነ ንግዱ በጣም በለጸገ፤ 1ነገ. 10፥11-29። ስለ ዕፀዋትና እንስሳት ብዙ ዕውቀት ነበረው፤ 1ነገ. 4፥33:34። በዘመነ መንግሥቱ ስለ ሥነ ጽሑፍ ትልቅ እንቅስቃሴ ተደረገ። ስለ «ጥበብ» የሚናገሩ አንዳንድ ቅዱሳት መጻሕፍትን እርሱ እንደጻፋቸው ይታመናል፤ ምሳ. 1፥1፤ መ.መ. 1፥1፤ «ተግሣጽ» ይመ.

ብዙ ሚስቶችን አገባ፤ እነርሱም የባዕድ አምልኮ ወደ እስራኤል እንዲገባና ሰዎች እንዲከታተሉት አደረጉ። በዚህም ሰሎሞን እግዚአብሔርን አሳዘነው፤ 1ነገ. 11። ከሞተ በኋላ የሰሜን ዐሥር ነገዶች ልጁ ሮብዓም እንዳይነግሥ ተቃወሙና ቀድሞ ከሰሎሞን በታች አለቃ የነበረው ኢዮርብዓምን መረጡ። ሰሎሞን ሲሞት የመንግሥቱ በሁለት መከፈል፥ በሀብቱና በዕውቀቱ ዝነኛ ቢሆንም በአስተዳደር በኩል ጨቋኝ መሆኑን ያመለክታል፤ 1ነገ. 12፥4። በጠቅላላው ታሪኩ ከ1ነገ. 1-11 እና ከ1ዜ.መ. 22 - 2ዜ.መ. 9 ተጽፎ ይገኛል። የሰሎሞን ክብር፥ ጥበብና መንግሥት ገናና ነበረ፤ ሆኖም ከእርሱ የሚበልጠው ክርስቶስ መጥቷል፤ ማቴ. 6፥29፤ 12፥42።

**ሰማ**፤ ሰው ብዙ ዓይነት ድምፅ ይሰማል፥ ሲሰማም ቃሉን ወዲያው ሊያስተውለው ወይም ላያስተውለው ይችላል፤ ዘፍ. 3፥8-10፤ ሐ.ሥ. 9፥7፤ 22፥9። ሰው መጥፎ ወሬ ቀጥተኛ ባልሆነ መንገድ ቢሰማ እጅግ ያዝናል፤ 1ሳሙ. 2፥23። እግዚአብሔር የሰዎችን ችግር፥ ሐዘን፥ ምስጋናና ልመና ሲመለከት ሰማ ይባላል፤ ዘጸ. 2፥24፤ 3፥7።

**ሰማርያ**፤ የጠባቂ ግንብ ማለት ነው። ከኢየሩሳሌም በስተሰሜን 65 ኪ.ሜ. ርቆ የሚገኝ ከተማ። ዛሬ ሄሮድስ በሰየመው ስም ሰባስቴ ይባላል። የእስራኤል ንጉሥ ዘንበሪ ተራራውን ገዝቶ ከተማ ሠራበት። መናገሻና መስገጃም አደረገው፤ 1ነገ. 16፥24:32። ከዝሆን ጥርስ የተሠራ የአክዓብ ቤት ፍርስራሽ (1ነገ. 22፥39)፥ ደግሞም የንጉሥ አልባሽና ደጋፊ የነበረው አለቃ ተረግጦ የሞተበት የበር ፍርስራሽ ተገኝቷል፤ 2ነገ. 7፥19-20። የሰሜኑ መንግሥት አንዳንድ ጊዜ ሰማርያ እየተባለ ይጠራ ነበር፤ 1ነገ. 13፥32፤ አሞጽ 3፥9። በአ.ኪ. ዘመን በገሊላና በይሁዳ መካከል ያለው አገር ሰማርያ ይባል ነበር፤ ዮሐ. 4፥4፤ ሐ.ሥ. 1፥8። ከ. 4 ሀ። «ሳምራውያን» ይመ.



በነገሥታት ዘመን የሰማርያ የአዕማድ ራሶች

**ሰማዕት**፤ ምስክር ማለት ነው። በሃይማኖቱ ምክንያት የተገደለ ሰማዕት ይባላል፤ ሐ.ሥ. 22፥20።

**ሰማይ**፤ ከምድር በላይ ያለው ሁሉ፤ ዘፍ. 1፥1፤ ማቴ. 5፥18። እግዚአብሔር ስለ ልዕልናው በሰማይ ይኖራል፤ ዘዳ. 26፥15፤ ማቴ. 5፥48። መላእክትም በሰማይ ይገኛሉ፤ ማር. 13፥32። ምእመናን በሰማይ ርስት አላቸው፤ 1ጴጥ. 1፥3-5፤ አሁንም በሰማያዊ ስፍራ ይገኛሉ፤ ኤፌ. 2፥6-7፤ 6፥12። አንዳንድ የአይሁድ ሊቃውንት ሰባት ሰማያት እንዳሉ ያስተምራሉ። በእነርሱ አስተሳሰብ ገነት ሦስተኛው ሰማይ ይመስላል፤ ነህ. 9፥6፤ 2ቆሮ.

12፥2-4። ሆኖም የአ.ኪ. ጸሐፊዎች ይህን ትምህርት የተቀበሉት አይመስልም። አንዳንድ ጊዜ ሰማይ፥ አንዳንድ ጊዜ ሰማያት ይላሉ፤ ነገር ግን የአሳብ ልዩነት አይታይባቸውም። በዓለም መጨረሻ አዲስ ሰማይና አዲስ ምድር ይገለጣሉ። ይህም እንዴት ያለ እንደሚሆን አናውቅም፤ ነገር ግን እንደ እግዚአብሔር ፈቃድ ስለሚሆን ጕድለት አይኖረውም፤ ኢሳ. 65፥17፤ 66፥22፤ 2ጴጥ. 3፥10-13፤ ራእ. 21፥1-3። «መንግሥተ ሰማያት» ይመ.

**ሰምርኔስ (እዝሚር)፤** በጥንት ጊዜ በትንሹ እስያ ምዕራብ የነበረች ወደብና ከተማ። የታወቀች ቤ.ክ. በሰምርኔስ ተቋቁማ ነበር። ጳውሎስ በኤፌሶን ሳለ የተመሠረተች ይመስላል፤ ሐ.ሥ. 19፥10፤ ራእ. 1፥11፤ 2፥8-11። ዛሬ እዝሚር ይባላል።

**ሰሞን፤** የካህናት የአገልግሎት ተራ ሳምንት። ዳዊት ካህናት በየሳምንቱ ተከፋፍለው በተራ በሃያ አራት ክፍሎች እንዲያገለግሉ አዘዘ፤ 1ዜ.መ. 24፤ ሉቃ. 1፥8።

**ሰራኩስ፤** ከኢጣልያ አገር በስተደቡብ በታላቁ ባሕር ውስጥ የምትገኘው የሲሲሊ ደሴት ከተማ። ጳውሎስ ታስሮ ወደ ሮም ሲሄድ መርከቡ ሦስት ቀን በሰራኩስ ዐረፈ፤ ሐ.ሥ. 28፥12። ካ. 7 ሠ።

**ሰርዴስ፤** በጥንት ዘመን ልድያ በተባለች ክፍለ ሀገር የነበረች ዋና ከተማ። በሮም መንግሥት ዘመን እንደ ቀድሞው ዘመን ትልቅ ከተማ አልነበረችም። በሥነ ጥበብ የታወቀች ነበረች። ጳውሎስ በኤፌሶን ሳለ ቤ.ክ. በሰርዴስ የተመሠረተች ይመስላል፤ ሐ.ሥ. 19፥10፤ ራእ. 1፥11፤ 3፥1-6። ዛሬ ትንሽ መንደር በቦታው ይገኛል። ካ. 7 ሰ።

**ሰርድዮን፥ ሰርዲኖን፤** የደም ዐይነት ቀለም ያለው ቀይ የከበረ ድንጋይ፤ ዘጸ. 28፥17፤ ራእ. 4፥3። «የከበሩ ድንጋዮች» ይመ.

**ሰርዶንክስ፤** የከበረ ድንጋይ። ዓይነቱ ነጭና ቡና መልክ ነው፤ ግን ከነጩ ቡናው ዓይነት ይበዛል፤ ራእ. 21፥20። «የከበሩ ድንጋዮች» ይመ.

**ሰርግ (የጋብቻ በዐል)።** በመ.ቅ. ስለ ልዩ ልዩ ሰዎች ሰርግ እናነባለን። የሰርግ ሥነ በዐል እንደ ዘመኑና እንደ አገሩ ባህል የተለያየ ነበር፤ ዘፍ. 29፥21-26፤ መሳ. 14፤ መዝ. 45፤ ማቴ. 22፥1-14፤ 25፥1-13፤ ዮሐ. 2፥1-11። ሰርግ ትልቅ ደስታ ነውና ሙሽራው ሙሽሪትን ወደ ቤቱ ሲወስድ ሰዎች ልዩ ልዩ ልብስ እየለበሱ በዐሉን በትልቅ ድግስ በዘፈንና በጨዋታ ያከብሩት ነበር። በዚህ አንፃር ክርስቶስ ሁለተኛ ሲመጣ የሚደረገው ደስታና ክብር በሰርግ ይመስላል፤ ራእ. 19፥7-9። «ጋብቻ» ይመ.

**ሰርፍ፤** በዙሪያው ዘርፍ ያለበት ጌጠኛ ያልጋ ልብስ፥ ምንጣፍም ሊሆን ይችላል፤ ምሳ. 7፥16።

**ሰሳብሳር፤** ቂሮስ የሾመው የኢየሩሳሌምን ቤተ መቅደስ መሠረት የጀመረ መስፍን፤ ዕዝ. 1፥8:11፤ 5፥14:16። ሰሳብሳርና ዘሩባቤል የአንድ ሰው ስሞች እንደሆኑ የሚያስቡ አሉ፤ ዘካ. 4፥9።

**ሰቅል፤** የጥንት የክብደት መለኪያ። የንጉሥ (2ሳሙ. 14፥26)፥ የሕዝብ (1ሳሙ. 17፥5)፥ የመቅደስ ሰቅሎች ነበሩ፤ ዘጸ. 30፥13። «ክብደት» ይመ.



ሰቅልና ግማሽ ሰቅል

**ሰቅሰቅ፤** እንደ ወንፊት የተታታና የተጠላለፈ የመስኮት መዝጊያ፤ መሳ. 5፥28።

**ሰቆቃወ ኤርምያስ፤** ሰቆቃው ማለት ሙሾ፥ ልቅሶ ማለት ነው። ጸሐፊው ኤርምያስ መሆኑና አለመሆኑ አልተረጋገጠም። ይሁን እንጂ ብዙ ሊቃውንት ኤርምያስ ነው ይላሉ። በመጽሐፉ ውስጥ የጸሐፊው ስም አይገኝም፤ እንዲሁም በዕብራይስጥ በመጽሐፉ አርእስት የኤርምያስ ስም አልተጠቀሰም። ሆኖም ጸሐፊው እንደ ኤርምያስ፥ ኢየሩሳሌምን የሚወድ፥ ውድቀትዋን አይቶ ያዘነና በሥቃይዋ የተካፈለ ሰው መሆኑ አያጠራጥርም።

አምስቱ ምዕራፎች አምስት የሐዘን ሙሾዎች ናቸው። በም. 1፤2፤4 እያንዳንዱ ቍጥር የሚጀምረው በሃያ ሁለቱ የዕብራይስጥ ፊደላት ሲሆን፥ ፊደሎቹም ቅደም ተከተላቸው ተጠብቋል። በም. 3 ፊደላቱ የሚለዋወጡት በየሦስት በየሦስት ቍጥር ነው። እነዚህም ፊደላት በአማርኛ መ.ቅ. ተጽፈው ይገኛሉ (አሌፋት ይመ.)።



አንድ ሰው ስለ ኢየሩሳሌም መፍረስ ሲያለቅስ

ይህም መጽሐፍ የመከራንና የሥቃይን መራራነት ሲገልጽ እግዚአብሔር በፍርዱ ጻድቅ

መሆኑን ይመሰክራል፤ 1፥18። በድለናልና ፈጽሞ ያልጠፋነው ከምሕረቱ የተነሣ ነው (3፥22)፤ በመከራ ጊዜ የእግዚአብሔርን ማዳን ተስፋ ማድረግ መልካም ነው ይላል፤ 3፥26።

**ሰባቱ ሱባዔ**፤ «በዓላት» ይመ.

**ሰባቱ ከዋክብት**፤ አንድ ላይ የተሰበሰቡትና እጅግ ደምቀው የሚታዩት ሰባት ከዋክብት፤ ኢዮብ 38፥31፤ አሞጽ 5፥8።

**ሰባኪ፤ ስብከት**፤ የክርስቶስ የመጨረሻ ትእዛዝ «ወንጌልን ለፍጥረት ሁሉ ስበኩ» ይላልና (ማር. 16፥15)፥ ስብከት በጌታ የታዘዘ ሥራ ነው። አንድ ሰው በቤ.ክ. ውስጥ ወይም በውጭ የእግዚአብሔርን ቃል ካስተማረ ሰባኪ ይባላል። ይህም ከእግዚአብሔር በቤ.ክ. በኩል ሲላክ ነው። በአ.ኪ. ብዙ ጊዜ «ሰበከ» ማለት ያላመኑትን ለማሳመን የወንጌልን ቃል ተናገረ ማለት ነው፤ ሮም 10፥14፤ 15፥20። ምእመናን ሁሉ የክርስቶስ ምስክሮች እንዲሆኑ ተጠርተዋል፤ በተለይም ባላመኑት መካከል ወንጌልን ለመስበክ እንደ ፊልጶስ የተጠሩ አሉ፤ ሐ.ሥ. 21፥8፤ ኤፌ. 4፥11። በቤ.ክ. ውስጥ የሚያስተዳድሩ እንደ ጢሞቴዎስ የወንጌል ሰባኪነትን ሥራ ጨምረው መሥራት ይገባቸዋል፤ 2ጢሞ. 4፥5። «የቤተ ክርስቲያን አስተዳደር» ይመ.

**ሰብአ ሰገል**፤ የጥበብ፥ የዕውቀት ሰዎች ማለት ነው። ከጥንት ጀምሮ በዓለም ሕዝብ መካከል ከዋክብትን የሚመረምሩ ጠቢባን ነበሩ፤ ዳን. 1፥3:4። «ኮከብ» ይመ.። ማቴዎስ ከምሥራቅ መምጣታቸውን እንጂ ብዛታቸውንና አገራቸውን፥ ስማቸውንና ያመጡትን ስጦታ ትርጕም፥ መምጣታቸውም የትንቢት ፍጻሜ መሆኑን አይገልጥም። እግዚአብሔር የገለጠላቸውን ተከታትለው ለክርስቶስ ሰገዱ፤ ካላቸውም የተሻለውን ስጦታ አቀረቡለት፤ ማቴ. 2፥1-12። ሆኖም በመዝ. 72፥9-15 እና በኢሳ. 60፥6፤ 49፥23 ላይ ለተነገረው ትንቢት ፍጻሜ እንደሆነ ብዙ ሊቃውንት ይተረጕማሉ።

**ሰነፍ**፤ እግዚአብሔርን የማያምን፥ ሰውን የማይረዳ፥ ለራሱ ምቾት የሚኖር በጠቅላላው በጠባዩ የተበላሸ ማለት ነው፤ 1ሳሙ. 25፥25፤ መዝ. 14፥1፤ ምሳ. 15፥2፤ መክ. 10፥14፤ ኢሳ. 32፥6፤ ሉቃ. 12፥20።

**ሰናክሬም**፤ ከ705-681 ከክ.በ. የነገሠ የአሦር ንጉሥ። በሕዝቅያስ ዘመን መንግሥት ይሁዳን ወረረ፤ 2ነገ. 18፥13፤ ኢሳ. 36፥1። ሕዝቅያስን ከባድ ግብር አስገበረ (2ነገ. 18፥14-16)፥ በኋላም ጦር ሠራዊቱ በእግዚአብሔር መልአክ ስለ ተቀሠፈ ኢየሩሳሌምን ለመያዝ አልቻለም፤ 2ነገ. 19፥35። ስለ ውጊያውና ስለ መንግሥቱ መስፋፋት የሚናገር ጽሑፍ ከጭቃ በተሠራ ሸክላ ላይ ተጽፎ ተገኝቷል።

**ሰናዖር**፤ በባቢሎን ዙሪያ ያለ ሰፊ ሜዳና አገር፤ ዘፍ. 10፥10፤ ዳን. 1፥2። «የባቢሎን ግንብ» ይመ.



ሰናክሬም በሁለት አማልክት መካከል እንደቆመ የሚያሳይ ማኅተም

**ሰናፊል**፤ ሰፊና ረጅም ሱሪ፤ ዳን. 3፥21።

**ሰናፍጭ**፤ የጕመን ዓይነት፥ ፍሬው ትንንሽ ቁመቱ ግን ረጅም የሆነ፥ አፍንጫን የሚሰነፍጥና የሚለበልብ፥ የሚያስለቅስ ተክል። የእግዚአብሔር መንግሥት ተመስሎበታል፤ ማቴ. 13፥31፤ 17፥20።

**ሰን**፤ ከነሐስና ከመዳብ ከሌላም ማዕድን የሚሠራ እንደ ማንቈርቈሪያ ያለ መታጠቢያ። አብዛኛውን ጊዜ ሰንና ብርት ይባላል። ብርት ማስታጠቢያው፥ ሰን ውሃ መያዣው ነው፤ ሰሎሞን ዐሥር ሰኖች ለቤተ መቅደስ አገልግሎት አሠርቶ ነበር፤ 1ነገ. 7፥38:39።

**ሰንበር**፤ በበትር ከመመታት የተነሣ በአካል ላይ የሚታይ ምልክት። ከሸክላ፥ ከእንጨትና ከቀንድ ከልዩ ልዩ ማዕድናትም በሚሠሩ ዕቃዎች ላይ በመስመር ዓይነት የሚደረግ የቅርጽ ጌጥ ሰንበር ይባላል፤ 1ነገ. 7፥28:35:36።

**ሰንበት፥ ሰንበታት**፤ በዕብራይስጥ የቃሉ ትርጕም ማቆም፤ መተው ማለት ነው። እስራኤል ሰባተኛውን ቀን ለእግዚአብሔር እንዲቀድሱት በዐሥርቱ ቃላት ታዝዘዋል፤ ዘጸ. 20፥8-11። ለሰው ዕረፍት ያስፈልጋል። ከዚህም በላይ ሰንበት በእግዚአብሔርና በሕዝቡ መካከል የቃል ኪዳን ምልክት ነው፤ ዘጸ. 31፥17። በዚህም ምክንያት ሰንበትን አለማክበር ከባድ ቅጣትን ያስከትል ነበር፤ ዘኍ. 15፥32-36። ሰንበት የእግዚአብሔር ሥራ እንዲታወስ ያደርጋል። በመጀመሪያ እግዚአብሔር ስድስት ቀን ሠርቶ እንዳረፈ ሁሉ፥ ሰውም በዚህ ዓለም ሠርቶ ወደ ዘለዓለም ዕረፍት እንደሚገባ ያመለክታል፤ ዘፍ. 2፥2:3፤ ዘጸ. 20፥8-11። እስራኤላውያን ወደ ዕረፍት አገራቸው ሲደርሱ ዐሠርቱ ቃላት በድጋሚ ተነገራቸው። ከዚህም ላይ ሰንበት እግዚአብሔር እስራኤልን ከግብጽ ባርነት እንዳወጣቸው ያመለክታል፤ ዘዳ. 5፥12-16። እስራኤል ቀኑን በሚገባ ባለማክበራቸው በነቢያት ተወቅሰዋል (ሕዝ. 20፥12-16፤ አሞጽ 8፥6) እንዲያከብሩትም ተስፋ ተሰጥቷቸዋል፤ ኢሳ. 56፥2-4፤ 58፥13:14። ነህምያ ሰንበትን አስከብሯል፤ ነህ. 10፥31፤ 13፥15-22። ኢየሱስ ሰንበትን አክብሯል (ሉቃ. 4፥16)፥ የፈሪሳውያንን

የሰንበት አከባበር ግን ተቃውሟል። እነርሱ ቀኑ እንዲከበር ብቻ እሸት ከመቅጠፍ፥ ድውይ ከመፈወስ እስኪከለከሉ ድረስ ብዙ ሕግና ወግ ደንግገው ነበር። ክርስቶስ ግን ከሰው ወግና ሥርዓት ምሕረት እንደሚበልጥ ራሱም የሰንበት ጌታ መሆኑን አስተማረ፤ ማቴ. 12፥1-14።

ከሳምንቱ በመጀመሪያው ቀን ክርስቶስ ስለተነሣ ተከታዮቹ በዚህ ቀን መሰብሰብ ጀመሩ። አይሁድና ክርስቲያኖች እየተራራቁ፥ ወንጌልም በአሕዛብ ዘንድ እየተስፋፋ ሲሄድ ምእመናን የእግዚአብሔርን ቀን በሳምንቱ በመጀመሪያው ቀን አከበሩ፥ ቀኑም የጌታ ቀን ተባለ፤ ሉቃ. 24፥1፤ ሐ.ሥ. 20፥7፤ 1ቆሮ. 16፥2፤ ራእ. 1፥10። ይህም ከቀኑ መሠረተ አሳብ ጋር ይስማማል፤ ምክንያቱም ክርስቶስ በትንሣኤው ደኅንነትን ፈጽሟል። ምእመናንም በሥራቸው ሳይሆን፥ ክርስቶስ በፈጸመው ሥራ ወደ ዘለዓለም ዕረፍት ገብተው መዳናቸውን በመልካም ሥራቸው ለማሳየት ይተጋሉ፤ ዕብ. 4፥1-11፤ 10፥25።

**ሰንበት፤** (መጀመሪያ፥ አራተኛ ሰንበት)፤ ዳዊት የሚዘምሩ ካህናትን በሰሞን እንዳዘጋጀ ሁሉ፥ የሚዘመረውን መዝሙርና የሚዘመርበትንም ቀን በክፍል በክፍል አድርጎ መድቦ ነበር። ለምሳሌ ወር በገባ በመጀመሪያው ሰንበት መዝ. 24፥ ወሩ ሲያልቅ ወይም በአራተኛው ሰንበት መዝ. 94 ይዘመር ነበር ማለት ነው፤ መዝ. 24፤ 94 አርእስት።

**የሰንበት መንገድ፤** ሰንበት እንዲከበር በፈሪሳውያን ወግ እስከ አንድ ኪ.ሜ. ያህል መሄድ የተፈቀደ ነበር፤ ሐ.ሥ. 1፥12። በመሠረቱ በሰንበት ቀን የግል ፈቃድን ለመፈጸም መንገድ መሄድ አልተፈቀደም፤ ኢሳ. 58፥13።

**ሰንባላጥ፤** ነህምያን የተቃወመው አንድ የሰማርያ ባለ ሥልጣን፤ ነህ. 2፥10:19:20፤ 4፥1-3:7:8፤ 6፥1-14፤ 13፥28።

**ሰንደል፤** የተጣራ ሽቱ ያለው እንጨት። ለቤት መከታ፥ ለዜማ መሣሪያ ይሆናል፤ 1ነገ. 10፥11:12።

**ሰንፔር፤** ሰማያዊ ቀለም ያለው፥ አልፎ አልፎ ወርቅ መሳይ ያለበት የከበረ ድንጋይ፤ ዘጸ. 24፥10፤ ራእ. 21፥19።

**ሰኰና፤** ተረከዝ፥ ታችኛው የእግር ክፍል፤ ዘፍ. 3፥15፤ 25፥26፤ 49፥17፤ ኢዮብ 18፥9። ሰው ወይም እንስሳ ለጉዳት ሊጠቀምበት ይችላል፤ መዝ. 41፥9፤ ዮሐ. 13፥18። ሰኰናው ያልተሰነጠቀ እንስሳ ርኩስ ሲባል፥ ሰኰናው የተሰነጠቀ ርኩስ እንዳይደለ በብ.ኪ. ተገልጧል፤ ዘሌ. 11፥26-27።

**ሰው፤** እግዚአብሔር ሰውን ከምድር አፈር አበጀው፤ የሕይወትንም እስትንፋስ እፍ አለበት (ዘፍ. 2:7)፤ ስለዚህ ሰው ሥጋና ነፍስ (መንፈስ) ነው። ሴትንም ከወንድ ፈጠረ፤ ዘፍ. 2፥21:22። መ.ቅ. እግዚአብሔር ሰውን እንዴት እንደፈጠረው ከዚህ የበለጠ መግለጫ አይሰጥም። ሰው አስቀድሞ ሕይወት ካለው እንስሳ ሳይሆን ግዑዝ ከሆነ ከዐፈር መፈጠሩን መ.ቅ. በግልጥ ያስተምራል። ሰው ከእንስሳት ፈጽሞ የተለየ መሆኑ በእግዚአብሔር መልክና ምሳሌ በመፈጠሩ ይታያል፤ ዘፍ. 1፥26፤ 2፥7፤ 3፥19። ብዙ ክርስቲያኖች እግዚአብሔር ሰውን በአንድ ቀን እንደፈጠረ ያምናሉ፤ ሌሎች ግን መ.ቅ.ን በዘመናዊ ሳይንስ ከሚገኘው ከአዝጋሚ ለውጥ መላምት አሳብ ጋር ለማዛመድ እግዚአብሔር ሰውን በረጅም ጊዜ ውስጥ ፈጠረው ሲሉ ይሰማሉ።

የሰው ታሪክ ሦስት ደረጃዎች አሉት፤ እነርሱም መፈጠሩ፥ በኃጢአት መውደቁና ከኃጢአት ውድቀት መነሣቱ ናቸው። የሰው ደኅንነትም ሁለት ደረጃ አለው፤ አሁን ነፍሱ ድናለች፤ በኋላም ዳግም ምጽአት ጊዜ ደግሞ ሥጋው ከነፍሱ ጋር በትንሣኤ ይድናል፤ 1ቆሮ. 15፥20-22።

ሰዎች በልዩ ልዩ አገር በአንድ ጊዜ ተፈጠሩ የሚሉ አሉ። መ.ቅ. ግን ከአዳም ከተገኙት በቀር ሌሎች ሰዎች እንደነበሩ አይገልጥም፤ «የትውልድ ሐረግ» ይመ.

የሰው መንፈሳዊ ሁኔታ አንዳንድ ጊዜ ነፍስ፥ በሌላ ጊዜ መንፈስ ይባላል። በ1ተሰ. 5፥23 እና በዕብ. 4፥12 ነፍስና መንፈስ የተለያዩ ይመስላሉ። በሌሎች ጥቅሶች ግን መንፈስና ነፍስ የሰውን መንፈሳዊ ሁኔታ ከሁለት አቅጣጫ እንደሚያመለክቱ ይታያል። በመ.ቅ. ውስጥ በአንዳንድ ቦታ ሰው ሥጋና ነፍስ (ማቴ. 6፥25፤ 10፥28)፥ በሌላ ቦታ ሥጋና መንፈስ (ማር. 14፥38፤ 1ቆሮ. 5፥3:4) እንደሆነ ተገልጧል፤ ዕብ. 12፥23 እና ራእ. 6፥9 ያነጻጽሩ። ሰው ኃጢአት በመሥራት ሞተ፤ ሮም 6፥23። ክርስቶስን በማመን ግን ይድናል፤ ሮም 3፥21:22።

**የሰው ልጅ፤** ሕዝቅኤልና ዳንኤል የሰው ልጅ ተብለው ተጠሩ፤ ሕዝ. 2፥1፤ ዳን. 8፥17። ዳንኤል በራእይ የሰው ልጅ የሚመስል የዓለማትን መንግሥትና ክብር ሁሉ ለዘለዓለም ሲቀበል አየ፤ ዳን. 7፥13:14። ክርስቶስ ስለ ራሱ ሲያስተምር ብዙ ጊዜ «የሰው ልጅ» በሚለው ስም ይጠቀም ነበር። በዚህ ስም የመሢሕነቱን ሥራ ገለጠ፤ ሉቃ. 9፥26፤ 19፥10። «ኢየሱስ»፥ «መሲሕ» ይመ.

**ሰውነት፤** ጠቅላላ የሰው ሁኔታ ሥጋና ነፍስ፥ ሰው መሆን ማለት ነው፤ ማቴ. 5፥29፤ 6፥22። የውስጥ ሰውነት የሰውን መንፈስ (ሮም 7፥22፤ ኤፌ. 3፥16:17)፥ የውጭ ሰውነት ሥጋን ያመለክታል፤ 2ቆሮ. 4፥16። «አካል» ይመ.

**በሰው የሚነግዱ፤** ባሪያ ፈንጋይ፥ ሰውን አፋኝ። በሙሴ ሕግ ሰውን ስለ መግዛትና መሸጥ ተጽፏል፤ ዘጸ 21፥2-11። በአ.ኪ.ም ዘመን ሮማውያን ሰውን በመግዛትና በመሸጥ ታላቅ ንግድ ነበራቸው። ሆኖም ይህ በአ.ኪ. ቃል አስጸያፊ ኃጢአት ተብሏል፤ 1ጢሞ. 1፥9-11። «ባሪያ» ይመ.

**ሰዓት፤** እስራኤላውያን ፀሐይ ወጥታ እስክትጠልቅ ቀትን፥ ገብታም እስክትወጣ ሌሊቱን ለብቻ በሰዓት ይቈጥሩ ነበር፤ ማቴ. 20፥ 2-5፤

ሐ.ሥ. 2፥15። ሮማውያን ደግሞ ከእኩለ ሌሊት እስከ እኩለ ቀን፥ ከእኩለ ቀን እስከ እኩለ ሌሊት ቀንና ሌሊቱን አያይዘው በሰዓት ይቈጥሩ ነበር። ሰዓት የተወሰነ ጊዜን (ዮሐ. 4፥52:53)፥ አጭር ጊዜን (ራእ. 17፥12) ሊያመለክት ይችላል። በጥላና በሌላም ይለካ ነበር፤ 2ነገ. 20፥11።

**ሰይጣን፤** አሰናካይ ማለት ነው። የወደቁት መላእክት አለቃ፤ የመልካም ነገር ተቃራኒ፤ ማቴ. 25፥41። በሚከተሉት ስሞች ይጠራል ፦ ዲያብሎስ (ማቴ. 4፥1፤ 1ዮሐ. 3፥8)፥ ብዔል ዜቡል (ማቴ. 12፥24)፥ ቤልሆር (2ቆሮ. 6፥15)፥ አብዶንና አጶልዮን (ራእ. 9፥11)፥ የወንድሞች ከሳሽ (ራእ. 12፥10)፥ ባላጋራ (1ጴጥ. 5፥8)፥ የዓለም ሁሉ አሳች፥ ታላቁ ዘንዶ፥ የቀደመው እባብ (ራእ. 12፥9)፥ ክፉው (ማቴ. 13፥19)፥ ነፍሰ ገዳይ፥ የሐሰት አባት (ዮሐ. 8፥44)፥ የዚህ ዓለም ገዥ (ዮሐ. 12፥31)፥ የዚህ ዓለም አምላክ (2ቆሮ. 4፥4)፥ በአየር ላይ ሥልጣን ያለው አለቃ (ኤፌ. 2፥2)፥ ፈታኝ፤ 1ተሰ. 3፥5።

ጠባዩ በሚያገሳ አንበሳ ተመስሏል፤ 1ጴጥ. 5፥8። ምንም እንኳን ኃያል ቢሆንም በእግዚአብሔር ፈቃድና በክርስቶስ ሥራ ተወስኗል፤ ኢዮብ 1፥12፤ 2፥6፤ ማቴ. 12፥29፤ ሉቃ. 22፥31፤ ራእ. 20፥2። በመጀመሪያ ቅዱስ ሆኖ ተፈጠረ። በኋላ ግን በትዕቢቱ ወደቀ፤ ኢሳ. 14፥12-20፤ ሕዝ. 28፥12-19፤ 1ጢሞ. 3፥6። እግዚአብሔርን እየተዳፈረ፥ መልካም የሆነውን ነገር ሁሉ እየተቃወመ የራሱን መንግሥት ሊያቆም ይጥራል። ክርስቶስ ግን በሕይወቱና በሞቱ (በመስቀሉ) ድል ነሣው፤ በዓለም መጨረሻም ለዘለዓለም ይፈርድበታል፤ ማቴ. 4፥1-11፤ 12፥29፤ ዮሐ. 12፥31:32፤ ቆላ. 2፥15፤ ራእ. 20፥10፤ 1ዮሐ. 3፥8። «መልአክ» ይመ.

**ሰይፍ፤** ከብረት የሚሠራ የጦር መሣሪያ፤ 1ሳሙ. 13፥19:22። አንዳንዱ ሰይፍ ባለ ሁለት አፍ ነው፤ መዝ. 149፥6። የእግዚአብሔር ቃል ምሳሌ ነው፤ ኤፌ. 6፥17፤ ዕብ. 4፥12። «የጦር መሣሪያ» ይመ.

**ሰደቃ፤** ሰፊና ዝርግ የሆነ ባለ ረዥም እግር የማዕድ ገበታ፤ 1ሳሙ. 20፥29።

**ሰዱቃውያን፤** ክርስቶስ በምድር በነበረበት ጊዜ ከአይሁድ ወገን አንድ ክፍል። ብዙዎች ካህናት ነበሩ። ብዙ ጊዜ ሊቀ ካህናት ከእነርሱ ይመረጥ ነበር። ከአይሁድ ሸንጎም የሚበዙት ሰዱቃውያን ነበሩ። ፈሪሳውያንን በመቃወም የሙሴን ሕግ እንጂ ተጨማሪውን ወግ አይቀበሉም ነበር። ዋና ተስፋቸው በቤተ መቅደስና በሥርዓቱ ነበር። በትንሣኤ፥ በመናፍስት፥ በሚመጣው ዓለም ሰው እንደ ሥራው ዋጋውን እንደሚቀበልም አያምኑም ነበር፤ ማቴ. 22፥23-33፤ ሐ.ሥ. 23፥8። ክርስቶስ ስለ ሰዱቃውያን ማስጠንቀቂያ ሰጥቷል፤ ማቴ. 16፥6-12። እነርሱም ክርስቶስን አሳልፈው ሰጡት፥ በኋላም ሐዋርያትን አሳደዱ፤ ሐ.ሥ. 4፥1-22።

**ሰዶማውያን፤** ግብረ ሰዶምን የሚፈጽሙ፥ ማለትም ወንድ ከወንድ፥ ሴት ከሴት ጋር ዝሙት የሚያደርጉ ማለት ነው። ይህ ኃጢአት በሰዶም ይበዛ ነበርና ግብረ ሰዶም ተባለ፤ ዘፍ. 19፥5። በሙሴ ሕግ ይህን ኃጢአት የሚፈጽሙ ሁሉ ያለ ምሕረት ይገደሉ ነበር፤ ዘሌ. 20፥13፤ ዘዳ. 23፥17። ሆኖም ይህ ኃጢአት በእስራኤል የተለመደ ነበር፤ መሳ. 19፥22፤ 1ነገ. 14፥24፤ 2ነገ. 23፥7። ሰዎች እግዚአብሔርን መፍራትና ማምለክ ሲተዉ፥ ለጣዖታትም ሲሰግዱ የዚህ ዓይነት መጥፎ መንፈስ ያድርባቸዋል፤ በአሕዛብ መካከል ይህ ኃጢአት ይገኛል፤ ሮም 1፥22-27፤ 1ጢሞ. 1፥9-11። ይህ ዓይነት መንፈስ ያደረባቸው ሰዎች በወንጌል ኃይል ሊድኑ ይችላሉ፤ ማር. 6፥11፤ 1ቆሮ. 6፥9-11። «ቀላጭ» ይመ.

**ሰዶም፤** ሰዶምና ገሞራ በዮርዳኖስ ሸለቆ የተቈረቈሩ ከተሞች ነበሩ። ኃጢአታቸው በተለይም የዝሙት ሥራቸው አስጸያፊ ስለነበረ እግዚአብሔር ሊያጠፋቸው ወሰነ፤ ዘፍ. 18፥20፤ 19፥5-9። ሁለት መላእክት ሎጥን ከከተማው ካወጡ በኋላ እግዚአብሔር ሰዶምንና ገሞራን በእሳትና በዲን አጠፋ፤ ዘፍ. 19፥10-26። ሰዶምና ገሞራ አሁን በጨው ባሕር እንደተሸፈኑ ይገመታል። ሰዶም የክፉት ሁሉ የፍርድም ምሳሌ በመሆን ተጠቅሷል፤ ኢሳ. 1፥9:10፤ 3፥9፤ ኤር. 23፥14፤ ሰ.ኤ. 4፥6፤ ሕዝ. 16፥46፤ ማቴ. 10፥15፤ ራእ. 11፥8።

**ሰገባ፤** የሰይፍና የጐራዴ መክተቻ ማኅደር፥ ቤት፤ ኤር. 47፥6፤ ሰ.ኤ. 3፥13።

**ሰገነት፤** በቤት ጣራ ላይ የሚሠራ መናፈሻና መዝናኛ፤ 2ሳሙ. 11፥2፤ ዳን. 4፥29። ከደርብ ላይ ያለ ማደሪያ ክፍል፤ 1ነገ. 17፥19።

**ሰገገ፤** አሰገገ ማለት ለማየት ወይም ለመታየት አንገትን ማስረዘም፥ ማንጋጠጥ ማለት ነው። የትዕቢት ድርጊት፤ ኢዮብ 15፥26፤ 16፥14፤ ኢሳ. 3፥16።

**ሰጐን፤** አንገቱና ቅልጥሙ የረዘመ የበረሃ አሞራ። በፍጥነት ይሮጣል፤ አይበርም፤ ኢዮብ 39፥13-18። «ወፎች» ይመ.



**ሰፍነግ**፤ እንደ እስፖንጅ ውሃ የሚመጥ የሚቋጥር፥ የሚያሰራጭ ከባሕር የሚገኝ የተክል ዓይነት። ከባሕር ሰብስበው ሲያደርቁት ለማበስ፥ ለመጥረግና ለማጠጣት ይጠቅማል፤ ማቴ. 27፥48።

**ሱራፌል**፤ በራእይ ለኢሳይያስ የታዩ፥ በእግዚአብሔር ዙፋን አጠገብ የሚያገለግሉ ሰማያውያን ፍጥረቶች፤ ኢሳ. 6፥1-7።

**ሱርስት**፤ የሶርያውያን ቋንቋ፤ 2ነገ. 18፥26፤ ዕዝ. 4፥7፤ ኢሳ. 36፥11፤ ዳን. 2፥4።

የሱርስት አጻጻፍ ከቀኝ ወደ ግራ ነው፤ ፊደሉም በመጠኑ የዕብራይስጥንና የዐረብኛን ፊደል ይመስላል። መ.ቅ. ቀደም ሲል ወደ ሱረስት የተተረጐመ ስለሆነ፥ እንዲሁም እንደ እነቅዱስ ኤፍሬም ያሉ ሶርያውያን ሊቃውንት ስለተነሡ የሱረስት ቋንቋ ጥናት ከፍተኛ ስፍራ ሊይዝ ችሏል።

**ሱሳ**፤ ከባቢሎን በስተምሥራቅ 340 ኪ.ሜ. ርቆ የሚገኝ የፋርስ ከተማ። ሱሳ ከሦስቱ የፋርስ መንግሥት መናገሻ ከተማዎች አንዱ ነበር። ዳንኤል፥ ነህምያና አስቴር በሱሳ ኖረዋል፤ ነህ. 1፥2፤ አስ. 1፥2፤ ዳን. 8፥2። ሱሳ ከክ.በ. የመኖሪያ ከተማ መሆኑ ቢቀርም ፍርስራሹ እስከ ዛሬ ድረስ ይታያል። ካ. 1ረ።



በሱሳ በሸክላ ላይ ከተሣለ ሥዕል የተገለበጠ የፋርስ የክብር ዘበኛ

**ሱባዔ**፤ «ቍጥር» ይመ.

**ሱነም**፤ ከኢይዝራኤል በስተሰሜን አምስት ኪ.ሜ. ርቆ ከተራራ ዐቀበት ላይ የሚገኝ ከተማ። የዳዊት አልጋ አንጣፊና ወገብ ዳባሽ የነበረችው የአቢሳ ቤት በሱነም ነበር፤ 1ነገ. 1፥3። ኤልሳዕ በሱነም ለተቀበለችው ሴት የሞተውን ልጅዋን አስነሣ፤ 2ነገ. 4፥8-37።

**ሱፍ**፤ ቅጠሉ እሾህነት፥ አበባው ብጫነትና ቀይነት ያለው፥ ፍሬው ቅባት የሚወጣው ተክል፤ መ.መ. 2፥16፤ 4፥5።

**ሲላስ**፤ በኢየሩሳሌም ይኖር የነበረ ምእመንና ነቢይ። ከጳውሎስ ጋር ሆኖ ከኢየሩሳሌም ጉባኤ የተላከውን ደብዳቤ ወስዶ ለአብ.ክ. አደረሰ፤ ሐ.ሥ. 15፥22-35። በ2ኛው የጳውሎስ የወንጌል ጉዞ ከጳውሎስ ጋር አብሮ ሄደ (ሐ.ሥ. 15፥40-18፥22)፥ ስልዋኖስ በመባል የሚጠራው ምናልባት እርሱ ይሆናል፤ 2ቆሮ. 1፥19፤ 1ጴጥ. 5፥12።

**ሲሞን**፤ መንፈስ ቅዱስን የመስጠት ኃይል በገንዘብ ለመግዛት የፈለገ ጠንቋይ፤ ሐ.ሥ. 8፥9-24።

**ሲሣራ**፤ የከነዓናውያን ንጉሥ የኢያቢስ የሠራዊቱ አለቃ። ሃያ ዓመት እስራኤልን ካስጨነቀ በኋላ ዲቦራና ባርቅ አሸነፉት፤ መሳ. 4፥1-16፤ 1ሳሙ. 12፥9፤ መዝ. 83፥9። በሽሽት ላይ ሳለ የቄናዊው የሐቤር ሚስት ኢያዔል ገደለችው፤ መሳ. 4፥17-24፤ 5፥24-31።

**ሲራክ**፤ መጽሐፈ ሲራክ፤ ጸሓፊው ኢያሱ ወልደ አልዓዛር ወልደ ሲራክ ይባላል። መጽሐፈ ምሳሌን የመሰለ የምክር ቃል የያዘ መጽሐፍ ነው። የኦርቶዶክስና የካቶሊክ አብ.ክ. ከብ.ኪ. መጻሕፍት ጋር ቈጥረው ይቀበሉታል።

**ሲሮፊኒቃዊት**፤ የሶርያ ፊንቄ ሴት፤ ማር. 7፥26። «ፊንቄ» ይመ.

**ሲሳይ**፤ ምግብ። ሲሳይ ከእርሻና ከእንስሳት ኃይል ይገኛል፤ ምሳ. 13፥23፤ 14፥4፤ 27፥27።

**ሲባ**፤ የሳኦል ሎሌ። ሜምፊቦስቴን ለማስመጣት ዳዊትን ረዳ። ለሜምፊቦስቴ አረሰ፤ 2ሳሙ. 9፥2-11። በአቤሴሎም ሴራ ጊዜ ሜምፊቦስቴን በሐሰት ከሰሰ፤ የሜምፊቦስቴ እርሻ ተሰጠው፤ 2ሳሙ. 16፥1-4። ተንኰሉ በተገለጠበት ጊዜ እርሱና ሜምፊቦስቴ እርሻውን እንዲካፈሉ ታዘዙ፤ 2ሳሙ. 19፥24-30።

**ሲና**፤ 1. ከግብጽ አገር በስተምሥራቅና ከእስራኤል በስተደቡብ የሚገኝ አገር። በሲና ምድረ በዳ እስራኤላውያን 40 ዓመት ተንዙ፤ ዘጸ. 19፥1። ካ. 1መ።

2. ደብረ ሲና፤ ዐሠርቱ ቃላት የተሰጡበት ተራራ፤ ዘጸ. 19፥20። ኮሬብም ተብሎ ይጠራል፤ ዘጸ. 3፥1፤ ዘዳ. 4፥9:10። ካ. 2ኃ።

**ሲኖዶስ**፤ ሲኖዶስ ማለት ጉባኤ ማለት ነው። መጽሐፈ ሲኖዶስ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤ.ክ. በከፊል ሐዋርያት ጽፈውታል በማለት ከአ.ኪ.

መጻሕፍት ጋር ቁጥራ የምትቀበለው የቤ.ክ. ሥርዓት መጽሐፍ ነው። ሐዋርያት ጽፈውታል የተባለው በአራት ክፍል ተከፍሏል፤ ክፍሎቹም ትእዛዝ፥ ግጽው፥ አብጥሊስ፥ ሥርዓተ ጽዮን በመባል ይታወቃሉ። በተጨማሪም መጽሐፉ ብዙ የቤ.ክ.ን ጉባኤ ውሳኔዎች አጠቃልሎ ይዟል።

**ሲኦል፤** መ.ቅ. ለሲኦል ሁልጊዜ አንድ ዓይነት ትርጉም አይሰጥም :-

1. ኃጢአተኞች ከሞት በኋላ ይቀጡበታል፤ ዘዳ. 32፥22፤ መዝ. 9፥17፤ ምሳ. 5፥5፤ 7፥27፤ 9፥18፤ 15፥24፤ ሉቃ. 16፥23።

2. ሲኦል ጻድቃንም ኃጥአንም ሁለቱም በሥጋቸው ሟቾች መሆናቸውንና የሚቀበሩበትን ቦታ ያመለክታል፤ ኢዮብ 17፥13-14፤ መዝ. 89፥48፤ ሆሴዕ 13፥14።

3. መቃብርን ያመለክታል፤ ዘፍ. 42፥38፤ ዘኊ. 16፥30-33።

4. የጌታችን መቃብር ሲኦል ተብሏል፤ መዝ. 16፥10፤ ሐ.ሥ. 2፥24-31። በአ.ኪ. ምእመናን ወደ ክርስቶስ እንደሚሄዱ ተነግሯል፤ ሉቃ. 23፥43፤ ፊል. 1፥21-23። እግዚአብሔር ወደ ሲኦል ሊያወርድ ሊያወጣም ይችላል። ክርስቶስ የሲኦልን መክፈቻ ይዟል፤ ይህም የፈራጅነቱን ሥልጣን ያሳያል፤ 1ሳሙ. 2፥6፤ ራእ. 1፥18። በክፉ መንገድ ለሚራመዱ ሲኦል አስፈሪ ነው (ምሳ. 5፥5፤ 7፥27፤ 9፥18፤ 15፥24)፥ በዚያም ይሠቃያሉ፤ ዘዳ. 32፥22፤ ሉቃ. 16፥23:28። በመጨረሻ ሰዎች ሁሉ ለፍርድ ከሲኦል ይነሣሉ፤ ራእ. 20፥13:14። «ገሃነም» ይመ.

**ሲካር፤** ከሴኬም በስተደቡብ አንድ ኪ.ሜ. ርቆ የሚገኝ ቦታ። በሲካር ያዕቆብ መሠዊያ ሠራ፤ የውሃ ጉድጓድም ቈፈረ። ኢየሱስም በዚህ የውሃ ጉድጓድ አጠገብ አንዲት የሰማርያን ሴት አነጋገረ፤ ዘፍ. 33፥18-20፤ ዮሐ. 4፥5-7። ዛሬ የውሃው ጉድጓድ በአንዲት ቤ.ክ. ውስጥ ይታያል። የጉድጓዱ መግቢያ ከዛሬው የመሬት አቀማመጥ ልክ ስድስት ሜትር ዝቅ ያለ ነው፤ የጉድጓዱ ጥልቀት 32 ሜትር ነው።

**ሲዶና፤** ሲዶን፤ በታላቁ ባሕር ዳር ያለች የፊንቄ ጥንታዊት ወደብ፤ ዘፍ. 10፥15:19። ከእስራኤል ልጆች ለአንዱ ለአሴር ወገን ብትመደብም በእርሱ አልተወረሰችም፤ መሳ. 1፥31። ንጉሥ ሰሎሞን ቤተ መቅደስን ሲያሠራ የሲዶና ሰዎች እንጨቱን ጠረቡለት፤ 1ነገ. 5፥6፤ 1ዜ.መ. 22፥4። ለበአልና ለአስታሮት ይሰግዱ ነበር፥ በዚህም እስራኤልን አረከሱ፤ 1ነገ. 11፥5። ሲዶና የአክዓብ ሚስት ኤልዛቤል የተወለደችባት ከተማ ነበረች፤ 1ነገ. 16፥31-33። ነቢያት በሲዶና ላይ ትንቢት ተናገሩባት፤ ኤር. 27፥2-6፤ ኢዩ. 3፥4-6። ብዙ የሲዶና ሰዎች የክርስቶስን ትምህርት ሰሙ፥ ክርስቶስ ሲዶናን ጐበኘ፤ ማር. 3፥8፤ 7፥24:31። ጳውሎስ በሲዶና ከነበሩት ወዳጆች እርዳታ ተቀበለ፤ ሐ.ሥ. 27፥3። ዛሬ ሲዶና በሊባኖስ ውስጥ ናት፥ ሳይዳም ተብላ ትጠራለች። ካ. 7ቹ።

**ሲፓራ፤** የሙሴ ሚስት፥ የምድያም ካህን የዮቶር (የራጉኤል) ልጅ። ጌርሳምንና አልዓዛርን ለሙሴ ወለደች፤ ዘጸ. 2፥16-22፤ 18፥3:4። ወደ ግብጽ በሚጓዙበት ጊዜ ልጅዋን በመግረዝ ሙሴን ከእግዚአብሔር ቍጣ አዳነችው፤ ዘጸ. 4፥20:24-26። አባትዋ ወደ ሲና ምድረ በዳ ወደ ሙሴ አመጣት፤ ዘጸ. 18፥1-5።

**ሳሌም፤** በሄኖን አቅራቢያ የነበረ የመልከ ጼዴቅ ከተማ፤ ዘፍ. 14፥18፤ ዮሐ. 3፥23። ሳሌም በሚባለው ቦታ ላይ ኢየሩሳሌም የተሠራች ይመስላል፤ ወይም ሳሌም ማለት ራሱ ኢየሩሳሌም ማለት ይሆናል፤ መዝ. 76፥2፤ ዕብ. 7፥1-2።

**ሳሙኤል፤** ሳሙኤል ማለት የእግዚአብሔር ስም ወይም አምላካዊ ስም ማለት ነው። የመሳፍንት መጨረሻ ነው። ሳሙኤል ሳኦልንና ዳዊትን ቀብቶ አነገሠ፤ ሐ.ሥ. 3፥24፤ 13፥20። በጸሎት ከሙሴ ጋር ተቈጠረ፤ ኤር. 15፥1።

የኤፍሬማዊው የሕልቃናና መካን የነበረችው የሐና ልጅ ነው። እናቱ እንደ ስእለቷ ጡት በጣለ ጊዜ ለእግዚአብሔር አቀረበችው፥ ዔሊም አሳደገው፤ 1ሳሙ. 1። የዔሊ ልጆች ባለጌዎች ነበሩ። ሳሙኤል በዔሊ ፊት ሲያገለግል እግዚአብሔር ተገለጠለት፤ 1ሳሙ. 2-3። ዔሊ ሲሞት የእስራኤል ፈራጅና ካህን ሆነ፤ 1ሳሙ. 7፥15-17። የሳሙኤል ልጆች አካሄድ እንደ አባታቸው ባለመሆኑ ሕዝቡ ንጉሥ እንዲያነግሥላቸው ፈለጉ፤ ሳሙኤልም ሳኦልን ቀባ፤ 1ሳሙ. 8፥10። ሳኦል የእግዚአብሔርን ቃል ከናቀ በኋላ ሳሙኤል ዳዊትን ቀባ፤ 1ሳሙ. 13፥14፤ 15፥23፤ 16፥1-13። ዳዊትን በስደቱ ጊዜ አጽናናው (1ሳሙ. 19፥18-24)፥ ሳሙኤል በአገሩ በአርማቴም ሞተና በቤቱ ተቀበረ፤ 1ሳሙ. 25፥1። ከሞተ በኋላም በአንዲት የመናፍስት ቀስቃሽ አማካይነት ለሳኦል ተገለጠ፤ 1ሳሙ. 28፥11-19።

**የሳሙኤል መጻሕፍት፤** ማን እንደጻፋቸው አልተገለጠም ሆኖም፥ እነሳሙኤል የዘመናቸውን ታሪክ የጻፉ መሆኑ ታውቋል። የጻፉትም ዛሬ ላለው መጽሐፍ መሠረት ሆነ፤ 1ዜ.መ. 29፥29። አከፋፈል :-

1. የሳሙኤል ዳኝነት፤ 1ሳሙ. 1-7።

2. የሳኦል መንግሥት፤ 1ሳሙ. 8-31።

3. የዳዊት መንግሥት፤ 2ሳሙ. 1-24።

**ሳሚ፤** ዳዊትን የረገመ የብንያም ሰው። ዳዊት በስደት ላይ ስለነበረ ለጊዜው ሳሚን አልተበቀለም። በኋላ ግን ሳሚን እንዲቀጣ ለሰሎሞን መከረው፤ 1ነገ. 2፥9። ሰሎሞን ጊዜያዊ የግዞት ምሕረት አደረገለት። ከጥቂት ጊዜ በኋላ ግን ወደ ጌት ስለሄደ ገደለው፤ 1ነገ. 2፥36-46።

**ሳማ፤** የሚፋጅና ገላን የሚለበልብ ቅጠል፤ ምሳ. 24፥31፤ ኢሳ. 34፥13።

**ሳምራውያን፤** በሰማርያ የኖሩ ሕዝቦች። የአሦር ነገሥታት ስልምናሶርና ሳርጎን ሰማርያን ከያዙ በኋላ ዋና ዋና ሰዎችን ማረኩ። በእነርሱ ፈንታም

ሰዎችን ከልዩ ልዩ አምስት አገሮች አምጥተው በሰማርያ አሰፈሩአቸው፤ 2ነገ. 17፥24። እነርሱም ከቀሩት አይሁድ ጋር ተጋቡ። እግዚአብሔርን ስላልፈሩ የአንበሳ መዓት ተሰድዶባቸው ነበር። በኋላም አንበሶች እንዳይገድሏቸው እግዚአብሔርን ለማምለክ ሬለጉና የሙሴን ሕግ እንዲያውቁ ካህን ተላከላቸው፤ 2ነገ. 17፥24-33። አይሁድ ከባቢሎን ሲመለሱ ሳምራውያን ከእነርሱ ጋር ቤተ መቅደስን ለመሥራት ቀረቡ። ዘሩባቤል ግን ጥንታውያን የእስራኤል ዘሮች ስላይደሉ አልተቀበላቸውም፤ ዕዝ. 4፥1-4። ነህምያም ከኢየሩሳሌም አባረራቸው፤ ነህ. 13፥4-9። ከዚህም በኋላ ሳምራውያን ለራሳቸው በገሪዛን ተራራ መቅደስን ሠሩ። በዚያም ሰገዱ፤ ዮሐ. 4፥20። ክርስቶስ በምድር ሳለ አይሁድ ከሳምራውያን ጋር አይገናኙም ነበር (ዮሐ. 4፥9)፥ ሳምራዊም መባል ንቀት ነበረ፤ ሉቃ. 10፥33:37፤ 17፥16፤ ዮሐ. 8፥48። ሳምራውያን ኦሪትን እንጂ ነቢያትን አይቀበሉም ነበር። እስከ ዛሬም ድረስ በሳምራውያን ሕግና አምልኮት የሚመሩ ጥቂት ሰዎች በሴኬም (በናብሉስ) አሉ። «ሰማርያ» ይመ.

አይሁድ ቢነቅፏቸውም በሰማርያ ክርስቶስን የተቀበሉ ነበሩ፤ ዮሐ. 4፥39-42። ከተፈወሱት ከዐሥሩ ለምጻሞች ክርስቶስን ያመሰገነ ሳምራዊው ብቻ ነበር (ሉቃ. 17፥16)፥ በምሳሌም በመልካም አርአያነት የተጠቀሰ ርኅሩኅ ሳምራዊ ነው፤ ሉቃ. 10፥33። ኢየሱስ በመጀመሪያ ደቀ መዛሙርቱን ወደ ሳምራውያን አልላከም። ምክንያቱም በዚያን ጊዜ ኢየሱስ አገልግሎቱን በአይሁድ ዘንድ ወስኖ ስለነበረ ነው፤ ማቴ. 10፥5፤ ሉቃ. 9፥52:53። ከትንሣኤው በኋላ ግን በሰማርያ እንዲመሰክሩ ሐዋርያትን አዘዛቸው። በዚህም መሠረት ፊልጶስ በሰማርያ ወንጌልን በሰበከ ጊዜ ብዙዎች አመኑ፤ ሐዋርያትም በጸለዩላቸው ጊዜ መንፈስ ቅዱስን ተቀበሉ፤ ሐ.ሥ. 1፥8፤ 8፥5-25።

**ሳምንት**፤ በሰባት የሚቈጠር ከእሑድ እስከ እሑድ ያሉት ቀናት። እግዚአብሔር ዓለምን በስድስት ቀን ፈጥሮ በሰባተኛው ቀን ከሥራው ዐረፈ፤ ዘፍ. 2፥1-3። ያዕቆብ ሰባቱን ዓመት በሰባት ቀምሮ ሳምንት አለ፤ ዘፍ. 29፥27። እስራኤል ከግብጽ ሲወጡ የሰባት ቀን ሳምንት ለመዱ። እንዲያከብሩትም ታዘዙ፤ ዘጸ. 16፥21-30፤ 20፥8-11።

**ሳሮን**፤ ሰሮና፤ በታላቁ ባሕር አጠገብ ከኢዮጴ እስከ ቀርሜሎስ ያለው ፍሬያማ ሜዳ፤ 1ዜ.መ. 27፥29፤ ኢሳ. 35፥2፤ 65፥10፤ ሐ.ሥ. 9፥35።

**ሳቅ**፤ ደስታን (ዘፍ. 21፥6፤ ሉቃ. 6፥21)፥ አለማመንንና ማፌዝን (ዘፍ. 18፥12-15)፥ መንቀፍን (መዝ. 2፥4፤ ኤር. 20፥7) ሊያመለክት ይችላል። ቅዱሳት መጻሕፍት ከሳቅ ይልቅ ኀዘንን ጠቃሚ እንደሆነ ይናገራሉ፤ ያዕ. 4፥9።

**ሳቢላኒስ**፤ ከደማስቆ በስተሰሜን፥ ከሊባኖስም ዐስተምሥራቅ ያለው አገር፤ ሉቃ. 3፥1።

**ሳቢሳ**፤ መልኩ ነጭ፥ ቅልጥሙ ዘለግ ያለ፥ ብዙ መንጋ እየሆነ ከከብት ጋር የሚሰማራ የረግረግና የወንዝ አሞራ፤ ዘሌ. 11፥19። «ወፎች» ይመ.

**ሳባ**፤ በዚህ ስም ፦ 1. የኩሽ ልጅ (ዘፍ. 10:7)፥ 2. የራዕማ ልጅ (1ዜ.መ. 1፥9)፥ 3. የዮቅጣን ልጅ (ዘፍ. 10፥28)፥ 4. የአብርሃም የልጅ ልጅ የዮቅሳን ልጅ (ዘፍ. 25፥3)፥ 5. ከነገደ ጋድ አባቶች አንዱ ተሰይመዋል፤ 1ዜ.መ. 5፥13።

በመ.ቅ. ሳባ ብዙ ጊዜ ከኤርትራ ባሕር በስተምሥራቅ በደቡብ ዐረብ የነበረችውን አገርና መንግሥት ያመለክታል (የአሁኑ የየመን አገር)። የሳባ ሰዎች ነጋዴዎች ስለነበሩ ወደ ብዙ አገር ይደርሱ ነበር፤ ኢዮብ 6:19፤ 1ነገ. 10፥1-13፤ ኢሳ. 60፥6፤ ኤር. 6፥20፤ ሕዝ. 27፥22። በሳባና በአክሱም መንግሥት የነበረው ግንኙነት በ2ዜ.መ. 21፥16 የተገለጠ ይመስላል። «ኢትዮጵያ» ይመ.

**ሳባጥ**፤ «ወር» ይመ.

**ሳንቲም**፤ ከናስ የተሠራ የእስራኤል ቅንስናሽ ገንዘብ፤ ሉቃ. 12፥6፤ 21፥2። «ገንዘብ» ይመ.

**ሳኦል**፤ የስሙ ትርጉም «(ከእግዚአብሔር) የተለመነ» ማለት ነው። በመጀመሪያ የእስራኤል ሁሉ ንጉሥ የሆነው የብንያማዊው የቂስ ልጅ። እስከ ሳኦል ዘመን ድረስ እግዚአብሔር ሙሴንና አሮንን ኢያሱንም እንዳስነሣላቸው ሁሉ፥ ለሕዝቡ መሳፍንትንም ይሰጣቸው ነበር። ከእነርሱም ታላቅ የሆነው ሳሙኤል በሸመገለ ጊዜ ሕዝቡ ንጉሥ ስጠን አሉት። ይህም አሳባቸው መልካም አልነበረም፤ እግዚአብሔር ግን እንደ ፍላጎታቸው ንጉሥ ሰጣቸው፤ 1ሳሙ. 8፤ 12፥6-18። ሳኦል ከሳሙኤል ጋር እንደተገናኘ፥ እንደተቀባም፤ በኋላም በዕጣ እንደተመረጠ በ1ሳሙ. 9ና 10 በሰፊው ተጽፏል። ሳኦል በእግዚአብሔር መንፈስ ኃይል አሞናውያንን ድል በመንሣት ሕዝቡን ደስ አሰኛቸው፤ 1ሳሙ. 11፤ 14፥47-48። ነገር ግን ለእግዚአብሔር በመታዘዝ አልጸናም። ፍልስጥኤማውያንን ፈርቶ የሳሙኤልን መምጣት ሳይጠብቅ መሥዋዕትን በማቅረብ በደለ፤ 1ሳሙ. 13። በአማሌቅ ላይ በተላከ ጊዜ በሙሉ ልቡ ለእግዚአብሔር አልታዘዘም፤ 1ሳሙ. 15። ሳሙኤልም፥ መንግሥትህ አይጸናም (1ሳሙ. 13፥13:14)፤ እግዚአብሔር ናቀህ (1ሳሙ. 15፥23-28) አለው። ከዚህ ጊዜ ጀምሮ ክፉ መንፈስ አደረበት፤ 1ሳሙ. 16፥14-23። እግዚአብሔር ዳዊትን ለንጉሥነት መምረጡን ባስተዋለ ጊዜ ሳኦል በዳዊት ላይ ቀና፤ በልዩ ልዩ ተንኰል ሊገድለው በማሰብ ያሳድደው ነበር፤ 1ሳሙ. 18፥6-20፥42። ዳዊትን ስለረዳው ካህኑን አቢሜሌክንና ሌሎችንም አስገደለ፤ 1ሳሙ. 22፥6-23። ዳዊትን ያሳድድ ነበር እንጂ አልያዘውም፤ 1ሳሙ. 23-26። ሁለት ጊዜ ዳዊት ሳኦልን ሳይገድል ራራለት፤ ሳኦልም መጸጸቱን ገልጦ፥ በድያለሁ አለ፤ 1ሳሙ. 24፥17-21፤ 26፥21:25።

በመጨረሻም ሞቶ የነበረውን ሳሙኤልን ለመጠየቅ፥ መናፍስት ጠሪ ወደ ሆነች ሴት በድብቅ ሄደ። ሳሙኤል አንተና ልጆችህ ነገ ትሞታላችሁ ባለው ጊዜ በምድር ላይ ወደቀ፤ 1ሳሙ. 28፥20ን

ከ9፥2 ጋር ያነጻጽሩ። በግግሥቱ በፍልስጥኤማውያን ሲሸነፍ ራሱን ገደለ፤ 1ሳሙ. 31፤ 1ዜ.መ. 10። ዳዊት ሲያለቅስለት «ኃያላን እንዴት ወደቁ!» አለ፤ 2ሳሙ. 1፥17-27። በእውነትም የሳኦል ውድቀት አሳዛኝ ከመሆኑ በላይ የሚያስፈራ ማስጠንቀቂያ ነው፤ 1ዜ.መ. 10፥13:14።

**ሳውል፤** የጳውሎስ መጀመሪያ ስም፤ በመጀመሪያ የቤ.ክ. አሳዳጅ የነበረ፥ በኋላ ግን ሐዋርያ የሆነ፤ ሳውል በአይሁድ መካከል ሲኖር የተጠቀመበት ዕብራዊ ስም ነው፤ ሳኦልና ሳውል ባጻጻፍ ቢለያዩም ትርጉማቸው አንድ ነው፤ ሐ.ሥ. 7፥60፤ 8፥3፤ 9፥4፤ 13፥1-3። «ጳውሎስ» ይመ.

**ሳዶቅ፤** በዳዊትና በሰሎሞን ዘመን የነበረ ሊቀ ካህናት፤ 2ሳሙ. 8፥17፤ 1ነገ. 2፥35። ከአሮን ልጅ ከአልዓዛር ዘሮች ተወለደ፤ 1ዜ.መ. 6፥8:53። የሳኦልን ቤት ይቃወምና ዳዊትን ይደግፍ ነበር፤ 1ዜ.መ. 12፥28። ታቦቱን ወደ ጽዮን በማምጣት ረዳ፤ 1ዜ.መ. 15፥11:12። በአቤሴሎም (2ሳሙ. 15፥24-29:35፤ 17፥15)፥ እንዲሁም በአዶንያስ ሴራ ጊዜ ዳዊትን ደገፈ፥ ሰሎሞንንም ቀባ፤ 1ነገ. 1፥8:26:32-39። ዘሮቹ ሰሎሞን በሠራው ቤተ መቅደስ አለቆች ነበሩ፤ 1ዜ.መ. 6፥8-15፤ ከባቢሎን ምርኮ ተመለሱ፤ ዕዝ. 7፥2። ሕዝቅኤል በራእይ ባየው መቅደስ ውስጥ እንዲያገለግሉ የተመረጡ የሳዶቅ ልጆች ነበሩ፤ ሕዝ. 44፥15-31።

**ሴሎ፤** ከኢየሩሳሌም በስተሰሜን 32 ኪ.ሜ. ርቆ በኤፍሬም ድርሻ ውስጥ የሚገኝ ከተማ። ከኢያሱ እስከ ሳሙኤል ዘመን ድረስ የእግዚአብሔር ታቦት በሴሎ ይኖር ነበር። ሰዎችም ለዓመት በዓል ወደዚያ ይሄዱ ነበር፤ ኢያሱ 18፥1፤ መሳ. 21፥19። ሐና እግዚአብሔር ልጅ እንዲሰጣት በሴሎ ጸለየች፤ በኋላም ሳሙኤል በሴሎ አደገ፤ 1ሳሙ. 1። በመጨረሻ ሴሎ ፈረሰና ባድማ ሆነ፤ ኤር. 7፥12-14። ካ. 3ሰ።

**ሴም፤** የኖኅ ታላቅ ልጅ፤ ዘፍ. 5፥32፤ 6፥10። ከጥፋት ውሃ ዳነ፤ ዘፍ. 7፥13፤ 9፥18። የአባቱን ራቁትነት አለበሰ፤ ዘፍ. 9፥20-24። አባቱ ስለ እርሱ ትንቢት ተናገረ፤ ዘፍ. 9:26:27። አምስት ልጆችን በመውለዱ የብዙ ሕዝብ አባት ሆነ፤ ዘፍ. 10፥21-32። ልጁ አርፋክስድም የአብርሃም ቅድመ አያት ሆነ፤ ዘፍ. 11፥10-26። ስሙ በኢየሱስ ክርስቶስ የትውልድ መጽሐፍ ይገኛል፤ ሉቃ. 3፥36።

**ሴሰኝነት፤** ኃይለኛ የዝሙት ስሜት፥ ከባል ወይም ከሚስት ውጭ ሌላ ሰው መያዝና ማስቀመጥ፤ 1ቆሮ. 6፥9፤ ራእ. 21፥8።

**ሴት፤** የአዳምና የሔዋን ሦስተኛ ልጅ። ስሙንም «በአቤል ፋንታ እግዚአብሔር ሌላ ዘር ተካልኝ» ስትል እናቱ ሴት አለችው። በሴት ዘር በኩል ለአዳም የተሰጠ ተስፋ ተፈጸመ፤ ዘፍ. 4፥25-5፥8፤ ሉቃ. 3፥23-38፤ ገላ. 4፥4።

**ሴት፤** እግዚአብሔር በመልኩ የፈጠራት፤ ዘፍ. 1፥26:27። የመጀመሪያዋ ሴት ከወንድ ተፈጠረች። ደግሞ ለወንድ አጋዥ ሆነች፤ ሴትና ወንድ በጋብቻ አንድ ሥጋ ይሆናሉ፤ ዘፍ. 2፥18-24፤ «ሚስት» ይመ.። በሙሴ ሕግ የሴት መብት የተጠበቀ ነበር፤ ዘጸ. 15፥12፤ 23፥17፤ 24፥1-5:17። ኢየሱስ በቃልና በድርጊት ሴትን ያከብርና ይረዳ ነበር፤ ማቴ. 5፥27-32፤ 9፥18-26፤ ሉቃ. 10፥38-42።

በብ.ኪ. የታወቁት ሴቶች፥ ሣራ (ዘፍ. 12-23)፥ ርብቃ (ዘፍ. 24)፥ ራሔል (ዘፍ. 29)፥ ማርያም (ዘጸ. 2፥1-9፤ 15፥21፤ ዘኍ. 12)፥ ዲቦራ (መሳ. 4-5)፥ ሩት (ሩት 1-4)፥ ሐና (1ሳሙ. 1፥1-2፥11)፥ አስቴር (አስ. 1-10) ናቸው። በአ.ኪ. የታወቁ ሴቶች ኤልሣቤጥ (ሉቃ. 1፥5-80)፥ ማርያም (ሉቃ. 2፥5-19)፥ ሐና (ሉቃ. 2፥36-38)፥ ማርያምና ማርታ (ሉቃ. 10፥38-42)፥ ኢየሱስን የተከተሉት ሴቶች ናቸው፤ ሉቃ. 8፥2:3፤ ዮሐ. 20፥1-18፤ ሐ.ሥ. 1፥14፤ 12፥12። ልድያ ከአውሮጳ በመጀመሪያ ያመነች ሴት ነበረች፤ ሐ.ሥ. 16፥13-15። ብዙ ሴቶች እንደ ፌቤን በሮም ቤ.ክ. ያገለግሉ ነበር፤ ሮም 16፥1-3:6:15። ወንዶችና ሴቶች በእግዚአብሔር መልክ ተፈጥረዋል፥ በአንድ መንገድም በክርስቶስ ይድናሉ፤ ገላ. 3፥28። ሆኖም ወንድ አስቀድሞ ተፈጠረ፤ ሴትም ለወንድ ተፈጠረች፤ ግን ሴት ያለ ወንድ ወንድም ያለ ሴት አይሆንም፤ 1ቆሮ. 11፥3-16፤ 1ጢሞ. 2፥11-15። በቤ.ክ. የሴቶች አገልግሎት ብዙ ነው (ሐ.ሥ. 21፥9፤ 1ጢሞ. 5፥10)፤ ስለ አካሄዳቸውም ብዙ መመሪያ ተሰጥቷል፤ 1ጢሞ. 3፥11፤ ቲቶ 2፥3-5።

የሴት ክብር ትልቅ ነው። የክርስቶስ ሙሽራ የተባለችው ቤ.ክ. በሴት ተመስላለች፤ ኤፌ. 5፥21-33። ወንዶች ባልቴቶች ሴቶችን እንደ እናቶች፥ ቈነጃጅትን እንደ እኅቶች ማክበር ይገባቸዋል፤ 1ጢሞ. 5:1:2። «ወንድ» ይመ.

**ሴኬም፤** በጌባልና በገሪዛን መካከል የነበረው ከተማ። አብርሃም ወደ ከነዓን ሲገባ በመጀመሪያ መሠዊያን የሠራው በሴኬም ነበር፤ ዘፍ. 12፥6-8። ያዕቆብ በሴኬም መሬት ገዛ (ዘፍ. 33፥18-20)፥ ስምዖንና ሌዊ በእኅታቸው ምክንያት የሴኬምን ሰዎች ገደሉ (ም. 34)፥ ዮሴፍም በዚህ ቦታ ተቀበረ፤ ኢያሱ 24፥32። በሴኬም እስራኤል ሮብዓምን ካዱ። ኢዮርብዓምም በሴኬም ኖረ፤ 1ነገ. 12፥1:25። ካ. 3ሰ።

**ሴዎን፤** እስራኤልን የተቃወመ የአሞራውያን ንጉሥ። አገሩ ከሞዓብ አገር በስተሰሜን ነበር፤ በጦርነት ጊዜ በእስራኤል ተሸነፈ፤ ዘኍ. 21፥21-31።

**ሴይር፤** 1. በሴይር አገር የነበሩ ሕዝብ አባት፥ ሴይር ሖሪ ተብሎ ይጠራ ነበር፤ ዘፍ. 36፥20። 2. ዔሳው ወደ ኤዶም ከመግባቱ በፊት የኤዶም አገር ስም፤ ዘፍ. 32፥3። 3. በሴይር አገር የነበሩ ሕዝብ የሚጠሩበት ስም፤ ሕዝ. 25፥8። 4. በሴይር አገር ያለ የተራራ ስም፤ ዘፍ. 14፥6።

**ሴዴቅያስ፤** «የእግዚአብሔር ጽድቅ» ማለት ነው። በይሁዳ ከነገሡት ከኢዮስያስ ልጆች



በገሪዛንና በጌባል ተራሮች መካከል ተሠርቶ የነበረ የሴኬም ከተማ

ምስተኛው፥ በኢየሩሳሌም ከነገሡት ከዳዊት ዘሮች የመጨረሻው ነበረ። ከ597-587 ከክ.ል. ነገሠ። ክፉም ነበረ። የወንድሙ ልጅ ዮአኪን በተማረከ ጊዜ የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደነፆር በይሁዳ እንዲነግሥ፤ ግብር እንዲከፍል አስማለው። ከአራት ዓመት በኋላ ወደ ባቢሎን ተወስዶ ተመለሰ፤ ኤር. 51፥59። በኋላ በግብጽ ተማምኖ በባቢሎን ንጉሥ ላይ ዐመፀ። የባቢሎን ሠራዊት ኢየሩሳሌምን ከበቡ፤ ከዓመት ተመንፈቅ በኋላ ያዙአት። ሴዴቅያስ ተይዞ ተማረከ፤ ዕውር ሆኖ በግዞት ቤት ሳለ ሞተ፤ 2ነገ. 24፥18-25፥7፤ 2ዜ.መ. 36፥10-21፤ ኤር. 39፥1-10፤ 52፥1-11።

በኤርምያስ ትንቢት ሴዴቅያስና ከዮአኪን ጋር ያልተማረኩት በተበላሸ የበለስ ፍሬ ተመሰሉ፤ ኤር. 24፤ 29፥15-20፤ ሕዝ. 17፥13:14። ኤርምያስ ሴዴቅያስን ይመክረውና ያስጠነቅቀው ነበር፤ ግን አልሰማም፤ ኤር. 21፤ 32፥1-5፤ 37፤38። ሕዝቅኤል ሴዴቅያስ መሐላውን በማፍረስ በራሱና በከተማው ላይ ፍርድ እንደሚያመጣ ተነበየ፤ ሕዝ. 17 (በተለይ ቍ. 11-21)፤ 21፥24-27።

**ሰላች**፤ ቀጭንና አቋራጭ መንገድ፤ ሉቃ. 14፥21፤ ሐ.ሥ. 12፥10።

**ሰሌት**፤ ሒሳብ፥ እርዳታ፥ መተጋገዝ፤ ፊል. 4:15፤ ዕብ. 13፥17።

**ስልምናሶር**፤ «ሹልማን የተባለው አምላክ አለቃ ነው» ማለት ነው። ይህ የአምስቱ አሦራውያን ነገሥታት ስም ነው። አምስተኛው በመ.ቅ. ተጠቅሷል፥ እርሱም ሰማርያን ሦስት ዓመት ከብቦ ከያዛት በኋላ የእስራኤልን ሰዎች ወደ አሦር ማርኮ ወሰደ፤ 2ነገ. 17፥3፤ 18፥9፤ ሆሴዕ 10፥14።

**ስልዋኖስ**፤ «ሲላስ» ይመ.

**ስም**፤ አዳም በመጀመሪያ ለእንስሳት፥ በኋላም ለሚስቱ ስም አወጣ፤ ዘፍ. 2፥18-23፤ 3፥20።በእስራኤላውያን ዘንድ ስም ጠባይን፥ ግብርንና ሁኔታን እንደሚገልጥ ሆኖ ይሰየማል። ስለዚህ በብ.ኪ. ያለ ስም ሁሉ መጥሪያ ወይም መጠሪያ ብቻ ሳይሆን ብዙ ነገሮችን ያመለክታል። ለምሳሌ ምናሴ (ማስረሻ) የስም ሰጭውን ሁኔታ (ዘፍ. 41፥51)፥ ኢካቦድ (ክብር የለም) የሆነውን ድርጊት (1ሳሙ. 4፥21-22)፥ ያዕቆብ (አሰናካይ) ጠባዩን (ዘፍ. 25፥26)፥ ዮሴፍ (ይጨምር) የሰጭውን ተስፋ (ዘፍ. 30፥24) ያሳስባሉ። እግዚአብሔርም የሰውን ስም ሲለውጥ እንደ አብርሃም ሁኔታው ወይም እንደ እስራኤል ጠባዩ እንደተለወጠ ይገልጣል። የእግዚአብሔር ስሞች ባሕርዩን ይገልጣሉ፥ እንደ ስሞቹ እንደሚሠራ ያረጋግጣሉ፤ ዘጸ. 6፥3፤ 15፥3። ከሁሉም በላይ የስም ምሥጢር በጌታችን ይታያል። ኢየሱስ (አዳኝ) ሥራውን፤ አማኑኤል (እግዚአብሔር ከእኛ ጋር) አምላክነቱን ያሳያል። በክርስቶስ ስም ምእመናን ከፍርድ ይድናሉ (ዮሐ. 3፥18)፥ አጋንንትን ያወጣሉ (ማር. 16፥17)፥ መከራን ይቀበላሉ (ሐ.ሥ. 5፥41)፥ ልመናቸውንም ያቀርባሉ (ዮሐ. 16፥24)፤ ስሙ ከሁሉም በላይ ነውና፤ ፊል. 2፥9-11።

**ስምዖን**፤ «ሰማ» ከሚለው ግስ የተገኘ ነው። ልያ የወለደችለት የያዕቆብ ሁለተኛ ልጅ፤ ዘፍ. 29፥33። በእኅቱ ዲና ምክንያት ከወንድሙ ከሌዊ ጋር የሴኬምን ሰዎች ገደለ፤ ዘፍ. 34፥25:30:31፤ 49፥5-7። ዮሴፍ በግብጽ አሰረው፤ 42፥24። ከእስራኤል ነገዶች የአንዱ አባት ሆነ። በስሙም ነገደ ስምዖን ተብሎ ተሰየመ፤ ዘፍ. 46፥10፤ ዘኍ. 1፥4-6። በከነዓን የተቀበለው የርስት ድርሻ ከሌሎች ነገዶች በስተ ደቡብ፥ በይሁዳ ርስት መካከል ነበረ፤ ኢያሱ 19፥9። ካ. 30። «ነገድ» ይመ.

**ስምዖን**፤ በአዲስ ኪዳን በዚህ ስም የሚጠሩ ዋና ዋናዎቹ የሚከተሉት ናቸው ፦

1. በቤተ መቅደስ ሕፃኑ ኢየሱስን ተቀብሎ እግዚአብሔርን ያመሰገነ ነቢይ፤ ሉቃ. 2፥25-35።

2. ጴጥሮስ ተብሎ የተሰየመው ሐዋርያ፤ ማቴ. 4፥18። «ጴጥሮስ»ን ይመ.

3. ቀነናዊው፤ ከሐዋርያት አንዱ፤ ማቴ. 10፥4። ቀነናዊ ማለት ቀናተኛ ማለት ይሆናል፤ ሉቃ. 6፥15። «ሐዋርያ» ይመ.

4. የክርስቶስ ወንድም፤ ማቴ. 13፥55። «የጌታችን ወንድሞች» ይመ.

5. ክርስቶስን በቤቱ ያስተናገደ በቤቱም አንዲት ሴት የክርስቶስን እግር ሽቶ የቀባች አንድ ፈሪሳዊ፤ ሉቃ. 7፥36-50።

6. በቢታንያ ይኖር የነበረ፥ በቤቱም ማርያም ክርስቶስን የቀባችበት አንድ ለምጻም፤ ማቴ. 26፥6፤ ዮሐ. 12፥3።

7. ከቀሬና የመጣ የክርስቶስን መስቀል የተሸከመ፤ ማር. 15፥21።

8. በኢዮጴ የነበረ ቁርበት ፋቂ ሐ.ሥ. 9፥36:43፤ 10፥6።

**ስርቆት**፤ የሌላውን ሀብት ያለአግባብ መውሰድ። ስርቆት በሕግ ተከልክሏል፤ ዘጸ. 20፥15፤ ዘሌ. 19፥13፤ ኢሳ. 61፥8፤ ሕዝ. 22፥9። በጥንት ዘመን በየመንገዱ ብዙ ወንበዴዎች ነበሩ፤ መሳ. 5፥6፤ ሉቃ. 10፥30፤ 2ቆሮ. 11፥26። የሃይማኖት መሪዎች እንኳን በተለያየ ዘዴ ሰርቀዋል፤ ሆሴዕ 6፥9፤ ሉቃ. 20፥47፤ ዮሐ. 12፥6።

እንደ ፀሥራት ያለውን ተገቢውን ለእግዚአብሔር አለመስጠት ስርቆት ነው፤ ሚል. 3፥8። ሰው መስረቅ ሳይሆን እግዚአብሔር በሰጠው እየተደሰተ ሠርቶ ለሌሎች ማካፈል ይገባዋል፤ ኤፌ. 4፥28፤ ዕብ. 13፥5።

**ስርጓጉጥ**፤ ሸካራና ወጣ ገባ የሆነ መንገድ። ያልተስተካከለ አሳብ ምሳሌ ነው፤ ኢሳ. 40፥5።

**ስርጥ**፤ ጠባብና አደገኛ መንገድ፤ መሳ. 5፥6። በባሕር ውስጥ ጥልቀት የሌለው ቦታ ስርጥ ይባላል፤ ሐ.ሥ. 27፥39።

**ስስት**፤ ንፍገት፥ ሆዳምነት። ስስታም ከእግዚአብሔር ጋር ኅብረት የለውም፤ መዝ. 101፥5። ጻድቅ ሰው አይሰስትም፤ ምሳ. 21፥26። ክርስቶስ ፈሪሳውያንን ስለ ስስታቸው ወቀሳቸው፤ ማቴ. 23፥25።

**ስቅለት**፤ በእስራኤል ዘንድ ሰው የሞት ፍርድ ከተፈጸመበት በኋላ ሬሳው ለማስጠንቀቂያ ከዛፍ ላይ ይሰቀል ነበር። ነገር ግን እስራኤላውያን ሰውን በስቅላት አይገድሉም ነበር፤ ዘዳ. 21፥21-23፤ ኢያሱ 10፥26። ሮማውያን በብዙ ሥቃይ እንዲሞት የተፈረደበትን ሰው በተለይም ደግሞ ዐመፀኞችን ይሰቅሉ ነበር። ለምሳሌ አራት ዓመት ከክ.በ. ሁለት ሺህ ሰዎች በይሁዳ አገር ተሰቅለዋል። በ66 ዓ.ም. ሦስት ሺህ ስድስት መቶ አይሁድ በስቅላት ተቀጥተዋል። በክርስቶስ ዘመን አራት ዐይነት መስቀሎች ነበሩ ፦ + T X 1። ክርስቶስ የተሰቀለበት መስቀል የመጀመሪያውን ዓይነት ይመስላል።



ሰው በስቅላት ሲሞት ብዙ ጊዜ የሚከተሉት ነገሮች ይፈጸሙበት ነበር።

1. ከመሰቀሉ በፊት ይገረፋል፤ ማቴ. 27፥26።

2. መስቀሉን ወይም የመስቀሉን ግንድ ተሸክሞ ከከተማ ወደ ውጭ ወዳለው የመስቀያ ቦታ ይወሰዳል፤ ዮሐ. 19፥17-20።

3. በምሳሌ 31፥6 የተጻፈውን በማሰብ፥ በኢየሩሳሌም የነበረው የሴቶች ማኅበር የሥቃይ ማደንዘዣ መጠጥ ለሚሰቀሉት ይሰጥ ነበር፤ ማቴ. 27፥34።

4. በመስቀል ላይ በምስማር ይቸከራል፥ ወይም በገመድ ይታሰራል፤ ዮሐ. 20፥25።

5. ከበደለኛው ራስ በላይ የሚቹ ወንጀል ተጽፎ ይለጠፋል። ጲላጦስ በክርስቶስ የመስቀል ሞት የፈረደበት አይሁድ «ተሳድቧል» በሚለው ክሳቸው

ምክንያት ሳይሆን «የአይሁድ ንጉሥ» ነኝ ስላለ የቀማር ተቀናቃኝ ነው በማለት ነበር፤ ዮሐ. 19፥19፤ ቆላ. 2፥14:15።




በዕብራይስጥና በግሪክ፥ በላቲንኛም ከክርስቶስ ራስ በላይ ሲሰቀል «ኢየሱስ ናዝራዊ ንጉሠ አይሁድ» የሚለው የተለጠፈ ጽሕፈት

6. የተሰቀለውን ሰው ልብስ ወታደሮች እንዲካፈሉት ይደረጋል፤ ዮሐ. 19፥23።

7. የተሰቀለው ሰው የሚሞተው ደሙን በማፍሰስ ሳይሆን በልቡ ድካም ነው። የሚሰቀለው ሰው ብዙ ጊዜ በ2ኛው ወይም በ3ኛው ቀን ይሞት ነበር፤ ማር. 15፥44። ወዳጆች እንዳያወርዱት መስቀሉ በወታደሮች ይጠበቃል። ቶሎ እንዲሞት ሲፈልጉ እግሮቹን ይሰብሩ ነበር። ኢየሱስን ግን ጎኑን ወጉት፤ ዮሐ. 19፥31-34።

የአ.ኪ. ጸሓፊዎች ስለ ክርስቶስ መስቀል የሚከተሉትን አሳቦች ያስተምራሉ ፦

ሀ) መስቀል የመዳን ቃል ነው። ክርስቶስ የሞተው ስለ ኃጢአት ነውና የመስቀሉ ቃል የወንጌል ቃል ማለት ነው፤ 1ቆሮ. 1፥17-25፤ ቆላ. 1፥19-20።

ለ) መስቀል የማስታረቅ ቃል ነው። በሰዎች መካከል የነበረውን የጥል ግድግዳ አፍርሷልና፤ ኤፌ. 2፥14-16።

ሐ) የነውር ቃል ነው። ኢየሱስ በመስቀል ሲሞት በሮማውያንም በአይሁድም ዘንድ የተናቀ ሆነ። ነገር ግን በክርስትና ትምህርት አምላክ ነውና አምልኮትና ስግደት ተገባው። ይህ ለአይሁድ መሰናክል፥ ለአሕዛብ ሞኝነት ነበር፤ 1ቆሮ. 1፥18-25።

መ) የቤዛነት ቃል ነው። የክርስቶስ መስቀል የኃጢአት መሥዋዕት ነው፤ ሮም 3፥25። ስለዚህ የክርስቶስ ሞት ምእመናን ከሕጉ እርግማን የዳኑበትና የሕጉ ክስ የተሰረዘበት ነው፤ ገላ. 3፥13። ምእመናን በክርስቶስ በማመንና በመጠመቅ የክርስቶስ ሞትና ትንሣኤ ተባባሪዎች መሆናቸውን ይገልጣሉ፤ ሮም 6፥1-11።

ሠ) የቅድስና ቃል ነው። ይህም ከክርስቶስ መስቀል ጋር በእምነት ተባባሪ መሆን ከኃጢአት ፍርድ መዳን ብቻ ሳይሆን ከኃጢአትና ከዓለም ኃይልም መላቀቅ ነው፤ በቅድስና ለመኖርም ኃይል ነው፤ ገላ. 2፥20፤ 5፥24፤ 6፥14።

ክርስቶስ በመስቀል ላይ ሳለ የተናገራቸው ሰባት ቃላት (በሉቃ. 23፥34፤ ዮሐ. 19፥25-27፤ ሉቃ. 23፥43፤ ዮሐ. 19፥28፤ ማቴ. 27፥46፤ ዮሐ. 19፥30፤ ሉቃ. 23፥46) ይገኛሉ። ስለ ክርስቶስ ሞት ትርጉም «መሥዋዕት»፣ «ማስተስረያ»፣ «ቤዛ»፣ «ደም» ይመ.

**ስብ**፤ እንደ ጥንቱ አስተሳሰብ ከሁሉ የተሻለውን ክፍል ያመለክታል፤ ዘፍ. 45፥18፤ መዝ. 81፥16። ሰዎች ከመሥዋዕቱ ሥጋን ሲበሉ ስቡን አልበሉም፤ ዘሌ. 3፥17፤ 7፥22-25። ለዚህ ሥርዓት የተሰጠ ምክንያት ባይኖርም ከመሥዋዕቱ የሚጣፍጠው ክፍል ለእግዚአብሔር በእሳት ላይ እንደሚቀርብ ሁሉ፣ ስለ ራሱ እንስሳውን የሚያቀርበው ሰውም ከሕይወቱ የተሻለውን ክፍል ለእግዚአብሔር እንደሚሰጥ ይታሰባል። «መሥዋዕት»፣ «ደም» ይመ.

**ስብሰባ**፤ በልዩ ልዩ ምክንያት ሰዎች የሚገኙበት ጉባኤ። የእግዚአብሔር ሕዝብ እንዲሰበሰብ ተጠርቷል፤ ዘኍ. 1፥18፤ 8፥9፤ 10፥3፤ ዕብ. 10፥24-25።

**ስናጋ**፤ የከብት የአፍንጫ ቀለበት፤ ኢዮብ 40፥26። የእግዚአብሔር ተግሣጽ ምሳሌ ነው፤ 2ነገ. 19፥28።

**ስንዝር**፤ ከአውራ ጣት ጫፍ እስከ ታናሹ ወይም እስከ መኻል ጣት ጫፍ። ለመለኪያ ሲሆን ሀያ ሁለት ሳንቲሜትር ያህል ነው፤ ዘጸ. 28፥16። «ርዝመት» ይመ.

**ስንዴ**፤ በእስራኤልና በሌላም ብዙ አገር ከሁሉ በላይ ተወዳጅ የሆነ እህል፤ ዘጸ. 9፥32፤ 34፥22፤ ዘዳ. 8፥7-9፤ መዝ. 81፥16፤ ሐ.ሥ. 27፥38። ክርስቶስ ስንዴን ብዙ ጊዜ በምሳሌ ተጠቅሞበታል፤ ማቴ. 3፥12፤ 13፥25-30፤ ሉቃ. 22፥31፤ ዮሐ. 12፥24። «እህል»፣ «ምግብ» ይመ.

**ስእለት**፤ ሰው በፈቃዱ አንድ ነገር ለእግዚአብሔር ለማድረግ ወይም ለመስጠት ቃል ሲገባ። ብዙ ጊዜ ሰው ወደፊት ከእግዚአብሔር በረከትን ለመቀበል ስእለት ይሳላል፤ ዘፍ. 28፥20-22፤ ዘሌ. 27፤ ዘኍ. 21፥1-3፤ መሳ. 11፥30:31። ሰው ለእግዚአብሔር ብሎ ራሱን ከተፈቀደ ነገር ለማራቅ እንደ ናዝራዊ ስእለት ይሳል ይሆናል። ሆኖም ከሚሰጠው ኀላፊነት ለመሸሽ ስእለት መሳል ኃጢአት ነው፤ ማር. 7፥10-13። ሰው ስእለቱን ባይፈጽም ኃጢአት ነውና በችኰላ መሳል አይገባም፤ ዘዳ. 23፥21-23፤ ምሳ. 20፥25፤ መክ. 5፥4-5።

**ስካር**፤ ሰው መጠጥ እንዳያበዛና እንዳይሰክር ተከልክሏል፤ ዘዳ. 21፥20፤ ምሳ. 23፥21፤ 1ቆሮ. 5፥11፤ 6፥10፤ ገላ. 5፥21፤ ኤፌ. 5፥18። ኖኅ ሰከረ (ዘፍ. 9፥21)፣ ሎጥን ሁለት ሴቶች ልጆቹ አሰከሩት (ዘፍ. 19፥33-35)፣ ናባል በቤቱ ታላቅ ግብዣ ባደረገ ቀን ሰከረ (1ሳሙ. 25፥36)፣ ዳዊት ኦርዮንን አሰከረው፤ 2ሳሙ. 11፥13። «ወይን» ይመ.

**ስደተኛ፤** በመገደድ ከትውልድ አገሩ ወጥቶ በሌላ አገር የሚኖር። እስራኤል በግብጽ ስደተኞች ስለነበሩ ስደተኞችን እንዲረዱ እንጂ እንዳይንቁአቸውና እንዳያስቸግሩአቸው ተከለከሉ፤ ዘጸ. 22፥21፤ ዘዳ. 10፥19።

**ስደት፤** መከራን፥ ሥቃይን መቀበል። ክርስቶስ ተከታዮቹ እንደሚሰደዱ ተናገረ፤ ማቴ. 10፥23፤ ማር. 13፥7:13። አይሁድ በተለይ ሰዱቃውያን ሐዋርያትን አሳደዱ (ሐ.ሥ. 4፥1-6:17፤ 5፥17-18:40)፥ እስጢፋኖስን ገደሉ፤ ሐ.ሥ. 7፥54-60። ያዕቆብ በሄሮድስ ተገደለ፤ ሐ.ሥ. 12፥2። ጳውሎስ ምእመናንን አሳዳጅ ነበር፤ ሐ.ሥ. 8፥1-3፤ 22፥4። አይሁድ በየቦታው ጳውሎስን አሳደዱ፤ ሐ.ሥ. 13፥50፤ 14፥19፤ 21፥27። አሕዛብ አንዳንድ ጊዜ ጳውሎስን አሳደዱ (ሐ.ሥ. 16፥19-24፤ 19፥29)፥ አገር አስተዳዳሪዎች ብዙ ጊዜ መብቱን አስከበሩለት፤ ሐ.ሥ. 19፥37-39፤ 18፥14-17። በኋላ ግን የሮም መንግሥትና ባለ ሥልጣኖች እንደ ፈቃዳቸው ምእመናንን አሳደዱ። ክርስቲያኖች እስከ 323 ዓ.ም. ድረስም ነፃነት አልነበራቸውም። እውነተኞች ምእመናን ምን ጊዜም ስደት አለባቸው (2ጢሞ. 3፥12)፥ ስደቱንም በደስታ ሊቀበሉት ይገባቸዋል፤ ማቴ. 5፥10-12። «መከራ» ይመ.

**ስድብ፤** «መሳደብ» ይመ.

**ስግደት፤** ሰው በአምላኩ ፊት አምልኮትን፥ በታላቅ ሰው ፊት አክብሮትን ለመግለጥ ሊጐነበስ (ራስን ማዘንበል፥ እጅ ንሣ፤ ኢሳ. 46፥2)፥ በጒልበቱ ሊንበረከክ (አስተብርኮ፤ 2ዜ.መ. 6፥13)፥ ወይም በግምባሩ በመሬት ላይ ሊወድቅ (ስግደት፤ ዳን. 2፥46) ይችላል። እነዚህ ሦስት ዓይነት ስግደቶች ናቸው። እንደ ሙሴ ሕግ ስግደት ለእግዚአብሔር ብቻ የሚሰጥ የአምልኮት መግለጫ ነው፤ ዘጸ. 20፥4-6። በዚህ ምክንያት መርዶክዮስ ለሐማ አልሰገደም፤ አስ. 3፥2-4። ጴጥሮስና የእግዚአብሔር መልአክ ስግደትን አልተቀበሉም፤ ሐ.ሥ. 10፥26፤ ራእ. 22፥8:9። ክርስቶስ ግን የሰዎችን ስግደት ተቀበለ፤ አምላክ ነውና፤ ማቴ. 28፥9። ክርስቶስ በሰውነቱ ለአብ ሰገደ፤ ማቴ. 26፥39፤ ሉቃ. 22፥41። ተፈላጊ ስግደት በእውነትና በመንፈስ የሚደረግ ስግደት ነው፤ ዮሐ. 4:24።

በመ.ቅ. ውስጥ በአንዳንድ ቦታ ለሰዎችና ለመላእክት ስግደት እንደተደረገ እናገኛለን፤ ይህም የአክብሮት እንጂ፥ የአምልኮት ስግደት እንዳይደለ ልናስተውል ይገባል፤ ዳን. 2፥46፤ 2ነገ. 4፥37፤ ሐ.ሥ. 16፥29።

**ስጦታ፤**

1. በሰው ለእግዚአብሔር የሚሰጥ። መሥዋዕትና ቍርባን ስጦታዎች ናቸው፤ ዘጸ. 28፥38፤ ዘኍ. 18፥11። ሌዋውያን ለእግዚአብሔር እንደ እስራኤል ስጦታ ይቈጠራሉ፤ ዘኍ. 18፥6።

2. በሰው ለሰው የሚሰጥ። ስጦታ በበዓልና በደስታ ጊዜ (አስ. 9፥22፤ ራእ. 11፥10)፥ ከማጫ ጋር (ዘፍ. 34፥12) ይሰጣል። ከአገልግሎት ዋጋ ጋር እንደ ጉርሻ (ዳን. 2፥6)፥ ወይም እንደ እጅ መንሻ ሆኖ ይሰጣል፤ ምሳ. 18፥16። ስጦታ ለወንጌል ማስፋፊያ ይሆናል፤ ፊል. 4፥17።

3. በአብ የዘለዓለም ሕይወት ወራሾች ለወልድ ተሰጥተዋል፤ ዮሐ. 6፥37-40፤ 17፥1-2።

4. በእግዚአብሔር ለሰው የሚሰጥ የዘለዓለም ሕይወት (ሮም 6፥23)፥ ደኅንነት (ሮም 5፥17)፥ መንፈስ ቅዱስ (ሐ.ሥ. 2፥38፤ «መንፈስ ቅዱስ 7.» ይመ.)፥ እምነት (ኤፌ. 2፥8)፥ እነዚህ ሁሉ ከእግዚአብሔር ለሰው ይሰጣሉ።

5. ክርስቶስ በመሲሕነቱ መንፈስ ቅዱስን፥ መሪዎችዋንም ለቤ.ክ. ሰጥቷል፤ ዮሐ. 15፥26፤ ኤፌ. 4፥7-11።

6. መንፈስ ቅዱስ ብዙ ስጦታዎችን ለቤ.ክ. ይሰጣል፤ የስጦታዎችም ዓይነት ብዙ ነው። አንዳንድ ስጦታዎች፥ ማለትም ትንቢትን መናገር ወይም ተአምራትን ማድረግ የመሳሰሉት ቀጥታ በመንፈስ ቅዱስ ይሰጣሉ። በማገልገል፥ በመምራት በመሳሰሉት ስጦታዎች ግን መንፈስ ቅዱስ ሰዎችን መሣሪያ አድርጎ እንደሚፈቅድ በመጠቀም የወንጌልን ሥራ ያስፋፋበታል። ስለዚህ ክርስቲያን ስጦታውን ለራሱ ክብር ሳይሆን ለማኅበር ጥቅም በፍቅር ሊጠቀምበት ይገባል። የማኅበር መሪዎችም «ሁሉ በአግባብና በሥርዓት» እንዲፈጸም የማድረግ ኀላፊነት አለባቸው፤ ዕብ. 2፥4፤ ሮም. 12፥6-8፤ 1ጴጥ. 4፥10-11፤ 1ተሰ. 5፥19-22፤ 1ቆሮ. 12፥4-11:28-31፤ 13፥1-3፤ 14፥16-40። «መንፈስ ቅዱስ 8.» ይመ.

ስጦታዎች ሁሉ በቤ.ክ. ዛሬ መታየት ይገባቸዋል ስለሚለው አመለካከት በየቤ.ክ. ልዩ ልዩ አስተያየት አለ። እግዚአብሔር እንደ ዘመኑና እንደ ቤ.ክ. ሁኔታ ሊሠራ ይችላል። ሆኖም ሃይማኖት «አንድ ጊዜ ፈጽሞ ስለተሰጠ» (ይሁዳ 3) ሌላ መገለጥንም ሆነ መገለጡን የሚያረጋግጡትን ተአምራት ዛሬ መጠበቅ አይገባንም የሚሉ አሉ። የተወሰኑት ደግሞ «በመጨረሻ ቀን» (ሐ.ሥ. 2፥17) እንኖራለንና ስጦታዎችን ሁሉ በመ.ቅ. አሳብ መሠረት መጠበቅ ይኖርብናል ይላሉ።

**ሶመያ፤** ባለጅንፎ የጦር ዣቢያ፤ ናሆም 2፥3።

**ሶምሶን፤** ከሳሙኤል በስተቀር መሳፍንት ከተባሉት የእስራኤል አዳኞችና ፈራጆች የመጨረሻው ነበረ። አባቱ የዳን ነገድ የሆነ ማኑሄ የሚባል ሰው ነበረ፥ እናቱ መካን ነበረች። የእግዚአብሔር መልአክ፥ «እስራኤልን ከፍልስጥኤማውያን እጅ ማዳን ይጀምራል» ብሎ ልጅ እንደምትወልድ ነገራት። ልጃቸው ሶምሶን ከልደቱ ጀምሮ ናዝራዊ ነበረ፤ መሳ. 13። «ናዝራዊ» ይመ.

በዚያን ዘመን ፍልስጥኤማውያን አንዳንዶቹን የእስራኤል ከተሞች ወስደው ይመኩባቸውና ይገዙአቸው ነበር፤ መሳ. 13፥1፤ 1ሳሙ. 7፥13:14። እስራኤላውያን ግን ሊዋጉአቸው አልደፈሩም፤ መሳ. 15፥11። ከዚህም የተነሣ

ሶምሶን፥ እግዚአብሔር በሰጠው ልዩ ብርታትና ኃይል (መሳ. 14፥6:19 ሌላም)፥ ብቻውን ይቃወማቸው ነበር እንጂ እንደ ጌዴዎን ሊዋጋ ሠራዊትን አልሰበሰበም። አስቀድሞ በፍልስጥኤማውያን ላይ ምክንያትን በመፈለግ አንዲት ፍልስጥኤማዊት አገባ፤ በእርስዋም ምክንያት በተጣሉ ጊዜ እህላቸውን አቃጠለ፥ ብዙዎቻቸውንም ገደለ፤ መሳ. 14፥1-15፥8። የይሁዳ ሰዎች የተቈጡትን ፍልስጥኤማውያን ፈርተው አሳልፈው ሊሰጡት ተስማሙ። ሶምሶን ግን የአህያ መንጋጋ ይዞ ከጠላቶቹ አንድ ሺህ ገደለ፤ መሳ. 15፥9-19። እስከ ሃያ ዓመት ድረስ በእስራኤል ላይ ፈራጅ ሆነ፤ መሳ. 15፥20። አንድ ጊዜ ጠላቶቹ በጋዛ ከተማ ሊይዙት ሲጠባበቁት የከተማይቱን በር መዝጊያ ነቅሎ በመውሰድ አመለጠ፤ መሳ. 16፥1-3።

ሶምሶን ኃይለኛ ጀግና የሆነው «በእምነት» ነበር፤ ዕብ. 11፥32-34። ነገር ግን በመጨረሻ ራሱን ካለመግዛቱ የተነሣ ተያዘ፤ መሳ. 16፥1:4። ደሊላ የተባለች ሴት ናዝራዊነቱን እስኪገልጥላት ድረስ ከነዘነዘችው በኋላ ለፍልስጥኤማውያን መኳንንት አሳልፋ ሰጠችው። እነርሱም ዐይኑን አሳውረው በጋዛ አሰሩት፤ መሳ. 16፥4-22። አምላካቸውን ዳጎንን ሊያመሰግኑ በተሰበሰቡ ጊዜ ሶምሶንን አስመጥተው ተዘባበቱበት። እርሱም ወደ እግዚአብሔር ጸልዮ የቤቱን ምሰሶች ገፋ፤ ቤቱ ሲወድቅ በውስጡ ከነበሩት መኳንንትና ከፍልስጥኤማውያን መካከል አያሌ ሺህ ሰዎች ተገደሉ፤ ሶምሶንም አብሮአቸው ሞተ፤ መሳ. 16፥23-31።

**ሶርያ፤** ከገሊላ በስተ ሰሜን በኩል ያለ አገር። ሶርያውያን ከአራም የተገኙ ሕዝብ ነበሩ፥ ዋና ከተማቸውም ደማስቆ ነበረ። የሶርያ መንግሥት እስከ አንጾኪያና እስከ ከርከሚሽ ተስፋፋች።

ዳዊት ሶርያን አሸነፋት (2ሳሙ. 10፥6-19)፥ በሰሎሞን ዘመን ግን ዐምፃ ነፃነትዋን መለሰች፤ 1ነገ. 11፥23-25። ከዚያም ጊዜ ጀምሮ ሶርያ በእስራኤልና በይሁዳ ላይ ብዙ ጊዜ ዘመተች፤ 2ነገ. 5፥7፤ 8፥12-13፤ 2ዜ.መ. 16፤ 18፤ 22፤ 28። የአሦር ንጉሥ በ732 ከክ.ል. ደማስቆን ሲይዝ የኢሳይያስ ቃል ተፈጸመ፤ ኢሳ. 7፥3-9፤ 17፥1-3። በአ.ኪ. ዘመን ሶርያ የሮም መንግሥት ጠቅላይ ግዛት ነበረች፤ ሉቃ. 2፥2። «አራም» ይመ.

**ሶስና፤** ሶስና በሐሰት ተከስሳ ዳንኤል እንዴት እንደፈረደላት በትልቁ የአማርኛ መ.ቅ. ከዳንኤል 1 በፊት እንደ መቅድም ሆና ታትማ ይገኛል።

**ሶባል፤** (ሱባ)፤ በኤፍራጥስ ወንዝ አጠገብ የነበረ አገር። ዳዊት የዚህን አገር ንጉሥ አድርአዛርን ገድሎ የአገሩን ሕዝብ ለእስራኤል ገባር አደረገ፤ 2ሳሙ. 8፥3:5-8፤ 10፥6። ስለዚህም ዳዊት ልዩ መዝሙር ዘመረ፤ መዝ. 60 እርእስት።

**ሶፎንያስ፤** እንደ ኤርምያስ በኢዮስያስ ዘመነ መንግሥት በይሁዳ የነበረ ነቢይ። በሶፎ. 1፥1 የተጠቀሰው ቅድመ አያቱ ንጉሥ ሕዝቅያስ ነው የሚሉ አሉ። ሶፎንያስ ማለት «እግዚአብሔር ሰውሯል» ወይም «ጠብቋል» ማለት ነው (ሶፎ. 2፥3 ይመ.)።

**የሶፎንያስ ትንቢት፤** ኢዮስያስ መንገሥ በጀመረ ጊዜ፥ ኢየሩሳሌም ከምናሴና ከአሞን ክፋት የተነሣ በኃጢአት ተሞልታ ነበር፤ ሶፎ. 1፥4-6፤ 3፥1-4። ሶፎንያስ በይሁዳ ላይ ብቻ ሳይሆን በምድር ሁሉ ላይ ስለሚመጣው የእግዚአብሔር የፍርድ ቀን ትንቢት ተናገረ፤ ሶፎ. 1፥2:14-18። እግዚአብሔርን ለሚፈልጉት ትሑታን ግን ተስፋ ሰጣቸው፤ ሶፎ. 2፥3። በመጨረሻም እግዚአብሔር ከምድር ሁሉ እንደሚሰበስባቸውና ስለ አዲሲቱ ኢየሩሳሌም ደስታ ተነበየ፤ ሶፎ. 3፥9-20። አከፋፈል ፦

1. 1፥1-2፥3፤ በሁሉም ላይ የሚመጣው ፍርድ።
2. 2፥4-15፤ በልዩ ልዩ ሕዝቦች ላይ የሚመጣው ፍርድ።
3. 3፥1-8፤ በይሁዳ ላይ የሚመጣው ፍርድ።
4. 3፥9-20፤ የእስራኤል መሰብሰብና በረከት።

**ሸለፈት፤** በወንድ አባለ ዘር ላይ ያለ ያልተገረዘ ሸፋን ወይም ወሸላነት፤ 1ሳሙ. 18፥25። የልብ ድንዳኔ ምሳሌ ነው፤ ዘዳ. 10፥16:17።

**ሸመልመሌ፤** ዝንጕርጕር ወይም ቡራቡሬ የሆነ የአረኛ በትር፤ ዘፍ. 30፥35-40፤ 31፥8-10።

**ሸማ፤** እንደ መጋረጃ ያለ ትልቅ ዐርበ ሰፊ ልብስ፤ ሐ.ሥ. 10፥11፤ 11፥5።



በ850 ዓመት ገደማ ከክ.ል. አዴር የተባለው የሶርያ ዋና አምላክ ምስል

**ሸማኔ፤** የሸማኔ ሥራ ከጥንት ጀምሮ የታወቀ ነው፤ ዘፍ. 4፥20፤ ኢዮብ 7፥6። ለቤተ መቅደስ መጋረጃ እንዲሠሩ እግዚአብሔር ለሸማኔዎች የተለየ ችሎታ ሰጣቸው፤ ዘጸ. 35፥30-35። ጳውሎስ፥ አቂላና ጵርስቅላ ድንኳን ሰፊዎች ነበሩ፤ ሐ.ሥ. 18፥2:3። ሸማኔ ሥራውን የሚያካሂደው በሱፍ፥ በግመልና በፍየል ፀጉር፥ በተልባ እግር፥ በበፍታና በሐር በጥጥም ነው፤ ምሳ. 31፥13:22:24። «ተግባረ እድ» ይመ.

**ሸምቀቆ፤** የወፍ፥ የእንስሳና የአውሬ መያዣ ወጥመድ፤ ኢዮብ 18፥10።

**ሸምበቆ፤** ቀጭን ቀርከሃ መሳይ ተክል። የሸምበቆ በትር ጥንካሬ ስለሌለው በመ.ቅ. የደካማ መንግሥት ምሳሌ ነው፤ 2ነገ. 18፥21፤ ኢሳ. 36፥6፤ ማቴ. 11፥7።

**ሸራ፤** ለዳስ፥ ለድንኳንና ለመርከብ የሚያገለግል ደርጅ ልብስ (ኢሳ. 33፥23) ለውሃ መቅጃም ያገለግላል።

**ሸነተረ፤** ተለተለ፥ ቀደደ ወይም በጣ፤ ሕዝ. 23፥34።

**ሸንጎ፤** የሕዝብ ሽማግሌዎች ሲሰበሰቡ ሸንጎ ይባላል። ዋና የአይሁድ ሸንጎ በኢየሩሳሌም ነበረ። እንደ ትውፊታቸው ሙሴ ከመረጣቸው ከሰባ ሽማግሌዎች ሲያያዝ የመጣ ነው፤ ዘኁ. 11፥16-24። ክርስቶስ በምድር ሳለ ለዚህ ሸንጎ ሰባ አባሎች ነበሩት፥ ሊቀ ካህናቱ ሊቀ መንበር ነበር። የካህናት አለቆች፥ የሊቀ ካህናቱ ዘመዶችና የአገር ታላላቅ ሽማግሌዎች የታወቁ ጻፎችም አባሎች ነበሩ፤ ማር. 15፥1፤ ሐ.ሥ. 4፥5:6። ኒቆዲሞስና የአርማትያሱ ዮሴፍ የዚህ ሸንጎ አባሎች ነበሩ፤ ማር. 15፥43፤ ዮሐ. 3፥1። ክርስቶስ በምድር ሳለ የሸንጎ አባሎች በፈሪሳውያንና በሰዱቃውያን አሳብ ተከፋፈሉ፤ ሐ.ሥ. 23፥6። የኢየሩሳሌም ሸንጎ ከሮም መንግሥት በታች ሆኖ ይሁዳን ያስተዳድር ነበር፥ ከፍተኛ ፍርድ ቤትም ነበር፤ የሞት ፍርድ ግን ሊፈርድ ሥልጣን አልነበረውም፤ ዮሐ. 18፥31:32።

**ሸክላ ሠሪ፤** ሸክላ ሠሪዎች እስከ ሦስት ሺህ ዓመት ከክ.ል. በእጅ ብቻ መልክ እየሰጡ የሸክላ ዕቃ ይሠሩ ነበር። ከዚያም በኋላ በመንኰራኵር እያሽከረከሩ መሥራት ጀመሩ። ሸክላ ሠሪ መንኰራኵሩን በእግሮቹ እያዞረ በእጁ የፈለገውን ዓይነት ቅርጽ ያዘጋጅ ነበር፤ ኤር. 18፥3:4። ጥሩ ዓይነት ሸክላ ለመሥራት ሸክላ ሠሪ ዐፈሩን ከውሃ ጋር ይረግጣል፤ ኢሳ. 41፥25። ሸክላ ሠሪ የፈለገውን ለመሥራት እንደሚችል ሁሉ፥ የእግዚአብሔርም ፈቃድ በሰው ላይ እንደዚሁ ነው፤ ኤር. 18፥5-10፤ ሮም 9፥20:21። «ተግባረ እድ» ይመ.

**ሸክም፤** ሲይዙት የሚከብድ የሚያደክም ከባድ ነገር። የእግዚአብሔርን ቃል መናገር ለነቢያት፤ ሕዝብን መምራት ለሙሴ ሸክም ተብሏል፤ ለኃጢአተኛም በደሉ በሸክም ተመስሏል፤ ዘኁ. 11፥11፤ ኢሳ. 13፥1፤ 14፥28፤ ማቴ. 11፥28-30። እውነት የሌላቸው ሁሉ ሸክሞች ናቸው፤ ኤር. 23፥33-40። የመንፈስ ድካምና ችግር፥ የፍርድ ውጤትም እንደ ሸክም ተቈጥረዋል፤ ስለዚህ ክርስቲያን የሌሎችን ችግር ማቃለል ይገባዋል። ሆኖም እያንዳንዱ እንደ ሥራው ዋጋውን ይቀበላል፤ ገላ. 6፥2:5።

**ሹልዳ፤** ታፋሽ በሚባለው የሥጋ ብልት አካባቢ የሚገኝ ቀይ ሥጋ። እስራኤላውያን ሹልዳ አይበሉም። መልአክ የያዕቆብን የጭኑን ሹልዳ በነካው ጊዜ ደንዝዞ ነበርና አለመበላቱ ለመታሰቢያ ያህል ነው፤ ዘፍ. 32፥23-32።

**ሹመት፤** ከሰዎች መካከል ተመርጦ የአገልግሎት ሥልጣን መቀበልን ለማረጋገጥ የሚሰጥ ማዕረግ። ተሿሚ ለሾመው ታማኝ መሆን አለበት። ሰው በሰው አማካይነት ቢሾምም፥ ሥልጣኑን ከእግዚአብሔር ማግኘቱን መረዳት ይኖርበታል። ኢየሱስ ራሱ በመሲሕነቱ፥ ሙሴ፥ ሊቀ ካህናት፥ ዳንኤል፥ ሐዋርያት፥ ሰብዓ አርድዕት የቤ.ክ. ሽማግሌዎችና ባለ ሥልጣናት ሁሉ የተሾሙ ናቸው፤ ዳን. 2፥48፤ ሉቃ. 10፥1፤ 22፥29፤ ሐ.ሥ. 14፥23፤ ሮም 13፥1፤ 1ጢሞ. 2፥7፤ ዕብ. 3፥2፤ 5፥1፤ 7፥28፤ 8፥3።

**ሺህ ዓመት፤** «ሺህ ዓመት» የሚለው ሐረግ በራእይ 20፥1-10 ብቻ ስድስት ጊዜ ተጠቅሷል። ስለ ሺሁ ዓመት ብዙ ጥያቄ የሚነሣ ሲሆን፥ ዋናውና 1ኛው ጥያቄ ዘመኑ የሚሆነው ክርስቶስ ዳግመኛ ከመምጣቱ በፊት ወይስ በኋላ ነው? 2ኛው ደግሞ በሺሁ ዓመት ክርስቶስ የሚነግሠው በምድር ነው ወይስ በሰማይ? 3ኛውም ጥያቄ ቤተ እስራኤል ከቤ.ክ. ጋር በትንቢት አተረጓጐም እንዴት ይገናኛል? የሚል ነው። ሺሁን ዓመት በተመለከተ ሦስት አመለካከት አለ።

1. የሺህ ዓመት ምሳሌአዊ አነጋገር፤ በዚህ አመለካከት መሠረት ሺሁ ዓመት እስከ ክርስቶስ ዳግም ምጽአት ድረስ ወንጌል የሚሰበክበትን ዘመን ሁሉ ያመለክታል። ይህ ዘመን ክርስቶስ የነገሠበት ዘመን ስለሆነ «ንጉሥ ሺህ ዓመት ይነግሥ» ከሚለው ከብ.ኪ. አነጋገር ጋር ተያይዞ ሺህ ዓመትሙላትን እንጂ ቍጥርን አያመለክትም። የሰይጣን መታሰር በ12፥4ና በማቴ. 12፥28-29 ተብራርቷል። ሰይጣን ቢታሰርና ብዙ ነገሮችን ማድረግ ቢችልም፥ ሰዎችን አምነው እንዳይድኑ ሊከለክላቸው አይችልም፤ ቍ 3። አማኞችም በመንፈሳዊ ዓለም ተቀምጠው ከክርስቶስ ጋር አሁን ይነግሣሉ፤ 1፥6፤ ኤፌ. 2፥6:7። ለእስራኤል ሕዝብ የተሰጡ የተስፋ ቃላት በተለይ በቤ.ክ. ይፈጸማሉ፤ ሐ.ሥ. 15፥13-18፤ ገላ 3፥16:29፤ 1ጴጥ. 2፥10።

2. ቅድመ ምጽአት ሺህ ዓመት፤ በዚህ አመለካከት ወንጌል በዓለም ሁሉ በመስፋፋቱ ከክርስቶስ ዳግም ምጽአት በፊት ለአንድ ሺህ ዓመት ሰዎች ለእግዚአብሔር ይታዘዛሉ፤ ሰላም በዓለም ይሰፍናል። ደግሞም በዚህ ዘመን የእስራኤል ሕዝብ ወደ እግዚአብሔር ይመለሳሉ። በተለይ ኢሳ. 11፥6-16ና ሮም 11፥25-29 ይህን ዘመን ያብራራሉ።

3. ድኅረ ምጽአት ሺህ ዓመት፤ በዚህ አመለካከት መሠረት ክርስቶስ ከተመለሰ በኋላ ምድራዊ መንግሥቱን በምድር ላይ ይመሠርታል። የእስራኤል ሕዝብ ወደ ጌታቸው ይመለሳሉ፤ ክርስቶስ ንጉሣቸው ሆኖ መላው ዓለም በሰላም ይኖራል። እንደ 2ኛው አመለካከት ሁሉ ስለ እስራኤል የተነገሩ የብ.ኪ. ትንቢቶች በሺሁ ዓመት ይፈጸማሉ።

እነዚህንና ሺሁን ዓመት ስለሚመለከቱ አስተያየቶች ራእ. 20፥1-10ን ከዮሐንስ ራእይ ጠቅላላ የአሳብ አገላለጥ፣ እንደዚሁም ከሌሎች የመጽሐፍ ቅዱሳዊ ትንቢቶች አሰጣጥ ሁሉ ጋር ማመዛዘንና ማዛመድ ያስፈልጋል። «የዮሐንስ ራእይ» ይመ.

**ሺሻቅ፤** በሰሎሞን ዘመን በግብጽ ላይ የነገሠ ንጉሥ። የናባጥ ልጅ ኢዮርብዓም ከሰሎሞን ሲሸሽ ሺሻቅ ተቀበለው፤ 1ነገ. 11፥40። በሰሎሞን ልጅ በንጉሥ ሮብዓም ላይ ዘመተ፤ 1ነገ. 14፥25:26፤ 2ዜ.መ 12፥2-12።

**ሻህኝ፤** ጭንቁር የሚባል ክፉ ቍስል። አብዛኛውን ጊዜ በአፍንጫና በከንፈር ላይ ይወጣል። በግብጽ ላይ ከወረደው መቅሠፍት አንዱ ሻህኝ ነበር፤ ዘጸ. 9፥8-12።

**ሻኛ፤** በበሬ፣ በግመል፣ በጐሽ ጀርባ ላይ እንደ ጓብ ወደ ላይ ጉብ ብሎ የሚወጣ ደንዳና ሥጋ። አብዛኛውን ጊዜ የከርማዎቹ በጣም ትልቅ ይሆናል፤ ኢሳ 30፥6።



አሦራውያን በፈረስ አንገትና በክብረ በዓል ልብስ ላይ ለጌጥ ያደርጓቸው የነበሩ ሻኩራዎች

**ሻኩራ፤** ሊቀ ካህናቱ ወደ ቤተ መቅደስ ሲገባ በቀሚሱ ዘርፍ ላይ የሚያስረው ከወርቅ የተሠራ ድምፅ የሚሰጥ ትንሽ ቃጭል፤ ዘጸ. 28፥33-35፤ 39፥25። ሻኩራ በቤት እንስሳት አንገት ላይም ይታሰር ነበር፤ ዘካ. 14፥20።

**ሼሻክ፤** ባቢል (ባቢሎን) ማለት ነው። በዕብራይስጥ ቋንቋ አንዳንድ ጊዜ ለእንቆቅልሽ ያህል የአሌፍን ፊደል በታው፣ የቤትን ፊደል በሺን፣ የጋሜልን ፊደል በሬስ፣ የላሜድን ፊደል በካፍ (በቆፍ) ... ወዘተ ለውጠው ይጽፉ ነበር። እንደዚህም ሲለወጥ ሼሻክ ባቢል ተብሎ ይነበባል፤ ኤር. 25፥26፤ 51፥41። የአለዋወጡ ዘዴ አትባሽ ይባላል።

**ሽመላ፤** ከአገር ወደ አገር የሚዘዋወር ወይም የሚዘዋወር ነጭ አሞራ። ቀመቱና እግሩ ረጅም ነው። እንቁራሪትን እህልን ይበላል፤ መዝ. 104፥16-17፤ ኤር. 8፥7። «ወፎች» ይመ.

**ሽማግሌ፤** ቃሉ በግሪክ ቋንቋ «ፕሬስቡቴሮስ» ይባላል። በግእዝም ብዙ ጊዜ «ቀሲስ፣ ቀሳውስት» ተብሎ ተተርጕሟል። በማናቸውም ሕዝብ ዘንድ ብስለት ያላቸው ሰዎች ይፈለጋሉ፤ በጥበብም በልምድም ብልጫ ያላቸው ይመረጣሉ። ብዙ ጊዜ ይህ ብልጫ ሊኖር የሚችለው በዕድሜ ሂደት ነውና ሕዝብን የሚመሩ ሰዎች ሽማግሌዎች ይባላሉ፤ ዘፍ. 50፥7፤ ዘኍ. 22፥7።

1. ሽማግሌዎች በእስራኤል፤ እስራኤላውያን ከግብጽ በወጡበት ጊዜ ሽማግሌዎች ሕዝቡን በመወከል ተንቀሳቅሰዋል፤ ዘጸ. 3፥16። ከዚያም በኋላ በተለይ 70 ሽማግሌዎች ከሙሴ ጋር በአስተዳደር ተሳትፈዋል፤ ዘጸ. 24፥1፤ ዘኍ. 11፥24-25። በየከተማውም የነበሩት ሽማግሌዎች በአስተዳደር (ሩት 4፥2)፣ ሌሎች ደግሞ በመንግሥት ደረጃ ይሠሩ ነበር፤ 1ሳሙ. 8፥4፤ 2ሳሙ. 5፥3፤ 1ነገ. 8፥1፤ 2ነገ. 23፥1፤ ሕዝ. 8፥1። በተጨማሪም ሽማግሌዎች ጸጥታንና ሕግን በማስከበር ረገድ (ዘዳ. 19፥12፤ 21፥2፤ 22፥15፤ 25፥7-10) ከፍተኛ ኀላፊነት ነበራቸው፤ የእግዚአብሔርንም ቃል በማስተማር ከካህናት ጋር ይተባበሩ ነበር፤ ዘዳ. 31፥9-13።

2. ሽማግሌዎች በአዲስ ኪዳን ዘመን፤ የአይሁድ ምኵራቦች የሚመሩት በሽማግሌዎች ነበር፤ ማር. 5፥22፤ ሉቃ. 13፥14፤ ሐ.ሥ. 13፥15። ሽማግሌዎች በአይሁድ መካከል ሥልጣን ነበራቸው። (ማቴ. 15፥2)፣ ከካህናት አለቆችም ጋር በታላቁ የኢየሩሳሌም ጉባኤ እየተገኙ አብረው ያስተዳድሩ ነበር፤ ማቴ. 26፥47:59፤ 27፥1:3: 12:20:41፤ ሐ.ሥ. 4፥5-6:23፤ 23፥14፤ 24፥1፤ 25፥15።

3. ሽማግሌዎች በቤተ ክርስቲያን፤ ቤ.ክ. በመጀመሪያ በሐዋርያት ትተዳደር ነበር፤ ሐ.ሥ. 6፥2። በኋላ ግን የኢየሩሳሌም ቤ.ክ. ሽማግሌዎች በአስተዳደር ሥራ መሳተፍ ጀመሩ፤ ሐ.ሥ. 11፥2፤ 15፥2:4:6:22:23፤ 16፥4። ጳውሎስም በአሕዛብ ዘንድ በተመሠረቱ አብ.ክ. ውስጥ ሁሉ ሽማግሌዎች እንዲሾሙ አድርጓል፤ ሐ.ሥ. 14፥23፤ 20፥17፤

ቲቶ 1፥5።

የሽማግሌ ጠባይና አገልግሎት በቲቶ 1፥5-9 ተዘርዝሯል። ብዙዎች ሽማግሌዎች በአስተዳደር ተግባር ሲሳተፉ አንዳንዶች ግን በስብከትና በማስተማር ተግባር ተሰማርተው ያገለግላሉ፤ እነርሱንም ዛሬ ቄሶች ብሎ መጥራት ተለምዷል፤ 1ጢሞ. 5፥17-19።

4. ሽማግሌዎችና ጳጳሳት፤ በግሪክ ቋንቋ «ኤጲስ ቆጶስ» ብዙ ጊዜ በእ.ኪ. «በጳጳስ» ሲተረጐም፥ መሠረታዊ ትርጕሙ «ጠባቂ»፥ «ተቈጣጣሪ» ማለት ነው። በሐዋርያት ዘመን «ጳጳስ» እና «ሽማግሌ» አንድ ዓይነት ሹመትን ያመለክቱ ነበር፤ ሐ.ሥ. 20፥17:28፤ ቲቶ 1፥5:7። «ሽማግሌ» የሰውዬውን ተፈላጊ ጠባይና ችሎታ ሲያሳይ፥ «ጳጳስ» ደግሞ ሥራውንና ኀላፊነቱን ይገልጣል። ጳውሎስ ለጢሞቴዎስ ስለ ኤጲስ ቆጶሳት (ጳጳሳት)፥ ለቲቶ ስለ ሽማግሌዎች ተፈላጊ ጠባይና ችሎታ ሲገልጥ በሁለቱ መካከል ልዩነት የለም። አለ ከተባለ፥ ለጳጳስ «ለማስተማር የሚበቃ» የሚል ግዴታን የሚገልጥ ሐረግ የተጨመረበት መሆኑ ብቻ ነው፤ 1ጢሞ. 3፥1-7፤ ቲቶ 1፥5-9። ከሐዋርያት ዘመን በኋላ ግን የቤ.ክ ሽማግሌዎች መሪ «ጳጳስ» ተባለ።

የሽማግሌ ወይም የጳጳስ ሥራ በሦስት አርእስት ሊከፈል ይችላል፥ እነርሱም ማስተማር፥ መጠበቅ፥ ማደራጀት ናቸው። በግድ ሳይሆን በውድ አገልግሎታቸውን የሚፈጽሙ ሽማግሌዎች በእረኞች ተመስለዋል፤ 1ጴጥ. 5፥1-4። ሽማግሌዎች እየጸለዩ በሽተኞችን በዘይት ይቀባሉ (ያዕ. 5፥14)፥ እጅ በመጫን ጸልየው ሰዎችን ለወንጌል ሥራ ይለያሉ፤ 1ጢሞ. 4፥14፤ ሐ.ሥ. 13፥3። ዛሬ በየቤ.ክ. ስለ ጳጳስ፥ ስለ ሽማግሌ እንዲሁም ስለ ቄስ ልዩ ልዩ የአገልግሎት ክፍፍልና የስም አጠራር አለ።

የቤ.ክ አባላት ሽማግሌዎችን እንዲያከብሯቸው፥ በሥራ እንዲደግፏቸውና እንዳያሳዝኑአቸውም ታዝዘዋል፤ 1ጢሞ. 5፥17-19፤ ዕብ. 13፥17። «የቤተ ክርስቲያን አስተዳዳር» ይመ.

**ሽባ፤** በበሽታ ምክንያት እጅና እግሩ የሰለለ፤ ማቴ. 4፥24፤ 8፥6፤ 9፥2፤ ሐ.ሥ. 8፥7፤ 9፥33። «በሽታ» ይመ.

**ሽቱ፤** ከልዩ ልዩ ተክሎች የሚቀመም እንደ ቅባት ያለ ለመድኀኒት፥ ለሰውነት መዓዛ የሚጠቅም። ሰው ሲሞት ሬሣው በሽቱ ይቀባ ነበር፤ ዘፍ. 37፥25፤ 43፥11፤ መ.መ. 4፥14፤ ማር. 16፥1፤ ዮሐ. 19፥39:40። ሙሴ ክቡር በሆነው ሽቱ የዘይት ቅብዓትን ሠራ (ዘጸ. 30፥22-29)፤ ይህም የኅብረት ምሳሌ ነው፤ መዝ. 133፥1:2።

**ሽንገላ፤** ማታለል፥ ማባበል፤ ዘሌ. 19፥16፤ መዝ. 34፥13፤ ሮም 3፥13።

**ሽኮኮ፤** በድንጋይና በዋሻ ውስጥ የምትኖር፥ መልኳ አይጥ የሚመስል፥ አካሏ ድመትን የሚያክል፥ አጭር ጆሯትና ጆሮ ያላት እንስሳ። ምግቧ ሣር፥ መንፈሷ ገር ነው፤ ዘሌ. 11፥5፤ መዝ. 104፥18፤ ምሳ. 30፥26።



**ሾላ፤** ቅጠሉ ሰፋት ያለው፥ ፍሬው ለሰውና ለወፍ ምግብ የሚሆን ዛፍ፤ 1ዜ.መ. 27፥28፤ ሉቃ. 19፥4።



የሾላ ቅርንጫፍ

**ሾተል፤** በሁለት ወገን ስለት ያለው ሰይፍ፤ ምሳ. 24፥22፤ የግርጌ ማስታወሻ።

**ሾጣጣ፤** ከሥር ወፍራም ሆኖ ከላይ ቀጭን የሆነ። ለምሳሌ የድንጋይ ሐውልት ሾጣጣ ሆኖ ይሠራል፤ ከሥሩ ይልቅ ላዩ ይቀጥናል፤ 1ሳሙ. 14፥4:5።

**ቀለም፤**

1. በብርዕ ተጠልቆ የሚጻፍበት ማንኛውም የቀለም ዓይነት፤ ኤር. 36፥18፤ 2ቆሮ. 3፥3፤ 2ዮሐ. 12፤ 3ዮሐ. 13።

2. የጨርቅ ቀለም፤ ከልዩ ልዩ ትሎችና ተክሎች ይዘጋጅ ነበር። ቀለም አግቢ (ነካሪ) ጨርቁን በተዘጋጀ ቀለም ይነክረዋል፤ የጨርቁ ቀለም በጣም እንዲጠቁር ከፈለገ ብዙ ጊዜ በቀለሙ ውስጥ ያቆየዋል፤ ዘጸ. 26፥1፤ ሉቃ. 16፥19፤ ሐ.ሥ. 16፥14። «ተግባረ እድ» ይመ.

**ቀለበት፤** ከወርቅ፥ ከብር ከሌላም የሚሠራ ለጌጥና ለክብር የሚታሰር። ቀለበት ለሥልጣን ምልክት ይሆን ነበር። በጋብቻ ወንድ ለሴት ቀለበት ይሰጣል። ብዙ ጊዜ በቀለበት ላይ አንድ ዓይነት መልክ ይቀረጽበትና እንደ ማኅተም ያገለግል ነበር፤ ዘፍ. 24፥22፤ 38፥18፤ 41፥42፤ ሐጌ 2፥23፤ ሉቃ 15፥22፤ ያዕ. 2፥2።




በ450 ዓመት ገደማ ከክ.በ. የተቀረጸ የፋርስ ቀለበትና እትሙ

**ቀላውዴዎስ፤** «ቄሣር» ይመ.

**ቀላይ፤** ጥልቅነት ያለው ባሕር፥ ውቅያኖስ፤ ነህ. 9፥11፤ ኢዮብ 38፥16:30። የፈተና ወይም የመከራ ምሳሌ ነው፤ ኢዮብ 41፥23:24። ጥልቅ የሆነ የሰውን ስሜት ሊያመለክት ይችላል፤ መዝ. 42፥7።

**ቀላጭ፤** ወንዳገረድ ለጾታው የማይገባ ዝሙትን ለመፈጸም እንደ ሴት ሆኖ ከወንድ ዘርን የሚቀበል። እንደዚሁም ሴት ከወንዳወንድ ሴት ጋር ዝሙት ስትፈጽም ቀላጭ ትባላለች፤ ሮም 1፥26፤ 1ቆሮ. 6፥9።

**ቀሌምንጦስ፤** ቀሌምንጦስ የተባለው ሰው በ90 ዓ.ም. ገደማ የሮም ጳጳስ ሆነ። በፊል. 4፥3 የተጠቀሰው ቀሌምንጦስ እርሱ ነው የሚሉ አሉ። መጽሐፈ ቀሌምንጦስም የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤ.ክ. ከጌታችን ለጴጥሮስ፥ ከጴጥሮስም ለጴጥሮስ ደቀ መዝሙር ለቀሌምንጦስ ተገልጿል ብላ ከአ.ኪ. መጻሕፍት ጋር ቈጥራ የምትቀበለው በ7 ክፍል የተከፈለ መጽሐፍ ነው። ከዚህም ሌላ በቀሌምንጦስ ስም የሚጠሩ አያሌ ጽሑፎች አሉ።

**ቀማሚ፤** ከልዩ ልዩ ተክል ሽቱንና ዕጣንን የሚያዘጋጅ ቀማሚ ለእግዚአብሔር ማደሪያ (ዘጸ. 30፥34-38)፥ ለሰውም መልካም መዓዛ ያለውን ሽቶ ያዘጋጅ ነበር፤ ምሳ. 7፥17፤ 27፥9፤ መ.መ. 3፥6።

**ቀረፋ፤** ለቅመምና ለሽቱ የሚሆን ያንድ ዓይነት ዛፍ ቅርፊት፤ ዘጸ. 30፥23፤ ምሳ. 7፥17፤ መ.መ. 4፥14፤ ራእ. 18፥13።

**ቀራንዮ፤** «ጎልጎታ» ይመ.

**ቀራጭ፤** ከነጋዴዎችና ከሕዝብ እየገመተ ቀረጥ የሚሰበስብ። የሮም መንግሥት ግብርን ለመሰብሰብ በየአገሩ ቀራጮችን ይሾም ነበር። እነርሱም በየከተማው በየመንገዱ ዳር ቀረጥን ያስከፍሉ ነበር። ብዙ ጊዜ ከመጠን በላይ በማስከፈል ትርፉን ለራሳቸው ያስቀሩ ነበር፤ ማቴ. 9፥9፤ ሉቃ. 3፥12:13፤ 19፥8። ግብር ስለሚያበዙ የሰበሰቡትንም ለባዕድ መንግሥት ስለሚሰጡ ብዙ ትርፍም ስለሚያካብቱ በእስራኤላውያን ዘንድ ቀራጮች የተጠሉ ነበሩ፥ ከማኅበርም ውጭ ነበሩ፤ ማቴ. 5፥46፤ 9፥10:11፤ 11፥19፤ 18፥17። «ግብር» ይመ.

**ቀሬና፤** በሰሜን አፍሪካ የነበረ ወደብ። ብዙ አይሁድ ይኖሩበት ነበር። የክርስቶስን መስቀል የተሸከመው ስምዖን የቀሬና ሰው ነበረ፤ ሉቃ. 23፥26። የቀሬና ሰዎች በጰንጠቆስጤ ዕለት በኢየሩሳሌም ተገኝተው ነበር፤ ወንጌልንም በአንጾኪያ ሰበኩ፤ ሐ.ሥ. 2፥10፤ 6፥9፤ 11፥20፤ 13፥1።

**ቀርሜሎስ፤** ፍሬያማ ቦታ ማለት ነው። ከገሊላ ባሕር በስተምዕራብ 20 ኪ.ሜ. ርቆ የሚገኝ ተራራማ አገር። ወሰኑ እስከ ታላቁ ባሕር ይደርሳል። ኤልያስ እሳት ከሰማይ ወርዶ መሥዋዕቱን እንዲበላ፥ ዝናብም እንዲዘንብ በቀርሜሎስ ተራራ ጸለየ፤ 1ነገ. 18፥17-46። ኤልሳዕም በዚህ ቦታ ይኖር ነበር፤ 2ነገ. 4፥25። ካ. 3ሀ።



የቀርሜሎስ ተራራ

**ቀርጤስ፤** በታላቁ ባሕር፥ በአውሮጳና በትንሹ እስያ መካከል ያለ ደሴት። ከሊታውያን የቀርጤስ ሰዎች ነበሩ፤ 1ሳሙ. 30፥14። በጰንጠቆስጤ ቀን ከቀርጤስ የመጡ አንዳንድ ሰዎች በኢየሩሳሌም ነበሩ፤ ሐ.ሥ. 2፥11። ጳውሎስና ቲቶ በቀርጤስ ቤተ ክርስቲያንን መሠረቱ፤ ቲቶ 1፥5-14። ካ. 6ኀ።

**ቀስት፤** ከእንጨት የሚሠራ የፍላጻ መወርወሪያ ደጋን፤ ዘፍ. 21፥20፤ 1ዜ.መ. 5፥18፤ ኤር. 50፥14። በመዝ. 18፥34 «የናስ ቀስት» ሲል ማስፈንጠሪያውን የሚያመለክት ይመስላል። «የጦር መሣሪያ» ይመ.



ቀስተኞች

**ቀስተ ደመና፤** እግዚአብሔር ለኖኅ የሰጠው የቃል ኪዳን ምልክት፤ ዘፍ. 9፥8-17። የክብር ምሳሌ ነው፤ ሕዝ. 1፥28፤ ራእ. 4፥3፤ 10፥1።

**ቀበሮ፤** በጫካ የሚኖር፥ ከውሻ ወገን የሆነ እንስሳ፤ መሳ. 15፥4። ምግቡ ጥንብ ሲሆን የተተከለ ፍራፍሬን የሚያጠፋበት ጊዜ አለ፤ መ.መ. 2፥15። በምሳሌያዊ አነጋገር የተንኰለኛና የደካማ ሰው ምሳሌ ነው፤ ሉቃ. 13፥32፤ ነህ. 4፥3።



ቀበሮ ከግልገሎቿ ጋር

**ቀባ፤** መቀባት በመ.ቅ. ለ3 ዓይነት ነገር ያገለግላል።

1. ለአገልግሎት። ሰዎችና ዕቃዎች ለእግዚአብሔር ሥራ ሲለዩ ይቀቡ ነበር። በብ.ኪ. ዘመን የመገናኛው ድንኳንና ዕቃው ተቀብቷል፤ ዘጸ. 30፥22-29። ካህናት፥ ነቢያትና ነገሥታት ተቀብተዋል። ይህም ለተጠሩበት ሥራ በእግዚአብሔር መለየታቸውንና ለሥራቸው የሚያበቃቸው በዘይቱ የተመሰለው መንፈስ ቅዱስ መሆኑን ያሳያል፤ ዘጸ. 30፥30፤ 1ነገ. 19፥16፤ 1ሳሙ. 9፥16፤ 10፥1። ክርስቶስ በመንፈስ ቅዱስ ተቀብቷል (በመንፈስ ቅዱስ ተሞላ፤ ሐ.ሥ. 10፥38)። ምእመናን በመንፈስ ቅዱስ ይቀባሉ፤ 2ቆሮ. 1፥21:22፤ 1ዮሐ. 2፥20:27። «መሲሕ» በዕብራይስጥ «ክርስቶስ» በግሪክ ቋንቋዎች የተቀባ ማለት ነው።

2. ለአክብሮት። ተጋባዦች ለአክብሮት ይቀቡ ነበር፤ ሉቃ. 7፥46። የሰዎች ሬሣ ሳይቀበር ሽቱ ይቀባ ነበር፤ ማር. 14፥8፤ 16፥1።

3. ለሕክምና። ቍስለኞችና ሌላም በሽታ ያለባቸው በዘይት ይቀቡ ነበር፤ ማር. 6፥13፤ ሉቃ. 10፥34፤ ያዕ. 5፥14። «ዘይት» ይመ.

**ቀትር፤** ከቀኑ ስድስት ሰዓት፥ ፀሐይ የምትሞቅበት ጊዜ፤ መዝ. 37፥6፤ 91፥6።

**ቀናተኛ፤** በመልካምም ሆነ በክፉ ለአንድ ነገር የሚቀና፤ ዘፍ. 37፥11፤ 1ነገ. 19፥14፤ ሐ.ሥ. 22፥3። ከመቃብያን ጊዜ ጀምሮ የእስራኤልን ነፃነት በኃይል ለማግኘት የተነሡ አይሁድ ቀናተኞች ይባሉ ነበር። ሐዋርያው ስምዖን ከእነርሱ አንዱ ሳይሆን አይቀርም፤ ሐ.ሥ. 1፥13። «ቅንዓት» ይመ.

**ቀን፤** 1. ከፀሐይ መውጫ እስከ መግቢያ ዐሥራ ሁለቱ ሰዓት፤ ዘፍ. 1፥5። 2. ሃያ አራቱ ሰዓት፤ ዘፍ. 1፥5። እስራኤላውያን ከፀሐይ መግቢያ፤ ሮማውያን ከእኩለ ሌሊት ቀኑን ይቈጥሩ ነበር። 3. ያልተወሰነ ጊዜ፤ እብ. 12። 4. አንድ ዓይነት ድርጊት የሚፈጸምበት ጊዜ፤ ዮሐ. 9፥4፤ 2ቆሮ. 6፥2።

**ቀንበር፤** ከእንጨት የሚሠራ የግብርና መሣሪያ። ሁለት በሬዎች ጐን ለጐን ይጠመዱበታል። በአንድ ቀንበር የተጠመዱ በሬዎች ጥምድ ይባላሉ። በመ.ቅ. ዘመን ገበሬዎች አብዛኛውን ጊዜ በሬዎችን፥ አንዳንድ ጊዜ አህያን በቀንበር ይጠምዱና ያርሱ እንደነበረ እናነባለን፤ ዘዳ. 22፥10፤ ኢዮብ 1፥14፤ አሞጽ 6፥11:12፤ ሉቃ. 14፥19። በምሳሌነት ቀንበር በግፍ መገዛትንና ጭቆናን መታዘዝንም ያመለክታል፤ 1ነገ. 12፥4:9-11፤ ኢሳ. 9፥4። ቀንበርን ከአንገት መጣልና መስበርም ነፃነት ማግኘት ማለት ነው፤ ዘፍ. 27፥40፤ ኤር. 2፥20። የክርስቶስን ቀንበር መሸከም ከእርሱ ጋር ተባብሮ ከእርሱ መማር እንደ እርሱ መሥራት ማለት ነው፤ ማቴ. 11፥29። ምእመናን በወንጌል ሥራ አብረው የተጠመዱ ናቸው፤ ፊል. 4፥3። ሁለት ዓይነት እንስሳት በአንድ ቀንበር መጥመድ ክልክል ነበር (ዘዳ. 22፥10)፥ እንደዚሁም ምእመናን ከማያምኑ ጋር መተባበር አይገባቸውም፤ 2ቆሮ. 6፥14።



በበሬዎች አንገት ላይ የሚጫን ቀንበር

**ቀንዲል፤** ማብሪያ። የዘይትና የሰም መብራት ማብሪያ፤ ዘጸ. 40፥4:25፤ ዘኍ. 4፥9።

**ቀንድ፤** በእንስሳት ራስ ላይ የሚበቅል ጠንካራ አፅቅ፤ ዘፍ. 22፥13፤ ዳን. 8፥5፤ ዘዳ. 33፥17። ከቀንድ ልዩ ልዩ መሣሪያ ይሠራል። የዘይት መያዣ (1ሳሙ. 16፥1)፥ ቀንደ መለከት፤ ኢያሱ 6፥5። ቀንድ በምሳሌነት ኃይልን (1ነገ. 22፥11፤ መዝ. 132፥17፤ ሉቃ. 1፥69)፥ ክብርን (1ሳሙ. 2፥1)፥ ሥልጣንን (1ሳሙ. 2፥10)፥ ንግሥን (ሕዝ. 29፥21) ያመለክታል። በብ.ኪ. መሠዊያዎች ላይ



ካህን ቀንደ መለከት ሲነፋ

በአራት ማዕዘን የቆሙት ቅርጾች ቀንዶች ተብለዋል፤ የመሥዋዕትም ደም ይረጭባቸው ነበር፤ ዘጸ. 29፥12፤ ዘሌ. 4፥7። አዶንያስና ኢዮአብ ከሰሎሞን በሸሹ ጊዜ የመሠዊያውን ቀንድ ይዘው ተማጠኑ፤ 1ነገ. 1፥49-53፤ 2፥28-34።

**ቀኝ እጅ መስጠት**፤ የቤ.ክ. መሪዎች ሰዎችን ለአባልነት ሲቀበሉ ወይም ለአገልግሎት ሲልኩአቸው ቀኝ እጃቸውን ዘርግተው ይጨብጡአቸው ነበር፤ ገላ. 2፥9።

**ቀዓት**፤ ከሌዊ ሦስት ልጆች ሁለተኛው፤ ዘፍ. 46፥11። እስራኤላውያን በምድረ በዳ ሲጓዙ ቀዓታውያን ታቦቱንና ሌሎች የተቀደሱ ዕቃዎችን በትከሻቸው ይሸከሙ ነበር፤ ዘኍ. 3፥27-32፤ 7፥9። ዳዊት ታቦቱን ወደ ጽዮን ሲያወጣ ያገለግሉ ነበር፤ 1ዜ.መ. 15፥5:15። የሙሴና የአሮን አባት እንበረም ከቀዓት ወገን ነበረ፤ ዘጸ. 6፥18:20።

**ቀያፋ**፤ ዮሴፍ ቀያፋ የተባለው ከ18 ዓ.ም. እስከ 36 ዓ.ም. ድረስ በኢየሩሳሌም ሊቀ ካህናት ነበረ። ኢየሱስን ለማስያዝ ከሌሎች የካህናት አለቆችና ከሽማግሌዎች ጋር ተማከረ፤ ማቴ. 26፥3-5። ፍርድም እንዲፈረድበት በኢየሱስ ላይ ምክንያት ፈለገ፤ ማቴ. 26፥57-68፤ ዮሐ. 11፥49-53። ጴጥሮስና ዮሐንስ በእርሱ ፊት ተመረመሩ፤ ሐ.ሥ. 4፥6-22። «ሐና» ይመ.



ቀንዲል

**ቀይ**፤ የደምን መልክ በመያዝ ሕይወትን፥ ኃይልን፥ ክብርንና አደጋን ሊያሳስብ ይችላል፤ ዘፍ. 49፥12፤ ምሳ. 23፥31፤ ማቴ. 16፥2-3፤ ዮሐ. 19፥5፤ ራእ. 12፥3፤ 17፥3-4።

**ቀደሰ**፤ ለየ፥ አከበረ፥ ከክፉነት ወደ መልካምነት ለወጠ፤ ዮሐ. 17፥17:19። «ቅዱስ» ይመ.

**ቀጋ**፤ ነጭ አበባና ጥሩ ሽታ ያለው፥ ፍሬው የሚበላ፥ ባለ እሾክ የጫካ ተክል፤ መ.መ. 4፥14።

**ቀጠና**፤ ራብ፥ ችግር፤ ኢዮብ 30፥3።

**ቀጭኔ**፤ ረዥም የሆነ ቀጭን ሰር፤ 1ነገ. 18፥28። «የጦር መሣሪያ» ይመ.

**ቀጰዶቅያ**፤ ከገላትያ በስተምሥራቅ የሚገኝ አገር። የሚገኘውም ዛሬ ቱርክ ተብሎ በሚጠራው አገር ውስጥ ነው፤ ሐ.ሥ. 2፥9፤ 1ጴጥ. 1፥1:2። ካ. 6በ።

**ቀጸላ**፤ የራስና የፊት መሸፈኛ፤ 1ነገ. 21፥38:41።

**ቁምራን**፤ በጨው ባሕር ዳር በስተሰሜንና በስተምዕራብ የነበረ ገዳም። ቦታው ምናልባት «የጨው ከተማ» በመባል ይታወቅ የነበረው ይሆናል፤ ኢያሱ 15፥62። 150 ከክ.በ. ገደማ አንዳንድ የአይሁድ ካህናት በቤተ መቅደስ ከሚያገለግሉት ካህናትና ከመቃብያን ጋር ተጣልተው በቁምራን በኅብረት መኖር ጀመሩ። መሪያቸውም «የጽድቅ መምህር» ተባለ። በኋላም እነዚህ ሰዎች ኤሲናውያን ተባሉ። ሮማውያን በ68 ዓ.ም. ወደ ገዳማቸው በሄዱ ጊዜ ብዙ የጽሑፍ ጥቅልሎችን በአቅራቢያው ባሉ ዋሻዎች ደበቁ። ጥቅልሎቹ በአንድ ዐረባዊ እረኛ በ1947 ዓ.ም. በድንገት ተገኙ። ጥቅልሎቹም «የጨው ባሕር ጥቅልሎች» ተብለው ተሰየሙ። ብዙዎቹ ከክርስቶስ በፊት የተጻፉ ናቸው። በመካከላቸውም ከአስቴር መጽሐፍ በቀር በሙሉ ወይም በከፊል የብ.ኪ. መጻሕፍት ይገኛሉ። ካ. 5ሠ።

**ቁራ**፤ ጥምብን የሚበላ ጥቁር አሞራ። የኖኅ መልእክተኛ፤ ዘፍ. 8፥7። ቁራዎች ነቢዩ ኤልያስን መግበዋል፤ 1ነገ. 17፥4-6። እግዚአብሔር እነርሱን ይመግባቸዋል፤ መዝ. 147፥9፤ ሉቃ. 12፥24። «ወፎች» ይመ.

**ቁባት**፤ ወንዶች ካገቡ በኋላ ወይም ሳያገቡ ከሚስት በታች አድርገው የሚያስቀምጡአቸው ሴቶች፥ የጭን ገረዶች፤ ዘፍ. 16፥1፤ 22፥24፤ መሳ. 8፥31፤ 19፥1:2፤ 2ሳሙ. 3፥7፤ 5፥13። የሙሴ ሕግ ቁባት ይፈቅድ ነበረ፤ ዘጸ. 21፥7-11፤ ዘዳ. 21፥10-14። በብ.ኪ. ዘመን ብዙ የታወቁ ሰዎች ቁባቶች ነበሩአቸው፥ አብርሃም (ዘፍ. 25:6)፥ ያዕቆብ

(ዘፍ. 35፥22)፥ ዳዊት (2ሳሙ. 5፥13)፥ ሰሎሞን (1ነገ. 11፥3) ... ወዘተ። ሆኖም ቁባቶቻቸው ጭቅጭቅ እንጂ ደስታ አላተረፉላቸውም።

**ቂም፤** በበደል ምክንያት ፍቅርን አጥቶ በቅርታ ውስጥ መገኘት፥ በቀልን መፈለግ፤ ዘሌ. 19፥18፤ ሮም 12፥19።

**ቄሣርያ፤** ክርስቶስ በምድር ሳለ በእስራኤል አገር የሮማዊ አስተዳዳሪ ዋና መቀመጫ። አብዛኛውን ጊዜ የአገር አስተዳዳሪው በቂሣርያ ቢኖርም፥ አንዳንድ ጊዜ ወደ ኢየሩሳሌም ይወጣ ነበር። ስለዚህ ጳውሎስ በቂሣርያ በሁለት የአገር አስተዳዳሪዎች ፊት ቀርቧል፤ ሐ.ሥ. 23፥23:24፤ 24፥10፤ 25፥3-6።

በቂሣርያ ሁለት ዓመት ታሰረ፤ ሐሥ. 24፥27። ቂሣርያ ለሮም ንጉሥ ለቄሣር ክብር በንጉሥ ሄሮድስ ተሠራ፤ በጳውሎስ ዘመን እስከ መቶ ሺህ ሰው ይኖርበት ነበር። የወንጌል ሠራተኛው ፊልጶስ (ሐ.ሥ. 8፥40፤ 21፥8) ደግሞም የመቶ አለቃው ቆርኔሌዎስ በቂሣርያ ይኖሩ ነበር፤ ሐ.ሥ. 10፥1። ከ. 5መ። «ፊልጶስ ቂሣርያ» ይመ.

**ቂርያትይዓሪም፤** ከኢየሩሳሌም ወደ ምዕራብ 15 ኪ.ሜ ርቆ የሚገኝ ከተማ። የዳን ሰዎች የሚካን የጣዖት ምስልና ኤፉድ ከዚህ ቦታ ወሰዱ፤ መሳ. 18። የእግዚአብሔር ታቦት በቂርያትይዓሪም በአሚናዳብ ቤት ሃያ ዓመት ተቀመጠ፤ 1ሳሙ. 7፥1:2።

**ቂሮስ፤** ከክ.በ. ከ559 ጀምሮ እስከ 530 የነገሠ፥ የፋርስን መንግሥት ያቋቋመ ንጉሥ። ብዙ አገሮችን የወረረ ኃይለኛ ንጉሥ ነበረ።



በ539 ከክ. በ. ባቢሎንን ድል አድርጎ የተማረኩት እስራኤላውያን ወደ ትውልድ አገራቸው እንዲመለሱ አዋጅ አስነገረ፤ 2ዜ.መ. 36፥22-23፤ ዕዝ. 1፥1-4። ይህንም ፈቃድ የሰጣቸው በራሱ አሳብ ሳይሆን፥ በእግዚአብሔር አሳሳቢነት መሆኑን መጽሐፈ ዕዝራ ይናገራል፤ ዕዝ. 1፥1።

ቂሮስ ከመንገሡ በፊት በእርሱ አማካይነት ወደ ባቢሎን የተማረኩት የይሁዳ አገር ምርኮኞች ወደ አገራቸው እንደሚመለሱ ነቢዩ ኢሳይያስ ትንቢት ተናግሮ ነበር፤ ኢሳ. 44፥27-28፤ 45፥1።

**ቂስ፤** የንጉሥ ሳኦል አባት የነበረው ብንያማዊ። የአበኔር አባት የኔር ወንድም ነበረ፤ 1ሳሙ. 9፥1፤ 14፥50:51፤ ሐ.ሥ. 13፥21። በዚህ ስም ሌሎች አራት ሰዎች ተጠርተውበታል።

**ቂጣ፤** (የቂጣ በዓል)፤ «ፋሲካ»፥ «በዓላት» ይመ.

**ቃል፤** ከልብ የሚመነጭ፥ የአሳብ መግለጫ፥ የፈቃድ መፈጸሚያ፥ የድምፅ ፍሬ ነገር። ሰው በቃሉ ይታወቃል፤ ከቃሉ የተነሣ ይፈረድበታል፤ ማቴ. 12፥36። እግዚአብሔር ዓለምን በቃሉ ፈጠረ፤ «ይሁን» ሲል ሁሉ ሆነ፤ ዘፍ. 1፥3:9። ቃል፥ ትእዛዝ፥ ሕግ ተብሎ ይተረጐማል፤ ዘጸ. 34፥28፤ ዘዳ. 4፥13። እግዚአብሔር ፈቃዱን ለነቢያት በቃል ገለጠ፤ ኤር. 1፥9፤ ሆሴዕ 1፥1፤ ኢዩ. 1፥1። ብዙ ጊዜ ቃል እንዴት እንደመጣላቸው አልተገለጠም። ቃል አንዳንድ ጊዜ በራእይ (ዘፍ. 15፥1) ወይም በድምፅ (1ሳሙ. 3፥4) ይሰጣል። የእግዚአብሔር ቃል አይለወጥም (ዘዳ. 12፥32)፥ ለዘለዓለም ይጸናል (ኢሳ. 40፥8)፥ ሁሉን ይፈጽማል፤ ኢሳ. 55፥11። ጌታችን ኢየሱስ የእግዚአብሔር ቃል በሰው ልብ እንደሚዘራ ተናገረ፤ ሉቃ. 8፥11። ቃሉ ሰዎች ዳግመኛ እንዲወለዱ ይሠራል፥ ያሳድጋቸዋል፥ ወደ ሰማያዊ ርስት ይመራቸዋል፤ ያደርሳቸዋልም፤ ሐ.ሥ. 20፥32፤ 1ጴጥ. 1፥23-2፥3። ይህ ቃል ኢየሱስ ያስተማረው ወንጌል ነው፤ ማር. 2፥2፤ ሐ.ሥ. 6፥2፤ ገላ. 6፥6፤ 1ጴጥ. 1፥25። ቃሉ የሕይወት (ፊል. 2፥16)፥ የእውነት (ኤፌ. 1፥13)፥ የመዳን (ሐ.ሥ. 13፥26)፥ የማስታረቅ (2ቆሮ. 5፥19) የመስቀል ቃል ነው፤ 1ቆሮ. 1፥18። የእግዚአብሔር ቃል በእሳትና በመዶሻ (ኤር. 23፥29)፥ በሰይፍ (ኤፌ. 6፥17)፥ በወተት ይመሰላል፤ 1ጴጥ. 2፥2። እግዚአብሔር ሁሉን ነገር በቃሉ አደረገ ሲባል በወልድ ነውና ቃል የወልድ አካላዊ ስም ነው፤ ዮሐ. 1፥1-4:14፤ 1ዮሐ. 1፥1፤ ራእ. 19፥13።

**ቃል ኪዳን፤** ሁለት ወይም ከሁለት በላይ የሆኑ ሰዎች ሲስማሙ ነገሩን ለማጽናት ቃል ኪዳን ይገባባሉ፥ ለምሳሌ ዮናታን ከዳዊት ጋር ቃል ኪዳን ገባ፤ 1ሳሙ. 18፥3-4። እግዚአብሔር ዓለምንና ሕዝቡን የሚያስተዳድረው በቃል ኪዳን ሥርዓት ነው። በማናቸውም ቃል ኪዳን ውስጥ የቃል ኪዳን ሰጪ፥ ተቀባይ፥ የአቀባበል ምልክት፥ ተስፋ፥ የተስፋውም ምልክት ይገኛሉ። እግዚአብሔር በሰው ደግነት ሳይሆን፥ እንዲሁ በጸጋው ቃል ኪዳንን ፈቅዶ ይሰጣል። ሰዎችም ቃል ኪዳኑን ተቀብለው ቢታዘዙለት የቃል ኪዳኑን በረከት ይቀበላሉ። ቃል ኪዳኑን ሲቀበሉ እግዚአብሔር የሚታይ ምልክት ያበጃል። ይህም የቃል ኪዳኑ ማኅተም ነው። እግዚአብሔር በቃል ኪዳኑ ውስጥ ላሉት ተስፋና የተስፋ ምልክት ይሰጣቸዋል። ስለ ሰው ያለው የእግዚአብሔር አሳብ አይለወጥም። ከመጀመሪያ ጀምሮ ሰውን በጸጋው ተመልክቷል። ከሰው የሚፈለጉት ደግሞ እምነትና መታዘዝ ናቸው። እነዚህ ነገሮች ከዘመን ዘመን አይለወጡም። ይሁን እንጂ እግዚአብሔር ፈቃዱን እየገለጠ ሲሄድ ምልክቶች ይለወጣሉ። በስንጠረዡ የእግዚአብሔር ጸጋ በቃል ኪዳን እንዴት እንደተገለጠ ልናይ እንችላለን።

ዘመን ሲለወጥ የቃል ኪዳኑ ዋና መሠረት አይሰረዝም፤ ገላ. 3፥15-18። ነገር ግን የአፈጻጸሙ

| የእግዚአብሔር ቃል ኪዳን የተሰጠው | ተቀባዮች | የመቀበላቸው ምልክት (ማኅተም) | ተስፋ | የተስፋ ምልክት (ማኅተም) |
|---|---|---|---|---|
| ለአዳም ዘፍ. 2፥8-17፤ ሆሴዕ 6፥7። | አዳምና ሔዋን | መልካምና ክፉን የሚያሳውቅ ዛፍ | ሕይወት | የሕይወት ዛፍ |
| ለኖኅ ዘፍ. 9፥1-17። | የዓለም ሕዝብ | | በምድር መኖር | ቀስተ ደመና |
| ለአብርሃም ሮም 4፥11፤ ዘፍ. 17፥1-21። | አብርሃምና ዘሩ | ግዝረት | የአሕዛብ በረከት፥ የከነዓን ምድር | |
| ለሙሴ (ብ.ኪ.) ዘጸ. 19፥5:6፤24፥7:8። | የእስራኤል ሕዝብ | (ግዝረት) ሰንበት ሕዝ. 20፥10-17። | ሕይወት ቧአገራቸው | የፋሲካ መታሰቢያ |
| በክርስቶስ (አ.ኪ.) ኤር. 31፥31-34። 1 ቆሮ. 11፥23-26። | በክርስቶስ የሚያምኑ ሁሉ | ጥምቀት | የዘለዓለም ሕይወት | ቅዱስ ቍርባን |

ድርጊት ይለወጣል፤ 2ቆሮ. 3፥6-18፤ ዕብ. 8፥6-13። እግዚአብሔር ደግሞ ለዳዊት (2ሳሙ. 23፥5)፥ ለሌሎችም ሰዎች ቃል ኪዳን ገብቶላቸዋል።

ለአዳምና በክርስቶስ ለምእመናን የተሰጡ ቃል ኪዳኖች በሚከተለው መንገድ እርስበርስ ተዛምደው ተገልጠዋል። እግዚአብሔር ከአዳም ጋር የሥራ ቃል ኪዳን አደረገ። አዳም ቢታዘዝ ኖሮ ለእርሱና ለዘሩ የዘልዓለምን ሕይወት ያስገኝ ነበር፤ ባለመታዘዙ ግን የኃጢአትን ፍርድ በእርሱና በዘሩ ላይ አስከተለ፤ ሮም 5፥12-21። ክርስቶስ ሁለተኛው አዳም ስለሆነ በእርሱ ለሚያምኑት ሕይወት አስገኝቶላቸዋል፤ 1ቆሮ. 15፥20:45-50።

**ቃርሚያ፤** እስራኤል መከር ከሰበሰቡ በኋላ የወደቀ ወይም የቀረ ፍሬ ለድሆች ይተዉ ነበር፤ ዘሌ. 19፥9:10፤ መሳ. 8፥2፤ ሩት 2፥2:16፤ ኢሳ. 17፥6።

**ቃና፤** ከናዝሬት ሰባት ኪ.ሜ. ርቆ በስተሰሜን የነበረ መንደር። የናትናኤል አገር ነበር፤ ዮሐ. 21፥2። በዚህ መንደር ክርስቶስ ወደ ሰርግ ታድሞ ሄደ (ዮሐ. 2፥1-12)፤ በቃና የቅፍርናሆምን ሹም ልጅ በቃሉ ፈወሰ፤ ዮሐ. 4፥46-54። ካ. 5ለ።

**ቃየል፤** (ቃየን) የአዳምና የሔዋን የመጀመሪያ ልጅ፤ ዘፍ. 4፥1። ቃየል ክፉ ልብ ነበረው፤ 1ዮሐ. 3፥12። እግዚአብሔርም በመሥዋዕቱ ያልተደሰተበት ምክንያት ይህ ነው። ወንድሙ አቤል ግን እግዚአብሔርን የሚፈራ ስለሆነ የእርሱ መሥዋዕት ተወደደ። ቃየል ይህን በመመልከት በምቀኝነት ተመርዞ ወንድሙን ጠላው።

እግዚአብሔር ብስጭቱን ዐውቆበት በወንድሙ ላይ ክፉ ሥራ እንዳይሠራ ቢያስጠነቅቀውም፥ ቃየል የፈጣሪውን ምክር በመናቅ ወንድሙን ገደለው፤ ዘፍ. 4፥3-8።

ይህ ክፉ ሥራ ከእግዚአብሔር ፊት መሰደድን አስከተለበት። ከእግዚአብሔርም ፊት ወጣ። እንደ ኰብላይና እንደ ተቅበዝባዥም ሆኖ ኖድ በተባለው አገር ተቀመጠ። በዚያም ሄኖሕ የተባለችውን ከተማ ቈረቈረ፤ ዘፍ. 4፥12-17።

**ቃዴስ፤** ቅዱስ ማለት ነው። ከከነዓን በስተደቡብ ያለ ምድረ በዳ ስፍራ፤ መዝ. 29፥8። ቃዴስ በርኔ ተብሎም ይጠራል፤ ዘኍ. 32፥8። እስራኤላውያን ከግብጽ አገር ወደ ከነዓን ሲጓዙ በቃዴስ ሰፈሩ። ዐሥራ ሁለቱ ሰላዮች ከከነዓን ከተመለሱ በኋላ፥ ሕዝቡ እግዚአብሔር ወደ አገራቸው ሊያደርሳቸው እንደሚችል የተነገራቸውን ስለተጠራጠሩ እስከ ሠላሳ ስባት ዓመት ድረስ በቃዴስ እንዲቀመጡ ተፈረደባቸው፤ ዘዳ. 1፥46። የሙሴ እኅት ማርያም በቃዴስ ሞተች። ሙሴም በዚህ ቦታ ድንጋዩን በመምታት እግዚአብሔርን አሳዘነው፤ ዘኍ. 20፥1-13። ካ. 2ሠ።

**ቃዴስ ንፍታሌም፤** በአሶርና በዳን መካከል የሚገኝ የከነዓናውያን ንጉሥ ከተማ፤ ኢያሱ 12፥22፤ 19፥35-38። በኋላም የመማጠኛ ከተማ ሆነ (ኢያሱ 20፥7)፥ የባርቅም ከተማ ነበር፤ መሳ. 4፥6።

**ቄሣር፤** መጀመሪያ የአንድ ትልቅ የሮም ቤተሰብ ስም ነበር፥ በኋላም ለሮም መንግሥት ዋና የማዕርግ ስም ሆነ። በመ.ቅ. ውስጥ የተጠቀሱ ቄሣሮች የሚከተሉት ናቸው።

1. አውግስጦስ (27 ከክ.ል. እስከ 14 ዓ.ም.፤ ሉቃ. 2፥1።)

2. ጢባርዮስ (14-37 ዓ.ም.፤ ሉቃ. 3፥1።)

3. ቀላውዴዎስ (41-54 ዓ.ም.፤ ሐ.ሥ. 11፥28፤ 18፥2።)

4. ኔሮን (54-68 ዓ.ም.) ኔሮንም በአ.ኪ. ውስጥ በስም አልተጠቀሰም፥ ሆኖም እላይ ከተጠቀሱት ቄሣሮች ሌላ በመ.ቅ. ቄሣር ወይም ንጉሥ በመባል ብቻ የሚጠራው ኔሮን እንደሆነ ግልጥ ነው። «ሮም»፥ «ገዥ»፥ «ንጉሥ»፥ ገጽ 94 ይመ.



ቀላውዴዎስ ቄሣር ከቅጠል የተሠራ አክሊል እንደደፋ የሚያሳይ ሥዕል

**ቄስ**፤ «ካህን»፥ «ሽማግሌ» ይመ.

**ቄናውያን**፤ በከነዓን አገር ይኖሩ የነበሩ የምድያም ነገድ፥ የቄና ሰዎች። የሙሴ አማት ቄናዊ ነበር። እስራኤል ወደ ከነዓን ሲገቡ ቄናውያን ከይሁዳ ሕዝብ ጋር ተባበሩ። ሔቤርና ሬካብ ቄናውያን ነበሩ፤ ዘፍ. 15፥19፤ ዘጸ. 2፥16፤ መሳ. 1፥16፤ 4፥11፤ 1ሳሙ. 15፥6፤ 1ዜ.መ. 2፥55።

**ቄኔዝ**፤ 1. በከነዓን ይኖር የነበረ ነገድ፤ ዘፍ. 15፥19። 2. ቄኔዝ የዔሳው የልጅ ልጅ የኤልፋዝ ልጅ፤ ዘፍ. 36፥15። 3. የካሌብ አባት ወይም ቅድም አያት፤ ኢያሱ 14፥6፤ 15፥17። አንዳንድ ሊቃውንት ሦስቱም አንድ ናቸው ብለው ይገምታሉ።

**ቄዳር**፤ ኃያል ማለት ነው። 1. የእስማኤል ልጅ፤ ዘፍ. 25፥13። 2. ከቄዳር የተገኘ ነገድ በዓረብ ምድረ በዳ ይኖር የነበረ ዘላን ሕዝብ፤ መዝ. 120፥5። በጎችን እያረባ ከጢሮስ ጋር ይነግድ ነበር፤ ኢሳ. 60፥7፤ ሕዝ. 27፥21። በድንኳን ነዋሪ ነበር፤ መ.መ. 1፥5። ቀስተኞቻቸው የታወቁ ነበሩ (ኢሳ. 21፥16:17)፥ ነገር ግን በናቡከደነፆር ድል ሆነ፤ ኤር. 49፥28:29።

**ቄድሮን**፤ በኢየሩሳሌምና በደብረ ዘይት መካከል ያለው ወንዝና ሸለቆ። ቦታው የንጉሥ ሸለቆ (ዘፍ. 14፥17፤ 2ሳሙ. 18፥18)፥ የኢዮሣፍጥም ሸለቆ ይባላል፤ ኢዩ. 3፥2። በክረምት ወንዙ እስከ ጨው ባሕር ይፈስሳል፤ በበጋ ግን ይደርቃል። ሳሚ ቄድሮንን እንዳይሻገር በሰሎሞን ተከለከለ፤ 1ነገ. 2፥37። ዳዊት ከአቤሴሎም ሲሸሽ (2ሳሙ. 15፥23)፥ ኢየሱስ ወደ ጌቴሴማኒ ሲሄድ ይህን ወንዝ ተሻገረ፤ ዮሐ. 18፥1። «የኢዮሣፍጥ ሸለቆ» ይመ.

**ቄጠማ**፤ በወንዝ ዳር የሚበቅል፥ ለቤት ጉዝጓዝ የሚሆን ሣር፤ ዘጸ. 2፥3:5፤ ኢዮብ 8፥11።

**ቅልጣን**፤ ምቾት፥ ቅምጥልነት። ቅልጣናም ሲል ግን የደላው ወይም የደላት የተመቻት ማለት ነው፤ ኢሳ. 47፥1።

**ቅልጥም**፤ አጥንትና የአጥንት ስብ፤ ኢዮብ 21፥24። በምሳሌነት የደስታ ምልክት ነው፤ ኢሳ. 25፥6።

**ቅሬታ**፤ ከሞት፥ ከስደትና ከሌላም ክፉ ነገር የተረፈ፥ የቀረ ሕዝብ ማለት ነው፤ 2ነገ. 19፥4:31። የእግዚአብሔር ሕዝብ ምንም እንኳን ኃጢአት ቢሠሩ እግዚአብሔር ከመካከላቸው ቅሬታን ለራሱ ያስቀራል፤ ሮም 9፥27-28፤ 11:3-5። እንደዚሁም ከዚህ በፊት በኃጢአት ምክንያት በሕዝቡ ላይ ፍርድ ባመጣ ጊዜ ቅሬታን አስቀርቷል፤ በቅሬታውም መሠረት ሕዝቡን እንደገና አስነሥቷል፤ ዕዝ. 9፥8፤ ኢሳ. 4፥3:4፤ 6፥13፤ ኤር. 23፥3፤ ሶፎ. 3፥13።

**ቅቤ**፤ ከላም ወተት የሚገኝ ለስላሳ ምግብ፤ ዘዳ. 32፥14፤ 2ሳሙ. 17፥28-29፤ ኢዮብ 20፥17፤ 29፥6፤ መዝ. 55፥21፤ ምሳ. 30፥33፤ ኢሳ. 7፥15:22።

**ቅብዓት (ቅባት)**፤ ከልዩ ልዩ እንጨቶች ተቀምሞና ተነጥሮ የሚወጣ ፈሳሽ ዓይነት፤ ዘጸ. 30፥22-32። የመንፈስ ቅዱስ ምሳሌ ነው፤ 1ዮሐ. 2፥20:27። «ቀባ» ይመ.

**ቅብጥ**፤ የግብጽ አገር ወይም ጥንታዊው የግብጽ ቋንቋ። የቅብጥ ቋንቋ በአማርኛ መ.ቅ. ውስጥ ተጠቅሶ አይገኝም። በግእዝ አ.ኪ. ግን በአንዳንድ ቅጂዎች በዮሐንስ ራእይ 9፥11 በዕብራይስጥ አብዶን የተባለው የጥልቅ መልአክ በቅብጥ አርማቅጦን ይባላል ይላል።

**ቅትርት**፤ የመንኰራኵር ብረት ወይም መወጠሪያ መሳይ እንጨት፤ 1ነገ. 7፥33።

**ቅኔ**፤ በልዩ ልዩ ዓይነት ግጥም የሚቀርብ ንግግር ወይም ጽሑፍ ቅኔ ይባላል። ቅኔ ጥልቅ ምሥጢርና ምሳሌ አለበት፤ መሳ. 5፥1፤ 2ሳሙ. 1፥17፤ 22፥1፤ መዝ. 33፥3፤ ኢሳ. 5፥1፤ 38፥20፤ ኤፌ. 5፥19። ካህናት ምሥጢር ባለው ቅኔ በመሰንቆ ያዜሙ ነበር፤ 1ዜ.መ. 15፥20። በአነባበብ ስልቱ ይለያል እንጂ ቅኔ ራሱ መዝሙር ነው፤ ራእ. 14፥3። ቅኔ በየቀኑ ሊደረስና አዲስ እየሆነ ሊቀርብ ይችላል፤ መዝ. 149:1።

**ቅን፥ ቅንነት**፤ በመልካም ጎሊናው እየተመራ የሚኖር፥ ተንኰል የሌለበት፥ ትክክለኛ፤ ዘፍ. 20፥5-6፤ ኢዮብ 2፥3፤ መዝ. 32፥11፤ 33፥1፤ ምሳ. 11፥3፤ ዮሐ. 1፥48።

**ቅንዓት**፤ ቅናት፤

1. ለሌላ ሰው የሆነውን ለራስ መፈለግ (መዝ. 73፥3)፤ ምእመናን መቅናት አይገባቸውም፤ ሮም 13፥13፤ 1ቆሮ. 13፥4፤ 2ቆሮ. 12፥20፤ ገላ. 5፥20፤ ፊል. 1፥15፤ 1ጢሞ. 6፥4:5፤ 1ጴጥ. 2፥1።

2. ክብር ወይም ፍቅር ወደ ሌላ ሲያልፍ መቈጣት፤ ማቴ. 27፥18፤ ሐ.ሥ. 13፥45፤ 17፥5። ሚስት

ለባልዋ ያላትን ፍቅር ለሌላ ስትሰጥ ባል መቅናት ይገባዋል፤ ዘኍ. 5፥14፤ ምሳ. 6፥34፤ መ.መ. 8፥6።

3. የእግዚአብሔር ቅንዓት ማለት ለእርሱ የሚገባው ክብርና ፍቅር ለሌላ እንዳይሰጥ መፈለጉን ያመለክታል፤ ዘጸ. 20፥6፤ 34፥14፤ ዘዳ. 4፥23-24፤ 5፥9፤ 6፥14-15፤ ሕዝ. 39፥25፤ 1ቆር. 10፥21-22፤ መዝ. 78፥58፤ ኢዩ. 2፥18፤ ዘካ. 1፥14፤ 8፥2፤ ያዕ. 4፥5። ሰው ስለ እግዚአብሔር ቅንዓት ሊኖረው ይችላል፤ 1ነገ. 19፥10:14፤ 2ቆሮ. 11፥2።

**የቅንዓት ጣዖት**፤ እግዚአብሔርን የሚያስቀና በቤተ መቅደስ የተሠራ ጣዖት ነበር፤ ሕዝ. 8፥3-5። ከዚህም በፊት ምናሴ ምስልን በቤተ መቅደስ በማቆም እግዚአብሔርን አስቀንቶ ነበር፤ 2ዜ.መ. 33፥7-15።

**ቅንጣት**፤ አነስተኛ የእህልና የተክል ፍሬ፤ ማቴ. 13፥31:32። «ዘር» ይመ.

**ቅኝ አገር**፤ በባዕድ መንግሥት የሚገዛ አገር። በሐዋርያው በጳውሎስ ዘመን ፊልጵስዩስ የሮም ቅኝ አገር ነበረች፤ ሐ.ሥ. 16፥12።

**ቅዱሳን**፤ የእግዚአብሔር የሆኑ ሁሉ ቅዱሳን ይባላሉ፤ 2ዜ.መ. 6፥41፤ መዝ. 16፥3፤ ዳን. 7፥27። በአ.ኪ. የቤ.ክ. አባሎች ሁሉ ቅዱሳን ተብለው ይጠራሉ፤ ሐ.ሥ. 9፥13፤ 1ቆር. 1፥2፤ 6፥1:2፤ 14፥33፤ 16፥1።

**የቅዱሳት መጻሕፍት ትርጉም**፤

በዕብራይስጥ ቋንቋ የተጻፈው ብሉይ ኪዳን ከጌታችን ልደት በፊት ወደ ግሪክ ቋንቋ ተተርጒሞ ነበር፤ ትርጒሙም ሴፕቱአጊንት (የሰባ ሊቃናት ትርጒም) ተብሎ ይጠራል። ከጌታችን ልደት ወዲህ ይህን ትርጒም ለማቃናትም ሆነ አዲስ የግሪክ ትርጒምን ለማዘጋጀት ከደከሙት ሊቃውንት በጣም የታወቁት ሲማኩስ (2ኛው መቶ ክፍለ ዘመን)፥ አኩላ (2ኛው መቶ ክፍለ ዘመን)፥ ቲዎድቲዮን (2ኛው መቶ ክፍለ ዘመን) እና ሊኪያኑስ (3ኛው መቶ ክፍለ ዘመን) የተባሉት ናቸው።

በተጨማሪም ብ.ኪ. ወደ አራማይክ ተተረጐመ፤ አንዳንድ ማብራሪያም ተጨመረበት። ከእነዚህ ትርጓሜዎች በጣም የታወቁት ኦንክሉስና ዮናታን የተባሉት የአይሁድ ሊቃውንት የተረጐሙአቸው ናቸው።

በኢትዮጵያም በ5ኛው መቶ ክፍለ ዘመን የመጡ ተሰዓቱ (ዘጠኙ) ቅዱሳን፥ ቅዱሳት መጻሕፍት ወደ ግእዝ እንዲተረጐሙ አደረጉ። ከእነርሱ ዘመን ቀደም ብሎ አንዳንድ መጻሕፍት በእነአባ ሰላማ ከሣቴ ብርሃን (በ4ኛው መቶ ክፍለ ዘመን) ጥረት ተተርጒመዋል። ከዚያም ወዲህ አባ ሰላማ መተርጒመ መጻሕፍት (በ14ኛው መቶ ክፍለ ዘመን) በትርጒም ሥራ ብዙ ደክመውበታል።

በግብጽም ቅዱሳት መጻሕፍት ወደ ቅብጥ ቋንቋ ተተረጐሙ፤ ይህ ቋንቋ በየክፍለ አገሩ ጥቂት ለየት የሚል ስለሆነ ትርጒሙ ሦስት ዓይነት ነው።

በሶርያም ብዙ ትርጒሞች በሱሪስት ተተርጒመዋል። በኋላም የሮሐ ኤጲስ ቆጶስ የሆነው ራቡላ (5ኛው መቶ ክፍለ ዘመን) የመንበግ ኤጲስ ቆጶስ የሆነ ፊልክስዮስ (5ኛው መቶ ክፍለ ዘመን) እና ቶማስ ዘሄራክልያ (7ኛው መቶ ክፍለ ዘመን) ትርጒሙ እንዲቃና አደረጉ። በአርማንያም ቅዱስ ሚስሮኝና ቅዱስ ሳሃክ (3ኛው - 4ኛው መቶ ክፍለ ዘመን) ቅዱሳት መጻሕፍትን ወደ አርመን ቋንቋ ተረጐሙ።

ቅዱስ ሄሮኒሙስም (ጀሮም፥ 4ኛው መቶ ክፍለ ዘመን) ብዙ ጥንታውያን የቅዱሳት መጻሕፍትን ቅጂዎች በማስተያየት ቢብልያ ቩልጋታ የሚባለውን የሮማይስጥ (የላቲን) ትርጒም አዘጋጀ።

ከዚህ በላይ የተጠቀሱት ትርጒሞች ጥንታውያን እንደ መሆናቸው መጠን የዛሬ ሊቃውንት ጥረት፥ እነዚህን በማስተያየት የተጣራ የመጽሐፍ ቅዱስ ትርጒም ማዘጋጀት ነው።

በኋላም በኤውሮጳ ማርቲን ሉተር (1483-1546 እ.ኤ.አ.) መጽሐፍ ቅዱስን ወደ ጀርመንኛ ተረጐመው። ኤራስሙስ (1466-1536 እ.ኤ.አ.) አዲስ ኪዳንን ከጥንታውያን ጽሑፎች ጋር አስተያይቶና አቅንቶ ወደ ላቲን ተረጐመ። ዊክሊፍ (1329-1384 እ.ኤ.አ.) እና ቲንዴል (1494-1536 እ.ኤ.አ.) ወደ እንግሊዝኛ ተረጐሙ።

በኢትዮጵያ በአንድምታ ትርጓሜ የሚደክሙ ሊቃውንት ምን ጊዜም ቅዱሳት መጻሕፍትን ወደ አማርኛ ሳይተረጒሙ አልቀሩም። እነጴጥሮስ ሄይሊንግ በከፊል ነጠላ ትርጓሜ ቢያዘጋጁም መጽሐፍ ቅዱስን በሙሉ በነጠላ ትርጓሜ ወደ አማርኛ የተረጐመ አብርሃም (አባ ሮሚ) የሚባል መነኩሴ ነበረ። ይህም ትርጒም በመጽሐፍ ቅዱስ ማኅበር በኩል በ1816 ዓ.ም. አራቱ ወንጌላት፥ በ1821 ዓ.ም. አዲስ ኪዳን፥ በ1832 ዓ.ም. ሙሉው መጽሐፍ ቅዱስ ታትሞ ወጣ።

የዕብራይስጥንና የግሪክን ቋንቋ የሚያውቁ አንዳንድ የውጭ አገር ዜጎች (ለምሳሌ ማርቲን ፍላድ) ከሌሎች ኢትዮጵያውያን ጋር በመተባበር ትርጒሙን ካሻሻሉት በኋላ በ1878 ዓ.ም. እንደ ገና ታርሞ ታተመ፤ ከዚያም ወዲህ በየጊዜው ታትሞ ወጥቷል።

ከኢጣልያን ወረራ በኋላ የቀድሞው ትርጒም እንዲታረም ስለታሰበ ብዙ ሊቃውንት ከደከሙበት በኋላ በ1953 ዓ.ም. አዲሱ ትርጒም ታተመ። ዛሬ በብዛት በሰው እጅ የሚገኘው የአማርኛ መጽሐፍ ቅዱስ ይህ ነው። ከዚያም በኋላ የኢትዮጵያ መ.ቅ. ማኅበር ቀለል ባለ አማርኛ በ1980 ዓ.ም. አዲስ ትርጒም አሳተመ።

አለቃ ተወልደ መድኅን ገብሩ መጽሐፍ ቅዱስን ወደ ትግርኛ፥ የወለጋው ተወላጅ አኔሲሞስ ነሲብም ወደ ኦሮምኛ ተርጒመውታል። «መጽሐፍ ቅዱስ» ይመ.

**የቅዱሳት መጻሕፍት ዝርዝር**፤

የመጻሕፍት ዝርዝር በግሪክና በእንግሊዝኛ ካኖን

ተብሎ ይጠራል። በካኖን ውስጥ የተዘረዘሩት የብሉይና የአዲስ ኪዳን መጻሕፍት በሙሉ እግዚአብሔር ያስጻፋቸው ናቸው፥ የእግዚአብሔር መንፈስ አለባቸው፤ ዋና የክርስቲያን መመሪያ ናቸው፤ ሮም 15፥4፤ 2ጢሞ. 3፥16-17።

ክርስቶስ በምድር ሳለ አይሁድ የተቀበሉአቸው የዕብራይስጥ ቅዱሳት መጻሕፍት የሚከትሉት ናቸው :-

1. <u>ብሔረ ኦሪት</u፤ ዘፍጥረት፥ ዘጸአት፥ ዘሌዋውያን፥ ዘኁልቍ፥ ዘዳግም 5

2. <u>ነቢያት</u>፤ ሀ) የቀደሙ ነቢያት :- ኢያሱ፥ መሳፍንት፥ ሳሙኤል፥ ነገሥት 4

ለ) የኋለኞች ነቢያት :- ኢሳይያስ፥ ኤርምያስ፥ ሕዝቅኤል፥ ደቂቀ ነቢያት። 4

3. <u>ጽሑፎች</u>፤ ሐ) መዝሙረ ዳዊት፥ ኢዮብ፥ ምሳሌ፥ ዳንኤል፥ ዜና መዋዕል፥ ዕዝራና ነህምያ። 6

መ) ጥቅልሎች (በበዓላት የሚነበቡ) መኃልየ መኃልይ፥ ሩት፥ ሰቆቃው፥ መክብብ፥ አስቴር። 5

የአይሁድ ቅዱሳት መጻሕፍት ድምር 24

አይሁድ በእነዚህ ሦስት ክፍሎች መጻሕፍትን እንደተቀበሉ በሉቃስ 24፥44 እናስተውላለን። ዛሬ እንደ ደቂቀ ነቢያት (ከሆሴዕ እስከ ሚልክያስ ድረስ) ያሉትን አንድ በአንድ በመቍጠር 24 ጥንታውያን የዕብራይስጥ መጻሕፍት 39 ናቸው። ዛሬ ከኦርቶዶክስና ከካቶሊክ አብ.ክ. በቀር በሌሎቹ አብ.ክ. ዘንድ በሚገኘው መ.ቅ. የብ.ኪ. መጻሕፍት ቍጥር 39 ነው።

ከእስራኤል አገር ውጭ ተበታትነው ይኖሩ የነበሩ አይሁድ ከዕብራይስጥ ይልቅ የግሪክን ቋንቋ የሚያውቁ ስለነበሩ በእነርሱ መካከል በዕብራይስጥ ቋንቋ ያልነበሩ፥ በግሪክ የተጻፉ አንዳንድ መጻሕፍት ተቀባይነት አገኙ፤ እነርሱም ዕዝራ ካልእ፥ 3 የመቃብያን መጻሕፍት፥ ጦቢት፥ ዮዲት፥ ባሮክ፥ ሲራክ፥ ጥበብ ናቸው። እነዚህም የሰባ ሊቃናት ትርጉም በሚባለው የብ.ኪ. የግሪክ ትርጉም ውስጥ ተጠቃልለው ይገኛሉ፤ ዛሬ ግን አይሁድ ከብ.ኪ. መጻሕፍት ጋር አይቈጥሩአቸውም። ከክርስቲያኖች መካከል እነዚህን ከሌሎች ቅዱሳት መጻሕፍት ጋር አስተካክለው የሚቀበሉአቸውም አሉ፤ የማይቀበሏቸውም አሉ። የማይቀበሏቸው እነዚህ ከጥንት በዕብራይስጥ አልተጻፉም፤ በቅድስት አገርም ይኖሩ በነበሩ አይሁድ ዘንድ ተቀባይነት አላገኙምና ክርስቶስ አልመሰከረላቸውም ይላሉ። ከማይቀበሉት አንዳንዶች እነዚህን የግሪክ መጻሕፍት አዋልድ ብለው ዝቅተኛ ደረጃ ይሰጡአቸዋል። የሚቀበሉአቸው ግን እነዚህ መጻሕፍት በአይሁድ ዘንድ የታወቁ ነበሩ፤ በሠላሳ ዘጠኙም መጻሕፍት ውስጥ የማይገኙትን አንዳንድ ነገሮች ይተርካሉ ብለው ይቀበሉአቸዋል።

በሐዋርያት ዘመን ብዙ ሰዎች የክርስቶስን የሕይወት ታሪክ በየተራው ለማዘጋጀት ሞከሩ፤ ሉቃ. 1፥1-4። ብዙ ሰዎችም መልእክቶችን ጻፉ፤ 2ተሰ. 2፥1:2፤ 3፥17። የቤ.ክ. አባቶች መጻሕፍትን ሲሰበስቡ በሐዋርያት ወይም ከሐዋርያት ጋር በሠሩት ሰዎች ያልተጻፉትን ጽሑፎች አልተቀበሉም። በአዲስ ኪዳን ክርስቲያኖች በሙሉ የሚከተሉትን መጻሕፍት ይቀበሉአቸዋል :-

1. ወንጌላት፤ ማቴዎስ፥ ማርቆስ፥ ሉቃስ፥ ዮሐንስ 4

2. የሐዋርያት ሥራ 1

3. የጳውሎስ መልእክቶች 14

4. የጴጥሮስ፥ የዮሐንስ፥ የያዕቆብና የይሁዳ መልእክቶች 7

5. የዮሐንስ ራእይ 1

የሐዲስ ኪዳን ድምር 27

ሁሉ የሚቀበሉአቸው የብ.ኪ. መጻሕፍት ድምር 39

ጠቅላላ ድምር 66

የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤተ ክርስቲያን 81 መጻሕፍትን ትቀበላለች። በመጽሐፈ ፍትሐ ነገሥት በግእዝ የተዘረዘሩት የሚከተሉት ናቸው፤

ኦሪት፥ 5 መጻሕፍት፥ ኢያሱ፥ መሳፍንት፥ ሩት፥ ዮዲት፥ ነገሥት፥ ሕጹጻን 2 መጻሕፍት፥ የዕዝራ መጻሕፍት 2፥ አስቴር፥ ጦብያ፥ መቃብያን 2 መጻሕፍት፥ ኢዮብ፥ ዳዊት፥ የሰሎሞን መጻሕፍት 5 ምሳሌያት፥ ቀሐልት፥ መኃልየ መኃልይ፥ ጥበብ፥ ጥበበ ባኃር፥ ኢሳይያስ፥ ኤርምያስ፥ ሕዝቅኤል፥ ዳንኤል፥ ሆሴዕ፥ አሞጽ፥ ሚክያስ፥ ኢዩኤል፥ አብድዩ፥ ዮናስ፥ ዕንባቆም፥ ሶፎንያስ፥ ሐጌ፥ ዘካርያስ፥ ሚልክያስ፥ ከእነዚህም የወጡ ጥበበ ኢያሱ ወልደ ሲራክና መጽሐፈ ዮሴፍ ወልደ ኮርዮን። 4ቱ ወንጌላት (ማቴዎስ፥ ማርቆስ፥ ሉቃስ፥ ዮሐንስ)፥ መጽሐፈ አብርክሲስ (የሐዋርያት ሥራ፥ የሐዋርያት መልእክቶች 7፥ የጴጥሮስ 2፥ የዮሐንስ 3፥ የያዕቆብ 1፥ የይሁዳ 1፤ የጳውሎስ መልእክቶች 14፥ መጽሐፈ አቡቀለምሲስ (የዮሐንስ ራእይ)።

የእነዚህ ድምር 81 ስላልሆነ፥ በፍትሐ ነገሥት አንድምታ ትርጓሜ ላይ አንዳንድ መጻሕፍት ተጨምረው ይገኛሉ፥ አቈጣጠሩ እንደሚከተለው ነው :-

| ሀ) <u>ብሉይ ኪዳን</u> | <u>መጻሕፍት</u> |
|---|---|
| 1. ኦሪት፥ ኢያሱ፥ መሳፍንት፥ ሩት | 8 |
| 2. ዮዲት | 1 |
| 3. ሳሙኤል፥ ነገሥት 1 እና 2 ዜና መዋዕል | 4 |
| 4. ዕዝራ ካልዕ፥ ዕዝራ ሱቱኤል | 2 |
| 5. አስቴር፥ ጦቢት | 2 |
| 6. መቃብያን | 2 |
| 7. ኢዮብ፥ መዝሙረ ዳዊት | 2 |
| 8. የሰሎሞን መጻሕፍት (ምሳሌ፥ ተግሣጽ፥ ጥበብ፥ መክብብ፥ መኃልይ) | 5 |

| | |
|---|---|
| 9. ነቢያት (4 ዐበይት ነቢያት 12 ደቂቀ ነቢያት) | 16 |
| 10. ሲራክ፥ ዮሴፍ ወልደ ኮርዮን | 2 |
| 11. ኩፋሌና ሄኖክ | 2 |
| የብ.ኪ. መጻሕፍት ድምር | 46 |

| ለ) <u>አዲስ ኪዳን</u> | <u>መጻሕፍት</u> |
|---|---|
| 1. ከማቴዎስ አንሥቶ እስከ ዮሐንስ ራእይ | 27 |
| 2. ሲኖዶስ (ሥርዐተ ጽዮን፥ ትእዛዝ፥ ግጽው፥ አብጥሊስ) | 4 |
| 3. መጽሐፈ ኪዳን | 2 |
| 4. ቀሌምንጦስና ዲድስቅልያ | 2 |
| አዲስ ኪዳን | 35 |
| ብሉይ ኪዳን | 46 |
| ጠቅላላ ድምር | 81 |

የካቶሊክ ቤተ ክርስቲያን ከ66ቱ የመጽሐፍ ቅዱስ ክፍሎች ጋር የምትቀበላቸው ሰባት ሌሎች መጻሕፍት አሉ። እነርሱም ዲዮትሮ ካኖኒካል ተብለው ሲጠሩ፥ 66ቱ ደግሞ ፕሮቶ ካኖኒካል ይባላሉ። በጠቅላላ 73 መጻሕፍት ሲሆኑ፥ ሁሉም እኩል ተቀባይነት አላቸው። ሰባቱ መጻሕፍት 1989 ዓ.ም. በአማርኛ ታትመው ወጥተዋል። እነዚህ ሰባት መጻሕፍት የሚከተሉት ናቸው :-

1. መጽሐፈ ጦቢት
2. መጽሐፈ ዮዲት
3. መቃብያን - 1
4. መቃብያን - 2
5. መጽሐፈ ጥበብ
6. መጽሐፈ ሲራክ
7. መጽሐፈ ባርክ

በተለይ ሁለቱ የመቃብያን መጻሕፍት በኦርቶዶክስ መጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ከተጠቀሱት ሦስቱ የመቃብያን መጻሕፍት ጋር በስም እንጂ በይዘት አይገናኙም። «መቃብያን» ይመ.

**ቅዱስ፤** የቃሉ ትርጉም የተለየ ማለት ነው። ሰው ወይም ማንኛውም ነገር ለእግዚአብሔር አገልግሎት ሲለይ ቅዱስ ይባላል። ሰዎች (ዘጸ. 28፥41)፥ እንስሳት (ዘጸ. 13፥2)፥ ቦታዎች (ዘጸ. 3፥5)፥ ቀናት (ዘፍ. 2፥3)፥ ማናቸውም ነገር ቅዱስ ሊባል ይችላል፤ ኢያሱ 6፥19።

እግዚአብሔር ከአማልክትና ከክፋት ሁሉ የተለየ ስለሆነ ቅዱስ ይባላል፤ ዘጸ. 15፥11፤ ኢሳ. 40፥25። እግዚአብሔር ቅዱስ በመሆኑ፥ ለእግዚአብሔር የሆነ ሁሉ ቅዱስ መሆን አለበት፤ ዘሌ. 19፥2፤ ዘካ. 14፥20:21፤ 1ጴጥ. 1፥15። የእግዚአብሔር ስም ከስም ሁሉ በላይ በመሆኑ ቅዱስ (ኢሳ. 57፥15፤ ሕዝ. 36፥20፤ ሉቃ. 1፥50)፥ ምስጋናውም ቅዱስ ነው፤ ኢሳ. 6፥3፤ ራእ. 4፥8።

ሰው ወይም ሌላው ነገር ቅዱስ የሚሆነው የእግዚአብሔር ስለሚሆን ነው። በብ.ኪ. ይህ በተለይ በሥነ ሥርዓት ተፈጽሟል። በአ.ኪ. አማኝ በክርስቶስ ሲሆን ቅዱስ ይባላል (1ቆሮ. 1፥2:30)፥ በጠባዩ እየተቀደሰ ይሄዳል፤ ዮሐ. 17፥17። ሰው ከመንፈስ ቅዱስ ዳግመኛ ሲወለድ የቅድስና ሥራ ይጀመራል፥ በሕይወቱ ሁሉ በቅድስና ያድጋል፤ በክርስቶስ ዳግም ምጽአትም ቅድስናው ፍጹም ይሆናል፤ 1ቆሮ. 15፥51፤ 1ተሰ. 4፥7፤ 5፥23:24።

ቅድስና በአማኝ ሕይወት ውስጥ የሚያድገው በእግዚአብሔር ኃይል ነው። ለእግዚአብሔር አገልግሎት የተለየ ስለሆነ በፍጹም ልቡ፥ በፍጹም ኃይሉ፥ በፍጹም አሳቡ እግዚአብሔርን መውደድ አለበት። ፍቅሩም ትእዛዛቱን በመጠበቅ ይገለጣል፤ ሕዝ. 37፥28፤ ማር. 12፥33፤ ዮሐ. 14፥21፤ ፊል. 2፥12-13።

**ቅዱስ ቍርባን፤** ክርስቶስ አልፎ በተሰጠበት ቀን ማታ ከደቀ መዛሙርቱ ጋር የፋሲካን እራት ከበላ በኋላ የቅዱስ ቍርባንን ሥርዓት ደነገገ፤ ማቴ. 26፥26-28፤ ማር. 14፥22-24፤ ሉቃ. 22፥19:20፤ 1ቆሮ. 10፥16:17፤ 11፥23-30። ይህ ሥርዓት ደግሞ የክርስቶስ ሥጋና ደም (ሥጋ ወደሙ፤ ማቴ. 26፥26:28፤ 1ቆሮ. 11፥27)፥ የጌታ እራት (1ቆሮ. 11፥20)፥ እንጀራ መቍረስ (ሐ.ሥ. 2፥42፤ 20፥7) በሚሉ ሐረጎች ተገልጧል። ቅዱስ ቍርባን የአዲስ ኪዳን ምሥጢር ነው (ማቴ. 26፥28)፥ ክርስቶስ በክብር እስኪመለስ ድረስ ምእመናን ይህን ሥርዓት መፈጸም ይገባቸዋል፤ 1ቆሮ. 11፥26። ቅዱስ ቍርባን የአንድነት ምሥጢር ሥርዓት ነው። ምእመናንን ከክርስቶስ ጋር አንድ ያደርጋቸዋልና፥ ከሌላ አምልኮት ሁሉ መራቅ ይገባቸዋል። ቀጥሎም ከሌሎች ምእመናን ጋር አንድ ስለሚያደርጋቸው በፍቅር መኖር ያስፈልጋቸዋል። ስለዚህ ከመቍረባቸው በፊት ራሳቸውን እንዲመረምሩ ታዝዘዋል፤ 1ቆሮ. 10፥14-20፤ 11፥27-30። «የፍቅር ግብዣ» ይመ.



ሰዎች እራት ሲበሉ

ክርስቲያን የሆኑ ሁሉ በዚህ ሥርዓት የእግዚአብሔርን ጸጋ እንደሚቀበሉ ያምናሉ፥ ነገር ግን ስለ ትምህርቱና ስለ አቀባበሉ በየቤተ ክርስቲያኑ ልዩ ልዩ አስተሳሰብ አለ።

**ቅዳሴ፤** በሥርዓት የተዘጋጀ ከቤተ መቅደስ ሥራ ፍጻሜ በኋላ የሚደረግ ምረቃ ወይም ቡራኬ፤ ዕዝ. 6፥17፤ ነህ. 12፥27። ዛሬም በቤ.ክ. እየተዘጋጀ የሚቀርበው የአምልኮ ዜማ ቅዳሴ ይባላል።

**ቅድስተ ቅዱሳን፤** ከተቀደሱት የተቀደሰች ወይም ከተለዩት የተለየች ማለት ነው። አምስቱ ንዋያተ ቅድሳት የነበሩበት የእግዚአብሔር ማደሪያና የቤተ መቅደስ ውስጣዊ ሦስተኛው ክፍል ነው፤ ዘጸ. 26፥33-35፤ 30፥6፤ ዕብ. 9፥3።

**ቅድስት፤** የተቀደሰች ወይም የተለየች ማለት ነው። ገበታ፥ መቅረዝና የዕጣን መሠዊያ የነበሩበት የእግዚአብሔር ማደሪያና የቤተ መቅደስ ሁለተኛው ክፍል፤ ዘጸ. 26፥33-35፤ 30፥6፤ ዕብ. 9፥2።

**ቅድስና፤** ከክፉት ወደ መልካምነት የመለወጥ እድገት፤ ሮም 6፥22፤ 2ቆሮ. 7፥1፤ 1ጢሞ. 2፥15፤ ዕብ. 12፥10:14። «ቅዱስ»፥ «ለውጥ» ይመ.

**ቅጣት፤** በእስራኤል ሕግ ነፍስ የገደለ፥ ወላጆቹን የመታ ወይም የሰደበ፥ ሰውን አፍኖ የወሰደ፥ እግዚአብሔርን የሰደበ፥ ሰንበትን የሻረ፥ ባዕድ አምልኮትን የተከተለ፥ ያመነዘረ፥ ከተፈጥሮ ጋር የማይስማማ የጾታ ግንኙነትን ያደረገ የሞት ቅጣት ይፈረድበት ነበር፤ ዘጸ. 21፥12-17፤ 22፥18-20፤ ዘሌ. 24፥14-16፤ ዘኍ. 15፥32-36። ሰው ሰውን ቢጐዳ እንደ ጉዳቱ መጠን ካሣ መክፈል ነበረበት፤ ዘጸ. 21፥23-25:30። ሰው ሲያጠፋ ሊገረፍ ይችላል፥ የግርፋቱ ቍጥር ግን እንደ ኃጢአቱ መጠን፥ ደግሞም በአርባ የተወሰነ ነበር፤ ዘዳ. 25፥1-3። በእስራኤል ዘንድ የሞት ቅጣት በድንጋይ በመውገር፥ በእንጨት ላይ በመስቀል (ዘዳ. 21፥22:23፤ 22፥24)፥ በሮማውያን ዘንድ ራስን በመቍረጥ (ማቴ. 14፥10)፥ ወይም በስቅላት ይፈጸም ነበር፤ ማር. 15፥21-25። እግዚአብሔር ሰውን እንደ ሥራው ይቀጣል፤ ሉቃ. 12፥46-48፤ ራእ. 20፥11-15። በደለኛ ለዘለዓለም ይቀጣል፤ ዳን. 12፥2፤ ማቴ. 25፥46። እግዚአብሔር ልጆቹን ይቀጣል፥ ይህም ለጥቅማቸው ስለሆነ በትዕግሥት ሊቀበሉት ይገባል፤ ዕብ. 12፥5-11። «ኵነኔ» ይመ.

**ቅጥራን፤** የመሬት ዘይት (ነዳጅ) ተንጥሮ የሚገኝ ጥቁር ሙጫ። ውሃ እንዳያስገባ መርከብ በቅጥራን ይቀባ ነበር፤ ዘፍ. 6፥14፤ ዘጸ. 2፥3። ዝፍትም በመ.ቅ. እንደዚሁ ነው፤ ዘፍ. 14፥10፤ ኢሳ. 34፥9።

**ቅጥር፤** በመ.ቅ. ዘመን በከተማዎች ዙሪያ ትላልቅ የመከላከያ ቅጥሮች ይሠሩ ነበር፤ ከተማ ይመ.። የኢያሪኮ ቅጥር በጣም የታወቀ ነበር፤ ኢያሱ 6፥5። የእግዚአብሔር ሕዝብ በከተማ በመመሰላቸው ቅጥር የኃይል (ኤር. 15፥20)፥ የመጠበቅ (ዘካ. 2፥5)፥ የመዳንም ምሳሌ ነው፤ ኢሳ. 26፥1።



የከተማ ቅጥርና ግንብ

**ቅጽበተ ዐይን፤** የዐይን ጥቅሻ። ቃሉ አጭር ጊዜን (ኢሳ. 54፥8)፥ ፍጥነትንም ያመለክታል፤ 1ቆሮ. 15፥51:52።

**ቅፍርናሆም፤** የናሆም መንደር በገሊላ ባሕር ዳር በስተሰሜን ያለች ከተማ። ክርስቶስ እየተዘዋወረ ሲሰብክ መኖሪያው በቅፍርናሆም ነበር፤ ማቴ. 4፥13-16። የዘብዴዎስና የጴጥሮስ አገር (ማር. 1፥29-31)፥ ማቴዎስም ከቅፍርናሆም ተጠራ፤ ማቴ. 9፥9። በቅፍርናሆም በአንድ መቶ አለቃ የተሠራ ምኵራብ ነበር፤ ሉቃ. 7፥1-9። ከምኵራብ አለቆች አንዱ ኢያኢሮስ ነበረ፤ ማር. 5፥22። በቅፍርናሆም ክርስቶስ ብዙ አስደናቂ ተአምራትን አደረገ (ማቴ. 8፥5-13፤ ማር. 2፥1-12፤ ዮሐ. 4፥46-54)፥ ነገር ግን የቅፍርናሆም ሰዎች አላመኑምና ክርስቶስ በቅፍርናሆም ላይ የፍርድ ትንቢት ተናገረባት፤ ማቴ. 11፥23:24። ዛሬ ሰው አይኖርባትም። ካ. 5ለ።

**ቆላስይስ፤** ቆላስይስ ከኤፌሶን 150 ኪ.ሜ. የምትርቅ፥ በእስያ አውራጃ የምትገኝ አነስተኛ ከተማ ነበረች። በአቅራቢያዋ የሚገኙ ከተማዎች ሎዶቅያና ኢያራ (ሂራፖሊስ) ይበልጡአት ነበር። ጳውሎስ ራሱ ወደ ቆላስይስ አልሄደም ነበር፤ ምናልባት ወንጌልን የሰበከላቸው በኤፌሶን ከሐዋርያው እንደበት የወንጌልን ቃል የሰማው የቆላስይስ ሰው ኤጳፍራ ይሆናል። ፊልሞናና አርክጳ ደግሞ በእዚያ አካባቢ የታወቁ ሰዎች ነበሩ፤ ሐ.ሥ. 19፥10፤ ቆላ. 1፥7-8፤ 2፥1፤ 4፥12-13:17፤ ፊልሞና 1-2:23። ካ. 7ሰ።

**የቆላስይስ መልእክት፤** ቅዱስ ጳውሎስ ከኤጳፍራ ስለ ቆላስይስ ቤ.ክ. ልዩ ልዩ መልካም ዜና ቢሰማም (1፥3-8)፥ ስለ ሐሰት ትምህርት መስፋፋት በመረዳቱ ይህን መልእክት ጻፈ። ቲኪቆስም አናሲሞስን ወደ ፊልሞና ቤት ለመሸኘት ስለሚሄድ መልእክቱን ለመላክ ምቹ ጊዜ ሆነለት፤ 4፥7-10። መልእክቱ የተጻፈው ጳውሎስ በሮም ታስሮ ሳለ በ60 ዓ.ም. ገደማ እንደነበረ አብዛኞቹ ይገምታሉ፤ ሐ.ሥ. 28፥30-31፤ ቆላ. 4፥18።

ክርስቶስ የፍጥረት ሁሉ ምንጭና መጋቢ ሆኖ

ከፍጥረትና ከኃይላት ሁሉ በላይ ነው፥ ለእርሱም ሁሉ ተፈጠረ፤ እርሱ የእግዚአብሔር «እውነተኛ ምሳሌ» ሲሆን፥ «በእርሱ የመለኮት ሙላት ሁሉ በሰውነት ተገልጦ ይኖራል»፤ በመስቀሉ ደም ሰላምን አድርጓል፥ ተቃዋሚዎቹን ሁሉ ድል ነሥቷል፤ እርሱም የቤ.ክ. ራስ ነው በማለት ጳውሎስ ክርስቶስን ከፍ ከፍ ያደርገዋል፤ በተለይ 1፥13-20፤ 2፥9:14-15:19 ይመ.

ጳውሎስ በክርስቶስ ክብርና ታላቅነት ላይ ያተኰረው የሐሰተኞች ትምህርት መሠረተ ቢስ መሆኑን ለማሳየት ነው። ሐሰተኞች ያስተማሩት በዝርዝር ባይገለጥም፥ ከጳውሎስ አጻጻፍ የተነሣ ትምህርታቸው በከንቱ ፍልስፍና ላይ የተመሠረተ ሰው ሠራሽ ወግና ዓለማዊ ሥርዓት እንደነበረው (2፥8)፥ ከፍ ያለ ስፍራ ለግዝረት እንደሰጠ (2፥11፤ 3፥1)፥ የመላእክትን አምልኮ ከፍ እንዳደረገ (2፥18)፥ የሰውን ፍትወት ለመግታት ስለ ምግብ ስለ መጠጥ ... ወዘተ. ልዩ ልዩ ትእዛዛት እንደደነገገ (22-23) እና በሃይማኖት ሰዎች መካከል «የዐዋቂዎችን ወገን» እንደለየ (1፥28፤ 3፥11) እናስተውላለን።

አማኞች በዚህ ምኘነት ፈንታ ከክርስቶስ ጋር በሞቱና በትንሣኤው አንድ ሆነው ወደ አዲስ ሁኔታ በመግባታቸው (3፥1-3)፥ «አሮጌውን ሰው ከሥራው ጋር» ጥለዋልና «አዲሱን ሰው» ለብሰዋል፤ 3፥4-10። የሐሰተኞች ምሥጢራዊ ዕውቀት በክርስቲያን ኑሮ መሠረት ስፍራ የለውም። ለብዙዎች የእነዚህ ሐሰተኞች ትምህርት ግኖስቲካዊና አይሁዳዊ አመለካከት የተቀላቀለበት ይመስላቸዋል።

አከፋፈል ፦

1. መግቢያ፤ ሰላምታ፥ ምስጋናና ጸሎት፤ 1፥1-12።

2. ክርስቶስ የሁሉ ጌታ ነው፤ 1፥13-2፥7።

3. ዓለማዊ ፍልስፍናና ሥርዓት ሁሉ አያድንም፤ 2፥8-23።

4. ክርስቲያናዊ ኑሮ፥ ሀ) በአዲስ አመለካከት (3፥1-11)፥ ለ) በቤ.ክ. (3፥12-17)፥ ሐ) በቤተሰብ (3፥18-4፥1)፥ መ) በአጠቃላይ ሁኔታ (4፥2-6) መታየት ይገባዋል።

5. መደምደሚያ፤ ስለ ታማኝ ሰዎች ምስጋና፥ ሰላምታዎች፥ ልዩ ልዩ መልእክት፥ የጳውሎስ ሰላምታ፤ 4፥7-18።

**ቆመ**፤ ባለበት ስፍራ ወይም ሁኔታ ጸና። አማኝ ባለበት ሲቆም የእግዚአብሔርን የማዳን ሥራ ያያል፤ ዘጸ. 14፥13፤ 1ቆሮ. 16፥13፤ ገላ. 5፥1፤ ኤፌ. 6፥13-15፤ ፊል. 4፥1፤ 2ተሰ. 2፥15።

**ቆሬ**፤ እንደ ወጭትና ገበቴ ያለ የቤት ዕቃ፤ መሳ. 6፥38።

**ቆሬ**፤ የይስዓር ልጅ። «ዳታን» ይመ.

**የቆሬ ልጆች**፤ በመዝሙረ ዳዊት አርእስት የተጠቀሱት ያሚናዳብ ልጅ የቆሬ ዘር ናቸው፤ 1ዜ.መ. 6፥22፤ መዝ. 42 ሌሎችም።

**ቆርቆሮ**፤ ብረትነት ካለው ማዕድን የሚሠራ ልዩ ልዩ ዓይነት ዕቃ፤ ዘኁ. 31፥22። ዝገት ያጠቃዋል፤ ስለዚህም የኃጢአትና የኃጢአተኛ ምሳሌ ሆኖ ተጠቅሷል፤ ኢሳ. 1፥25፤ ሕዝ. 22፥18።

**ቆሮስ**፤ ትልቅ መስፈሪያ፤ ዘሌ. 27፥16። «መስፈሪያ» ይመ.

**ቆሮንቶስ**፤ ቆሮንቶስ የግሪክ ከተማ ናት፤ ከአቴናም 75 ኪ.ሜ. ያህል ትርቃለች። በኢ.ኪ. ዘመን ስድስት መቶ ሺህ ሰዎች የሚኖሩባት ትልቅ ከተማ ነበረች። አቀማመጥዋ በሁለቱ የግሪክ አውራጃዎች በመቄዶንያና በአካይያ መካከል በሚገኘው ልሳነ ምድር ላይ ነበረ። ከተማይቱ የተመሠረተችው በባሕር መገናኛ ላይ በመሆኑ ከምሥራቅና ከምዕራብ ለሚመጡ መርከቦች ምቹ ወደብ ነበረች። ከዚህም የተነሣ ንግድ እየደራባት ሄደ፤ ከተማይቱም እጅግ ሀብታም ሆነች። የከተማይቱ ነዋሪዎች አፍሮዲቴ የምትባለዋን የፍቅር አምላክ ያመልኩ ነበር። «ቆሮንቶሳዊ!» መባል የስድብ ስም እስኪሆን ድረስ የዝሙት ኃጢአት በከተማይቱ በዛ። አብዛኞቹ ነዋሪዎች ግሪኮች ሲሆኑ፥ አይሁድና ብዙ ሮማውያን ነበሩ። ካ. 6ሸ።

**የቆሮንቶስ ቤተ ክርስቲያን**፤ ይህች ቤ.ክ. የተመሠረተችው ሐዋርያው ጳውሎስ ወንጌልን ሊሰብክ ሁለተኛ ጊዜ ወጥቶ ሳለ ወደ ግሪክ አገር ሲደርስ ነው፤ ሐ.ሥ. 15፥36፤ 16፥6-13። ሐዋርያው ከአቴና ወደ ቆሮንቶስ አልፎ ከአንድ ዓመት ተኩል በላይ እያስተማረ እዚያ ተቀመጠ፤ በዚህም ጊዜ አቂላና ጵርስቅላ ከእርሱ ጋር ተባብረው ይሠሩ ነበር፤ ሐ.ሥ. 18፥1-18። ቤተ ክርስቲያኒቱ ስታሳዝነውና ስታስቸግረው፥ ሐዋርያው ጳውሎስ ሁለት ጊዜ ሄዶ ምእመናንን የጠየቃቸው ይመስላል፤ 2ቆሮ. 13፥1።

**የቆሮንቶስ መልእክቶች፥ 1ኛው**፤ ቅዱስ ጳውሎስ በቆሮንቶስ ቤ.ክ.ን ካቋቋመ በኋላ አራት ዓመት ቆይቶ በ55 ዓ.ም ገደማ ከኤፌሶን ይህን መልእክት ጻፈ። ስለ ቆሮንቶስ ቤ.ክ. መጥፎ ወሬ ከልዩ ልዩ ሰዎች በመስማቱና ከቤ.ክ. ብዙ ጥያቄዎች በደብዳቤ በመቀበሉ እርምጃ መውሰድ ግዴታ ሆነበት፤ 1፥11፤ 7፥1፤ 16፥17። ችግሮች የተነሡት ከትምህርት ጉድለት ሳይሆን በከተማይቱ ከሚገኘው ፍልስፍናና አኗኗር ጋር የተያያዙ ነበሩ፤ 1፥22፤ 6፥9-11። በመልእክቱ 1ኛው ዋና ክፍል በመካከላቸው ስለነበረው መለያየት፥ ዝሙትና ሙግት መውቀስ ሲሆን፥ በ2ኛው ክፍል ደግሞ ስለ ጋብቻ፥ ለጣዖት ስለተሠዋ ሥጋ፥ በጌታ እራት በሚገባ ስለ መሳተፍ፥ ስለ መንፈስ ቅዱስ ስጦታዎች አጠቃቀምና ስለ ትንሣኤ ለቀረቡት ጥያቄዎች መልሶችን ይሰጣል። በማናቸውም ዘመን ስለእነዚህ ነገሮች ጥያቄዎች ሊነሡ ይችላሉ። ጉዳትን ሊያስከትሉ የሚችሉ ግን ቤ.ክ. መሠረታዊ ትምህርትዋን ከመስጠት ቸል ስትል ነውና ሐዋርያው ይህን በዚህ መልእክት «ዋልፍ» ቃላት በ15፥3-4 ያሳስባቸዋል።

አከፋፈል ፦

1. መግቢያ፤ ሰላምታና ምስጋና፤ 1፥1-9።

2. ቤ.ክ. የነበራት ክፉ አካሄድ፤ 1፥10-6፥20።

ሀ) መለያየት፤ 1፥10-4፥21። ይህም ስለ ጥበብ የግሪክ ፍልስፍና ተነሥቶ ነበር። ዓለማዊ ፍልስፍና ከመስቀሉ ትምህርት ጋር ምንም እንደማይገናኝ ካሳየ በኋላ (1፥17-2፥16)፥ የእግዚአብሔርን አገልጋዮች ሥራ ይገልጣል (3፥1-4፡5)፤ ከቆሮንቶስ ቤ.ክ. ጋር ያለውንም የራሱን አካሄድ ያብራራል፤ 4፥6-21።

ለ) ዝሙት፤ 5፥1-13፤ 6፥12-20። የእንጀራ እናቱን ሚስት ያደረገው ሰው ከቤ.ክ. መወገድ አለበት፥ ምክንያቱም «ጥቂት እርሾ ሊጡን ሁሉ ያቦካል»፤ 5፥1-8። ጳውሎስ ስለ ዝሙት አስቀድሞ የጻፈውን ደብዳቤ ያብራራል (5፥9-13)፥ ደግሞም ስለ ምግብ በልዩ ልዩ ባህልና በዝሙት መካከል ያለውን ልዩነት ማሳየት እንደሚያስፈልግ አጽንአት ይሰጣል፤ 6፥12-20።

ሐ) ሙግት፤ 6፥1-11። በምእመናን መካከል አለመግባባት ሲፈጠር፥ ቤ.ክ. እንጂ ዓለማዊ ዳኛ መፍረድ እንደማይገባው ያሳያል።

3. ለቤ.ክ. ጥያቄዎች መልሶች፤ 7፥1-15፥58።

ሀ) ስለ ጋብቻ፤ ም.7። ጋብቻን በአስቸጋሪ ዘመን እንዴት አክብሮ መያዝ እንደሚቻል ያስተምራል።

ለ) ለጣዖታት ስለተሠዋ ሥጋ፤ 8፥1-11፥1። «ዕውቀት» ያለው ክርስቲያን ለጣዖት የተሠዋን ሥጋ ቢበላ ራሱን ባይጐዳም፥ የደካማ ሰውን ሕሊና ማቍሰል ይችላልና አለመብላት ይሻለዋል፤ ም.8። ሐዋርያው ነፃነት እያለው በአማኞች ዘንድ መብቱን አልጠበቀም፤ ሌሎችን እያስተማረ ሕይወቱን እንደ እስፖርተኛ ይመራ ነበር፤ ም. 9። አማኝ ለጣዖት የተሠዋ ሥጋ በሚበላበት በአሕዛብ ግብዣዎች መሳተፍ የለበትም፥ ሌላ ምክንያት ይቅርና ሰው ከጌታ ማእድና ከአጋንንት ማእድ መካፈል አይችልም፤ ም. 10።

ሐ) አምልኮትን በሚገባ ስለመፈጸም፤ 11፥2-34። ሀ) ሴቶችም ወንዶችም ነፃነት ቢኖራቸውም የዘመኑን ባህል ተረድተው ክብራቸውን በአምልኮት ጊዜ መጠበቅ ይገባቸዋል፤ ቍ. 2-16። ለ) አማኙ ቅዱስ ቍርባንን ሲቀበል፥ ቅዱስ ምሥጢር ነውና የሚያደርገውን አስተውሎ መቅረብ አለበት፤ ቍ. 17-34።

መ) ስለ መንፈስ ቅዱስ ስጦታዎች፤ ም. 12-14። ቤ.ክ. በመንፈሳዊ ስጦታዎች ስትጠቀም አንድነትን ማጠንከር (ም. 12)፥ ፍቅርን መግለጥ (ም. 13) እና ሥርዓትን በአግባቡ ማስከበር አለባት፤ ም. 14።

ሠ) ስለ ሙታን ትንሣኤ፤ ም. 15። የክርስቶስ ትንሣኤ እውነት ነው (ቍ. 1-11) እና ያለ እርሱ ሃይማኖታችን ከንቱ ሲሆን (12-19)፥ ክርስቶስ ለራሱ ሁሉን ማስገዛቱንና የአማኙን ትንሣኤ ያረጋግጣል፤ 20-34። የአማኙም የትንሣኤ አካል የሚሞተው አካል ሲሆን፥ ከፍ ያለ ኃይልና ክብር ይኖረዋል (35-50)፤ በክርስቶስ ዳግም ምጽአት ይገለጣል፤ 51-58።

4. መደምደሚያ፤ ም. 16። ጳውሎስ ለኢየሩሳሌም ምእመናን ስለ ገንዘብ መዋጮ፥ ስለ ራሱና ስለ ሌሎች አገልግሎት ልዩ ልዩ ዕቅዶችን ከገለጠ በኋላ የመጨረሻውን ምክርና ቡራኬ ሰጠ።

## የቆሮንቶስ መልእክቶች፥ 2ኛው፤

ሐዋርያው ጳውሎስ ለቆሮንቶስ ከተማ ምእመናን መጀመሪያይቱን መልእክት ጽፎ ነበር፤ ሆኖም በቆሮንቶስ ቤ.ክ. አስነዋሪ ሥራ እየቀጠለ ሄደ። ሐዋርያው «እኔ ብሄድ ይሻላል» በማለት ወደ ቆሮንቶስ ሄደ፤ የቤ.ክ. ሰዎች ግን አልተቀበሉትም፤ በመካከላቸውም አንድ ሰው ተነሥቶ አሳዘነው፤ 2፥5-11፤ 12፥21። ጳውሎስም ወዲያውኑ ወደ ኤፌሶን ተመልሶ ከባድ መልእክት ጻፈና በቲቶ እጅ ላከው፤ 2፥1-6፤ 7፥8። መልእክቱን ካስተላለፈ በኋላ ግን ተጸጸተ። «እንደምን ይቀበሉት ይሆን?» በማለት ተጨነቀ፤ ጭንቀቱም ስለበዛበት «ቲቶ ሲመለስ እግረ መንገዴን አገኘዋለሁ» በማለት በጢሮአዳ በኩል ወደ መቄዶንያ ሄደ፤ 2፥12፡13። እንዳሰበውም ጳውሎስና ቲቶ ተገናኙ። ቲቶ ደስ የሚያሰኝ ወሬ ይዞ ነበር። የቆሮንቶስ ሰዎች የሐዋርያውን መልእክት በማየት ደነገጡ፤ በታላቅ ኀዘንም አዘኑ፤ ተጸጸቱም። ምክሩንም ለመቀበል ዝግጁ ሆኑ፤ 7፥5-16። የቲቶን ወሬ ሲሰማ ጳውሎስ እዚያው በመቄዶንያ እያለ ይህችን «ሁለተኛይቱ» የቆሮንቶስ መልእክት የተባለችውን ጻፈላቸው። ጊዜው 56 ዓ.ም. ነው።

እንደ እውነቱ ግን ጳውሎስ የጻፈላቸው ይህች መልእክት ሁለተኛይቱ ሳትሆን አራተኛይቱ ናት። ጳውሎስ በ1ቆሮ. 5፥9 ላይ የሚጠቅሳት መጀመሪያይቱ ትሆናለች፤ ቀጥሎም እኛ «መጀመሪያይቱ» የምንላትን ጽፏል፤ እርሷም 2ኛ ናት። ያች ከባድ መልእክት የያዘችው 3ኛ ናት፤ አሁንም ይህች እኛ «ሁለተኛይቱ» የምንላት 4ኛ ናት። መጀመሪያ የተጻፈችውና በተጨማሪም ከባድ መልእክት የያዘችው ያች መልእክት ጠፍተዋል፤ አንዳንዶች መምህራን ግን በ2ቆሮ. ም. 10-13 የምናገኘው ከባድ ተግሣጽ የ3ኛይቱ መልእክት ክፍል ነው ይላሉ፤ ይህም ሊሆን ይችላል።

በቆሮንቶስ ቤ.ክ. ስለ አገልግሎትና ስለ ሐዋርያዊ ሥልጣኑ ብዙ ጥያቄ ስለተነሣበት፥ ጳውሎስ ከብዙ መንፈሳዊ ምክር ጋር ዓላማውን፥ ያደረገውንና የሚያደርገውን አብራራ።

አከፋፈል ፦

1. መግቢያ፤ የጳውሎስ ሰላምታና ከመከራ ጋር ያገኘው የእግዚአብሔር መጽናናት፤ 1፥1-11።

2. የጳውሎስ አገልግሎት፤ 1፥12-7፥16።

ሀ) ዕቅዶቹ የተለወጡበት ምክንያት፤ 1፥12-2፥17።

ለ) አገልግሎቱ የአዲስ ኪዳን መሆኑ (ም.3)፥ ከባድ ኀላፊነት እንዳለበት (4፥1-5)፥ በክርስቶስ

ፍርድ ወንበር ፊት እንደሚመዘን (4፥6-5፥10)፥ ዕርቅን እንደሚያውጅ (5፥11-6፥2)፥ ብዙ መከራ እንደሚያስከትል (6፥3-13)፥ ሰዎችን ወደ ቅድስና እንደሚጠራ፤ 6፥14-7፥1።

ሐ) ከቲቶ በተቀበለው ዜና መደሰቱ፤ 7፥2-16።

3. ለኢየሩሳሌም ምእመናን ስለሚዘጋጀው አስተዋጽኦ፤ ም. 8-9።

4. የጳውሎስ እውነተኛ ሐዋርያነት፤ ም. 10-12።

ጳውሎስ መጀመሪያ በቆሮንቶስ ወንጌልን በመስበኩ (ም. 10)፥ ከሌሎች ይልቅ መከራን በወንጌል ምክንያት በመቀበሉ (ም. 11) እና ከፍ ያለ መገለጥ ለእርሱ በመሰጠቱ (12፥1-13) ሐዋርያነቱን አረጋገጠ።

5. መደምደሚያ፤ የመጨረሻ ማስጠንቀቂያዎችና ሰላምታ፤ 12፥14-13፥14።

**ቆብ**፤ በአሪት ዘመን የአሮን ልጆች በአገልግሎት ላይ ሳሉ ከጨርቅ ተሰፍቶ በራሳቸው ላይ የሚደፉት፤ ዘጸ. 28፥40።



**ቆንዳላ**፤ የራስ ጠጕር ጕንጕን። የሶምሶን ቆንዳላ ሰባት ጕንጕን ነበር፤ መሳ. 16፥13:14። ያልተጕነጐነ ጎፈሬም ቆንዳላ ይባላል፤ መ.መ. 5፥2:11።

**ቆዕ**፤ ጮርቃ፤ ያልበሰለ ለጋ ፍሬ፤ መ.መ. 4፥13።

**ቆጵሮስ**፤ በሜዲቴራኒያን ባሕር በስተምሥራቅ የሚገኝ ደሴት። ብዙ አይሁድ ይኖሩበት ነበር። በርናባስ ቆጵሮሳዊ ነበር፤ ሐ.ሥ. 4፥36። የቆጵሮስ ሰዎች ወደ አንጾኪያ ሲሄዱ ወንጌልን ለግሪክ ሰዎች ሰበኩ፤ ሐ.ሥ. 11፥19:20። ጳውሎስ፥ በርናባስና ማርቆስ ደሴቱን ጐብኝተው ወንጌል ሰበኩ፤ ሐ.ሥ. 13፥4-13። በኋላም በርናባስና ማርቆስ እንደገና ወደ ቆጵሮስ ሄዱ፤ ሐ.ሥ. 15፥39። ካ. 6ኛ።

**ቈላፍ**፤ 1. አስተካክሎ መናገር የማይችል ኰልታፋ። ሙሴ ከንፈረ ቈላፍ ነበር፤ ዘጸ. 6፥12:30። 2. ያልተገረዘ ወሸላ፤ ዘፍ. 17፥14።

**ቈረቈር**፤ በራስ ቆዳ ላይ የሚወጣ በሽታ። ጠጕርን ያነጣል፤ በመዳምም ያደርጋል። በብ.ኪ. ይህ ዓይነት በሽታ የያዘው ሰው እንደ ርኩስ ይቈጠር ነበር። የኃጢአት ምሳሌ ነው፤ ዘሌ. 13፥30-37።

**ቈርቈሮ**፤ «ቆርቆሮ» ይመ.

**ቈንጆ፥ ቈንጃጅት**፤ ለጋብቻ የበቃች ድንግል ሴት፤ ዘፍ. 24፥43፤ መዝ. 68፥25። ውበትንም ይገልጣል፤ በመኃልየ መኃልይ ብዙ ጊዜ ተጠቅሶ ይገኛል።

**ቋቁቻ**፤ ቃሉ በሥጋ ቆዳ ላይ ማናቸውንም የቀለም ለውጥ ያመለክታል፤ ዘዳ. 28፥27። «በሽታ» ይመ.

**ቋንቋ**፤ አንዱ ከሌላው ጋር የሚግባባበት ቃል ወይም ንግግር። ሰዎች በባቢሎን ግንብን ለመሥራት እስኪነሡ ድረስ ቋንቋቸው አንድ ነበረ። እግዚአብሔር ሲቀጣቸው ግን ቋንቋቸውን ደባለቀባቸው፤ ዘፍ. 11፥1-9። ብዙ ጊዜ ቋንቋ ከአገር ባህል ጋር ይያያዝና የሕዝብ መለያ ይሆናል፤ መሳ. 12፥5-6፤ ሕዝ. 3፥5-6፤ ራእ. 7፥9። ብሉይ ኪዳን የተጻፈበትና እስከ ባቢሎን ምርኮ ድረስ የእስራኤል ሕዝብ የተጠቀመበት ቋንቋ ዕብራይስጥ ነበረ። ከምርኮ በኋላ አይሁድ የተጠቀሙበት ቋንቋ ግን አረማይክ ነው። ይሁን እንጂ አዲስ ኪዳን የተጻፈው በዘመኑ በሠለጠነው ዓለም ቋንቋ በግሪክ ነበረ።

**ቋንጃ**፤ ከጭንና ከባት መካከል ከጕልበት በታች የሚገኝ የእግር ማጠፊያ። ፈረሶች ሠረገላን ለመሳብ እንዳይችሉ ቋንጃቸው ይቈረጥ ነበር፤ ኢያሱ 11፥6:9፤ 2ሳሙ. 8፥4።

**ቋጥኝ**፤ አለቁ አለቁ ቁጭ ያለ ከገደል ተሸርፎ የወደቀ ድንጋይ፤ ኤር. 4፥29።

**የቍልምጫ ስም**፤ የፍቅር ወይም የወዳጅነት ስም። አንድ ሰው ወዳጁን ሌሎች በማይጠሩት ስም ቢጠራው፥ ያ ስም የቍልምጫ ስም ነው ለማለት ይቻላል። የይስሐቅ ልጅ ስሙ ያዕቆብ ነበር። እግዚአብሔር ግን እስራኤል ብሎ የቍልምጫ ስም አወጣለት፤ ኢሳ. 45፥4።

**ቍልፈት**፤ ያልተገረዘ አባል ሸለፈት። አብርሃምና ወንድ የሆነ ቤተሰቡ ሁሉ ቍልፈታቸውን እንዲገረዙ ታዘዙ፤ ዘፍ. 17፥11:14:23:24። «ሸለፈት» ይመ.

**ቍርባን**፤ የቀረበ ወይም የተሰጠ ማለት ነው። ይኸውም ለእግዚአብሔር የሚቀርብ መባ ወይም መሥዋዕት ነው፤ ዘሌ. 1፥2:9፤ 2፥1 ... ወዘተ። ማርቆስ ቍርባን የሚለውን ቃል «መባ» ብሎ ተርጕሞታል፤ ማር. 7፥11። በመ.ቅ. ክርስቶስ የደነገገው ሥርዓት ቍርባን ተብሎ ሲጠራ አናይም። በቤ.ክ. አጠራር መሠረት ግን «ሥጋ ወደሙ» ካህናት ለምእመናን የሚያድሉት ስለሆነ ቍርባን ተብሏል። «ቅዱስ ቍርባን» ይመ.

**ቍርዬ**፤ ቅልጥመ ረጃጅም፥ «ቍር» የሚል ድምፅ ያለው አሞራ፤ ከብርድ ዘመን (ከክረምት) በኋላ ከደቡብ ተመልሶ ወደ እስራኤል የሚሄድ፥ ምግቡም እህልና ነፍሳት የሆነ። ሊቃውንት እንደሚሉት በመ.መ. 2፥11-12 ቍርዬ የተባለው ዋኖስ ነው። ጳሩ ግን በኢሳ. 38፥14 ሽመላ የተባለው ቍርዬ ነው። «ወፎች» ይመ.

**ቍስል**፤ ቃሉ የሥጋ ቆዳን የሚያበላሸውን የበሽታ ዓይነት ሁሉ ይገልጣል፤ ኢሳ. 1፥6፤ ራእ. 16፥2። «በሽታ» ይመ.

**ቍጣ፤** በሚገባ ወይም በማይገባ በሰው ላይ መፍረድ፥ መናገር፥ መቅጣት፥ መግሠጽ።

1. የእግዚአብሔር ቍጣ፤ እግዚአብሔር ቅዱስና ጻድቅ ስለሆነ በኃጢአት ምክንያት ይቈጣል፤ ዘጸ. 29፥23-28፤ ዕብ. 12፥29፤ ራእ. 16፥5-7፤ 19፥1-2። ቍጣው እንደ ሰው ቍጣ ቶሎ የሚነሣና የሚበርድ አይደለም፤ ቍጣውም በፍርዱ ይታያል፤ ዘጸ. 9፥5-8፤ ዘካ. 8፥14፤ ዮሐ. 3፥36፤ ሮም 1፥18፤ 2፥5፤ ኤፌ. 5፥6። ምእመናን ከእግዚአብሔር ቍጣ በክርስቶስ ይድናሉ፤ ሮም 5፥9፤ 1ተሰ. 1፥9:10።

2. የጻድቅ ሰው ቍጣ፤ ጻድቅ ሰው በዐመፅ ሥራ ላይ ሊቈጣ ይገባዋል፤ ክርስቶስ በዚህ ዓይነት ተቈጣ፤ ነገር ግን ጻድቁ ቍጣውን በኃጢአት መንገድ እንዳይገልጥ ተከልክሏል፤ 1ሳሙ. 20፥30-34፤ ማር. 3፥5፤ ኤፌ. 4፥26-27።

3. የኃጢአተኛ ቍጣ፤ ሰው መጥፎ ነገርን ሲያይ ሊቈጣ ይችላል፤ 1ሳሙ. 20፥30-34። አብዛኛውን ጊዜ የሰው ቍጣ ከፍርሃትና ከኵራት ከስንፍናም ይነሣል፤ ይህ የሥጋ ሥራ ነውና አሳዛኝ ውጤትን ያመጣል፤ ዘፍ. 27፥41-45፤ 30፥1:2፤ 49፥6፥7፤ ምሳ. 27፥4፤ ገላ. 5፥20። ልዝብ መልስ ወይም ስጦታ የሰውን ቍጣ ሊያበርድ ይችላል፤ ምሳ. 15፥1፤ 21፥14። አማኞች ቍጣን ማስወገድ ይኖርባቸዋል፤ ኤፌ. 4፥31፤ ቆላ. 3፥8፤ ያዕ. 1፥19። በቍጣ ፈንታ ፍቅርና ትዕግሥት፥ ይቅር መባባልም ያስፈልጋል፤ ኤፌ. 4፥32፤ ቆላ. 3፥12:13።

**ቍጥር፤** በዕብራይስጥ ብዛት ሲገለጥ ቍጥሩ በፊደል እንጂ በአኃዝ ብዙ ጊዜ አልተጻፈም። ቍጥሮች ሲገለበጡ ልዩ ልዩ ስሕተት የገባ ይመስላል፤ ለምሳሌ ልዩ ልዩ የሥነ ጽሑፍ ቅርሶች ከጥፋት ውሃ በፊት በነበሩት በአባቶች ዕድሜ አይስማሙም። ደግሞም ስለ አይሁድ አቈጣጠር እናውቅምና ሊቃውንት ዕድሜያቸውን ለመቍጠር በተለያዩ መንገዶች ይጀምራሉ። በዕብራይስጥም «ሺህ» እና «አለቃ» ተብለው የሚተረጐሙት ቃላት በጣም ስለሚመሳሰሉ፥ የሕዝብ ብዛትና የተገደሉ ወታደሮች ቍጥር ሲወርድ ሲዋረድ ስሕተት ገብቶበታል የሚሉ ሊቃውንት ጥቂቶች አይደሉም።

በመ.ቅ. ስለ ቍጥር አጠቃቀም ሌላ ነገር አለ፤ ይኸውም ቍጥሮች አንዳንድ ጊዜ የነገር፥ የሰውን ወይም የዘመንን ሁኔታ እንጂ ብዛትን አያመለክቱም። ይህም በተለይ በዮሐንስ ራዕይ ይታያል። ሆኖም ስለ ቍጥር አተረጓጐም የሊቃውንት አሳብ ብዙና የተለያየ ነው። ከዚህም ቀጥሎ ከሊቃውንት አሳቦች አንዳንዶችን እናቀርባለን።

1. የአንድነትና የብቸኝነት ቍጥር፤ በተለይም ስለ እግዚአብሔር፤ ዘዳ. 6፥4።

2. ከአንድ በላይ ለሆነ ነገር ሁሉ መግለጫ ቍጥር፤ መክ. 4፥8-11፤ ማቴ. 18፥19-20።

3. ፍጹም ቍጥር (ሉቃ. 13፥32)፥ በተለይም ስለ ሥላሴ ስምና አካል፤ ማቴ. 28፥19።

4. አራት ማዕዘን ለሆነ ለጠቅላላው ቍጥር፥ በተለይ ስለ ዓለም፤ ራእ. 7፥1።

6. የሥራና የሰው ቍጥር፥ ዘጸ. 20፥9፤ ራእ. 13፥18።

7. ሱባዔ፤ በእስራኤል ዘንድ በሥራም በቃልም የሚገለጥ ፍጹም ቍጥር፤ መዝ. 119፥164፤ ሩት 4፥15። እግዚአብሔር በሰባተኛው ቀን ከመፍጠር ሥራ ዐረፈ፤ ይህም ለዕረፍት ቀን፥ መሬት ለማይታረስበት ለሰባተኛው ዓመት፥ ለኢዮቤልዩ፥ ለበዓለ ኀምሳ፥ ለትንቢት ዓመታት ለሌላም መሠረት ይሆናል፤ ዘጸ. 20፥10፤ 34፥22፤ ዘሌ. 25፥2-10።

10. የሙላት ቍጥር። ከጥፋት ውሃ በፊት ዐሥር ሰዎች (ዘፍ. 5)፥ በግብጻውያን ላይ ዐሥር መቅሠፍት፥ ዐሠርቱ ትእዛዛት፥ ከእግዚአብሔር መንግሥት የሚከለክሉ ዐሥር ኃጢአቶች (1 ቆሮ. 6፥9:10)፥ ከእግዚአብሔር ሊያርቁን የማይችሉ ዐሥር ኃይላት (ሮም 8፥38:39)፥ በዮሐንስ ራእይ የተጠቀሰው አውሬ ዐሥር ቀንዶችና ዐሥር ዘውዶች (ራእ. 13፥1) ... ወዘተ።

12. የእግዚአብሔር ምርጥ ሕዝብ ቍጥር። ዐሥራ ሁለት የእስራኤል ነገዶች፥ ዐሥራ ሁለት ሐዋርያት፥ ዐሥራ ሁለት የአዲሲቱ ኢየሩሳሌም ደጆች (ራእ. 21፥12-14)... ወዘተ።

40. ወደ አዲስ ሁኔታ የመግቢያ ምልክት ቍጥር። የጥፋት ውሃ አርባ ቀን ዘነበ፤ ሙሴ በደብረ ሲና አርባ ቀን ቆየ፤ እስራኤል በምድረ በዳ አርባ ዓመት ኖሩ፤ ክርስቶስ አርባ ቀን ጦመ፤ ክርስቶስ ከትንሣኤው በኋላ አርባ ቀን በምድር ላይ ቆየ ... ወዘተ።

70. የእግዚአብሔር አስተዳደር ቍጥር፥ ሰባ የኖኅ ዘር (ዘፍ. 10)፥ ወደ ግብጽ የወረዱ ሰባ ሰዎች (ዘፍ. 46፥27)፥ ሙሴን የረዱ ሰባ ሽማግሌዎች (ዘኍ. 11፥16)፥ የሰው ዕድሜ ሰባ (መዝ. 90፥10)፥ ኢየሱስ የላካቸው ሰባ ደቀ መዛሙርት (ሉቃ. 10፥1)፥ ይቅርታ የሚደረግባቸው ጊዜያት ሰባት ጊዜ ሰባ (ማቴ. 18፥22) ... ወዘተ።

666. ስለዚህ ቍጥር ብዙ ትርጕም ቢኖርም፥ በተጠቀሰበት አንቀጽ አሳብ መሠረት የመንግሥት ሥልጣንና የንግድ ሁኔታ የተጣመሩ መሆናቸው ይታያል፤ 1ነገ. 10፥14፤ ራእ. 13፥11-18። «በየዕለቱ ከእግዚአብሔር ጋር» 4ኛ ዓመት ገጽ 205 ይመ.

1000። ያልተወሰነ የሰው ብዛት የዘመን ርዝመት ቍጥር፤ ዘጸ. 32፥30፤ 2ነገ. 11፥12፤ ራእ. 20። «ሺህ ዓመት» ይመ.

**ቍጥቋጥ፤** ከዳዊት ዘር ለተገኘው ለመሲሕ የተሰጠ ምሳሌያዊ ስም፤ ኢሳ. 4፥2፤ 11፥1፤ ኤር. 23፥5፤ 33፥15፤ ዘካ. 3፥8።

**ቍጥቋጦ፤** አንድ ዓይነት ዛፍ ሳይሆን ወደ ጫፈቃነት ያልደረሰ በትንሽ መተረቢያና ማጭድ የሚጠረግ አጭር ዛፍ፤ ዘጸ. 3፥2፤ ዘዳ. 33፥16፤ ሉቃ. 20፥37፤ ሐ.ሥ. 7፥30።

**በለሳን፤** ከአትክልት ወገን የሆነ ጥሩ ሽቱነት ያለው ቍጥቋጦ። ሙጫው ወይም ዘይቱ ተነጥሮ ለቍስል ማለስለሻ ቅባት ይሆናል፤ ዘፍ. 37፥25። ቅባቱ ከገለዓድ አገር ስለሚገኝ «በገለዓድ የሚቀባ መድኃኒት የለምን?» ተብሎ ይተረት ነበር፤ ኤር. 8፥22፤ 46፥11።

**በለስ፤** ቅጠሉ ሰፋፊ፥ ነጭ ደም ያለው፥ ፍሬው የሚበላ አጭር ዛፍ ወይም ቍጥቋጦ። ከቤት ጓሮ ይተከል ነበር፤ ዘፍ. 3፥7፤ ዘዳ. 8፥8፤ ማር. 11፥13፤ 13፥28፤ ሚክ. 4፥4።


የበለስ ዛፍና ፍሬው

**በለዓም፤** በመስጴጦምያ አገር ይኖር የነበረ የቢዖር ልጅ፤ ዘዳ. 23፥4። ሁብተ መርገም የተሰጠው ምዋርተኛ ነበረ። እስራኤልን እንዲረግም በሞዓብ ንጉሥ በባላቅ ተቀጠረ፤ ኢያሱ 13፥22። ከአሕዛብ ወገን ቢሆንም እንኳ ስለ እስራኤል አምላክ በጥቂቱ ሰምቶ ነበር። በተገለጠለትም መሠረት እስራኤልን በመርገም ፈንታ ባረካቸው፤ ዘኍ. ም. 22-24። «ከያዕቆብ ኮከብ ይወጣል፥ ከእስራኤል በትር ይነሣል፥ የሞዓብንም ማዕዘኖች ይመታል» በማለት ግሩም የሆነ ቃል ስለ እስራኤል ተናገረ። የኮከቡ ትንቢት በንጉሥ ዳዊት እንዲሁም ደግሞ ከወገኑ በተገኘው በክርስቶስ መምጣት እንደተፈጸመ ይታመናል፤ ዘኍ. 24፥17። በለዓምን አህያይቱ በሰው አንደበት እስክትናገረው ድረስ መልአኩ ገሥጸው። ነገር ግን በለዓም ለጊዜው ለእግዚአብሔር ቢታዘዝም፥ የተንኰል ሥራ መሥራቱ አልቀረም። ይኸውም የእስራኤል ልጆች ከእግዚአብሔር እንዲርቁ ለማድረግ በመምከሩ ነው፤ ዘኍ. 31። ከዚህም የተነሣ በኋላ በእስራኤላውያን እጅ ተገደለ።

በአ.ኪ. ውስጥ ክፉ ተጽእና የሚያሳድሩ የእግዚአብሔርን ሕዝብ የሚያሳዝኑ የግብዝ አስተማሪዎች ምሳሌ ሆኗል፤ ይሁዳ 11፤ 2ጴጥ. 2፥15።

**በሉር፤** እንደ ብርጭቆ ብርሃንን የሚያሳልፍ አረንጓዴ ወይም ምናልባት ቀይ የነበረ ድንጋይ፤ ዘጸ. 28፥18።

**በሊታ፤** በላተኛ ማለት ነው። አንዲት አገር በመከራ፥ በስደትና በሞት ምክንያት ያለ ሰው መቅረትዋን ያሳያል፤ ሕዝ. 36፥13:14።

**በሎታ፤** ከእንጨት ወይም ከብረት የሚበጅ ራሳም ዱላ፥ ከንተሮ፤ አብዛኛውን ጊዜ ከእንጨት የሚበጀው ባለማንጠልጠያ ነው፤ ኢዮብ 41፥21።

**በረሃ፥ የበረሃ ፍየል፤** ኢዮብ 39፥1። «እንስሳት» ይመ.

**በረቅ፤** እንደ ጠመኔ ያለ ነጭ ድንጋይ፤ ኢሳ. 44፥13።

**በረኛ፤** የከተማን ወይም የቤትን በር የሚጠብቅ ዘበኛ፤ 1ዜ.መ. 23፥5፤ ዕዝ. 7፥24፤ ማር. 13፥34።

**በረከት፤** ሰው ወይም ማንኛውም ነገር እንዲበዛ (ዘፍ. 1፥22:28)፥ ወይም ጠቃሚ እንዲሆን (ዘፍ. 2፥3፤ 1ቆሮ. 10፥16)፥ እንዲሁም መልካም ነገርን እንዲያገኝ መመረቅ በረከት ይባላል፤ ኤፌ. 1፥3። እግዚአብሔር ይባርካል፤ ሰዎችም በረከትን ይሰጣሉ፤ ዘኍ. 6፥22-27፤ 2ቆሮ. 13፥14። ሰዎች ለእግዚአብሔር የሚያቀርቡት ምስጋና በረከት ይባላል፤ መዝ. 144፥1፤ 1ዜ.መ. 29፥10።

**በረዶ፤** ሰብልንና እንስሳን፥ ሰውንም ሊያጠፋ ይችላል፤ ዘጸ. 9፥23-26፤ ኢያሱ 10፥11። በምሳሌነት የእግዚአብሔር ኃይል (ኢሳ. 28፥17)፥ ቍጣውም ይገለጥበታል፤ ራእ. 16፥21።

**በራይሌ፤** «እንስሳት» ይመ.

**በሬ፤** «ከብት» ይመ.

**በር፤** ወደ ከተማ የመግቢያና የመውጫ መዝጊያ። ብዙ ጊዜ በር ከእንጨት ይሠራና እንዳይቃጠል በናስ ይሸፈን ነበር፤ መዝ. 107፥16፤ ኢሳ. 45፥2። ስፋቱ 3 ሜትር ያህል ሲሆን፥ በግራና በቀኝ ግንቦች ይሠራሉ። በሮች በብረት ወይም በእንጨት መወርወሪያዎች ይዘጉ ነበር፤ 1ነገ. 4፥13። ማታ ይዘጋሉ። ጧት ይከፈታሉ፤ ኢያሱ 2፥5-7። በበሩ አጠገብ ባለው አደባባይ መቀመጫዎች ነበሩ። ከዚያም ጉዳይ ይፈጸም፤ ዐዋጅ ይታወጅ፤ ፍርድ ይሰጥ ነበር፤ ሩት 4፥1-11፤ ምሳ. 22፥22፤ 2ሳሙ. 19፥8። በበር መቀመጥ ማለት በከተማ ከሽማግሌዎች መካከል እንደ አንድ ሆኖ መቈጠር ማለት ነው፤ ዘፍ. 19፥1፤ ምሳ. 31፥23። በአ.ኪ. በር የክርስቶስን ወንጌል የመስበክ ዕድል ምሳሌ ነው፤ ዮሐ. 10፥1-7፤ 1ቆሮ. 16፥9። ሥዕሉን በገጽ 104 ይመ.

**በርባን፤** በኢየሩሳሌም ሁከትን ያስነሣ ወንበዴና ነፍስ ከገደሉት ዐመፀኞች መካከል የታወቀ እስረኛ። በኋላ ግን በፋሲካ ልማድ መሠረት በጲላጦስ ተፈትቷል፤ ኢየሱስ በበርባን ስፍራ ተገርፎ በመስቀሉ ለኃጢአተኞች ሁሉ መሞቱ ግልጽ ሆኗል፤ ማቴ. 27፥16-26፤ ማር. 15፥6-15፤ ሉቃ. 23፥18-19:25፤ ዮሐ. 18፥39-40።

**በርተሎሜዎስ፤** ከዐሥራ ሁለቱ ሐዋርያት አንዱ፤ ማቴ. 10፥3። በርተሎሜዎስ ማለት

የተሎሜዎስ ልጅ ማለት ነው። ምናልባት በርተሎሜዎስ የተባለው ናትናኤል ይሆናል። «ሐዋርያ» ይመ.



ነጋዴዎች በከተማ በር ላይ ሲነግዱ

**በርኒቄ፤** «ሄሮድስ» ይመ.

**በርናባስ፤** በቆጵሮስ የተወለደ ሌዋዊ። የመጀመሪያ ስሙ ዮሴፍ ነበረ፤ ሐዋርያት ግን በርናባስ ብለው ሰየሙት። ፍቹ የመጽናናት ልጅ ማለት ነው። ድሆችን ለመርዳት መሬቱን ሸጠ፤ ሐ.ሥ. 4፥36። ጳውሎስን ወደ ሐዋርያት አቀረበ፤ ሐ.ሥ. 9፥26-27። በኋላም ወደ አንጾኪያ አመጣው፤ እዚያም አብሮት ሠራ፤ ሐ.ሥ. 11፥22-26። በመጀመሪያው የስብከት ጉዞ ከጳውሎስ ጋር (ሐ.ሥ. 13ና 14)፥ ወደ ኢየሩሳሌም ሸንጎ ሄደ፤ ሐ.ሥ. 15። ስለ ማርቆስ በተነሣው ክርክር ከጳውሎስ ተለይቶ ወደ ቆጵሮስ ተመለሰ፤ ሐ.ሥ. 15፥36-41፤ 1ቆሮ. 9፥6፤ ገላ. 2፥1-9:13፤ ቆላ. 4፥10።

**በርኖስ፤** ከበግና ከፍየል ጠጉር የሚሠራ ማቅ። ጳውሎስ በርኖስ ይለብስ ነበር፤ 2ጢሞ. 4፥13።

**በርጤሜዎስ፤** ዕውር የነበረና በኢያሪኮ አጠገብ በኢየሱስ የተፈወሰ የጤሜዎስ ልጅ። ከእርሱ ጋር ሌላ ዕውርም እንደተፈወሰ ማቴዎስ ገልጧል፤ ማቴ. 20፥29-34፤ ማር. 10፥46-52፤ ሉቃ. 18፥35-43።

**በሽታ፤** ደዌ፥ ሕማም። በሽታ በኃጢአት ምክንያት ወደ ዓለም ገባ። የኃጢአትም ሁኔታ በበሽታ ምሳሌነት ተገለጠ፤ ኢሳ. 1፥6። አዳም ሲወድቅ ወዲያውኑ ፍርሃትና ሥቃይ ተሰማው፤ ዘፍ. 3፥10:16:17፤ 4፥13። እግዚአብሔር እርሱን ሲከተሉ ሕዝቡን ከበሽታ እንደሚያድናቸው ተስፋ ሰጣቸው፤ ዘጸ. 15፥25:26፤ ዘዳ. 7፥12-16። እግዚአብሔር በማይታዘዝ ሕዝብ ላይ በሽታን ያመጣል፤ ዘሌ. 26፥14-16፤ ዘዳ. 28፥22:27:58-61፤ ኤር. 24፥10። ልዩ ልዩ ሰዎች እንደ ሙሴ እኅት እንደ ማርያምና እንደ ግያዝ፥ እንደ ዘካርያስና እንደ በርያሱስ የመሳሰሉት ኃጢአት በሠሩ ጊዜ ወዲያውኑ በበሽታ ተቀጡ፤ ዘኁ. 12፥10፤ 2ነገ. 5፥25-27፤ ሉቃ. 1፥20፤ ሐ.ሥ. 13፥11። ብዙ ጊዜ ግን በሽታ የሚመጣው በግል ኃጢአት ምክንያት ላይሆን ይችላል፤ ዮሐ. 9፥2:3። ሰይጣን ሰውን በበሽታ ለመምታት ይፈቀድለት ይሆናል፤ ኢዮብ 2፥4-7፤ ሉቃ. 13፥16፤ ሐ.ሥ. 10፥38። «ጤና»፥ «ፈውስ» ይመ.

የመ.ቅ. ጸሐፊዎች ስለ በሽታዎች ሲጽፉ እንደ ዛሬ የሥነ ፍጥረት ሊቃውንት ሳይሆን፥ የዘመናቸውን ሕዝብ አቋም እንደተመለከቱት የደዌን ሁኔታ ገልጠዋል። በመ.ቅ. እንደተጠቀሱት ለምጽን የመሳሰሉት ቃላት ብዙ ዓይነት በሽታን አጠቃልለው ሊያመለክቱ ይችላሉ። ስለዚህም ብዙ ጊዜ በሽታ በመ.ቅ. ሲገለጥ የበሽታው ዓይነት እንጂ ልክ እንደ ዛሬ ሳይንስ (ሥነ ፍጥረት) አገላለጥ በሽታው ሊታወቅ አይችልም። ሐዋርያት ከአጋንንት በሚነሡና በሌሎች በሽታዎች መካከል ልዩነት መኖሩን አሳይተዋል፤ ማር. 1፥34። በዘመናዊ ሥነ ፍጥረት አገላለጥ ሳይሆን፥ ጸሐፊዎች እንደተመለከቱአቸው በመ.ቅ. የተጠቀሱ በሽታዎችን በሚከተሉት አራት አርእስት ለማጠቃለል እንሞክራለን።

1. በቆዳ ላይ የሚታዩ። ለምጽ፥ ቁረቁር፥ እባጭ፥ ብጉር፥ ቋቁቻ (ዘሌ. 14፥54-57)፥ ችፌ (ዘዳ. 28፥27)፥ የቊስል ጠባሳ (ዘሌ. 13፥23)(የአመንዝራ ቊስል) ቂጥኝ... ወዘተ. (ምሳ. 6፥32:33፤ ሚክ. 1፥9)፥ እከክ (ዘሌ. 21፥20)፥ ክፉ ቊስል (ኢዮብ 2፥7)፥ ፈሳሽ ነገር፤ ዘሌ. 15፥2። ዋናው ቁም ነገር በሽታው ርኩስና ተላላፊ መሆኑን ወይም አለመሆኑን ለማረጋገጥ ነበር።

2. የአእምሮ (የአንጎል) በሽታ። እብደት (ዘዳ. 28፥28)፥ ክፉ መንፈስ (1ሳሙ. 16፥14)፥ እንስሳን መምሰል፤ ዳን. 4፥33። ብዙ በሽታ በኃጢአት፥ በፍርሃት፥ በብስጭትና በሌላም ምክንያት እንደሚነሣ ተገልጧል፤ መዝ. 32፥9:10፤ 39፥3-11፤ ምሳ. 14፥30፤ 15፥30፤ 17፥22፤ ማር. 2፥1-12፤ ያዕ. 5፥14-16።

3. ከአጋንንት የሚነሡ። ጋኔን ሰውን ሊያሳብድ (ማር. 5፥1-5)፥ ሊጥል (ማር. 9፥18)፥ ልዩ ልዩ የአካል

ብልቶችም እንዳይሠሩ ሊያደርግ ይችላል። «ጋኔን» ይመ.

4. ልዩ ልዩ የሰውነት በሽታ። መቅሠፍት (ዘኍ. 11፥33)፥ ተቅማጥ (ሐ.ሥ. 28፥8)፥ ትል (ሐ.ሥ. 12፥23)፥ ትኵሳት፥ ንዳድ፥ ክሳት፥ ጥብሳት (ዘዳ. 28፥22)፥ የሆድ መነፋት (ሉቃ. 14፥2)፥ የሆድ በሽታ (1ጢሞ. 5፥23)፥ ከጊንጥና ከእባብ መርዝ የሚመጣ፤ ዘኍ. 21፥6፤ ዘዳ. 8፥15። ሰው ዐይነ ልም (ዘፍ. 29፥17)፥ በእርጅናም ምክንያት ዐይነ ሬዛዛ ሊሆን ይችላል፤ ዘፍ. 27፥1። ሰው በበሽታ ምክንያት ሽባ (ማር. 2፥3)፥ ደንቆሮና ኰልታፋ (ማር. 7፥32)፥ ዕውር፥ አንካሳ፥ ድንክ፥ ጃንደረባና ጕባጣ ሊሆን ይችላል፤ ዘሌ. 21፥18-20። «ጤና፥ ፈውስ» ይመ.

**በቀል፤** ብድራትን ክፋትን መመለስ። ሳምሶን ፍልስጥኤማውያንን ተበቀለ፤ መሳ. 15፥7:8። እስራኤል የእግዚአብሔርን በቀል በምድያም ፈጸሙ፤ ዘኍ. 31፥1-3። የእግዚአብሔር ሰዎች መበቀል አይገባቸውም፤ በቀል የእግዚአብሔር ፈንታ ነውና፤ 2ሳሙ. 22፥48፤ ሮም 12፥19፤ ዕብ. 10፥30። ቂምን በመያዝ ፈንታ ጠላትን መውደድ እንደሚገባቸው ታዝዘዋል፤ ማቴ. 5፥44:45፤ ሮም 12፥20። ሆኖም ሰዎች እልከኞች ሆነው በእግዚአብሔር ሥራ ላይ ቢነሡና ተቃውሟቸውን ቢያከሩ የእግዚአብሔር በቀል በጠላቶቹ እንዲደርስ እግዚአብሔርን መጠየቅ ተገቢ ልመና ነው፤ መዝ. 18፥47፤ መዝ. 69፥22-28፤ 109፤ ራእ. 6፥10፤ 19፥1-3። የእግዚአብሔር በቀል በኃጢአተኞች ላይ የሚገለጠው እንደጽድቁ ነውና ሥራቸውን በትክክል ይመልስላቸዋል፤ ዘዳ. 32፥35።

**በቅሎ፤** «እንስሳት» ይመ.

**በቋል፤** በቆሎንና ልዩ ልዩ እሸትን ፈልፍላ የምትበላ «ጥሬ ፈጅ» ወፍ፤ ዘሌ. 11፥16። «ወፎች» ይመ.

**በተሃ፤** ያልበሰለ፥ ለጋ ብርዝ ጠጅ፤ ኢዩ. 1፥5። የእግዚአብሔር በረከት ምሳሌ ነው፤ ኢዩ. 3፥18።

**በትረ መንግሥት፤** ከሰባቱ የንግሥ መጣሪያዎች አንዱ። ነገሥታት በሚነግሡበት ጊዜ በትረ መንግሥት ይይዛሉ፤ ዘፍ. 49፥10፤ መዝ. 45፥6።

**በትር፤** ጠንካራ የሆነ በእጅ የሚያዝ የእንጨት መቋሚያ፤ መዝ. 23፥4። ብዙ ጊዜ የሥልጣን ምልክት ነው፤ ኢሳ. 9፥4፤ ዘኍ. 24፥17፤ ኢሳ. 11፥1። ሙሴ በበትሩ ተአምራትን አደረገ፤ ዘጸ. 4፥2-5፥17፤ 9፥23፤ 14፥16። የአሮን በትር ወደ እባብነት ተለውጣ የጠንቋዮችን በትር ዋጠች፤ ዘጸ. 7፥9-12። በትሪቱ በመለምለምዋ የአሮን ክህነት ተረጋገጠ፤ ዘኍ. 17፤ ዕብ. 9፥4። ሰዎች በበትር ስለሚገረፉ በትር የቅጣትና የመከራ ምሳሌ ነው፤ ኢዮብ 9፥34፤ ኢሳ. 10፥5።



የእረኛ በትርና ሌላ ዕቃ

**በናያስ፤** ትርጓሜው እግዚአብሔር አጸና ማለት ነው። የዳዊት የክብር ዘብ አለቃና ጀግና የሆነ በይሁዳ አገር የተወለደ የካህን ልጅ፤ 2ሳሙ. 8፥18፤ 23፥20-23፤ 1ዜ.መ. 27፥5:6። ዳዊት ከሞተ በኋላ አዶንያስን ተቃወመ (1 ነገ. 1)፥ አዶንያስን፥ ኢዮአብንና ሳሚን በመግደል የሰሎሞንን መንግሥት አጸና፤ የሠራዊቱም አለቃ ሆነ፤ 1ነገ. 2፥24-46።

**በአል፤** ጌታ ወይም ባለቤት ማለት ነው።

1. ይህ ስም ብዙውን ጊዜ የፊንቃውያንንና የከነዓናውያንን የእርሻ አምላክ ያመለክታል። በእነርሱ እምነት ብዙ እህል፥ ትልቅ መንጋ፥ ለገበሬዎችም ብዙዎች ልጆችን የሚሰጥ አምላክ ተብሎ ይመለክ ነበር። እያንዳንዱ አካባቢ ወይም አገር የራሱ በአል ነበረው። በአሉች፥ ወይም በዕብራይስጥ አነጋገር በአሊም ብዙዎች ነበሩ ማለት ነው። በከነዓን አገር በአሊም የሚመለኩት በከፍተኛ ቦታዎች ነበረ፤ መሠዊያዎችም ተሠርተውላቸው ነበር። የአምልኮውም ሥነ ሥርዓት ዝሙት፥ ራስን ማጕሳቈል፥ ሰውንም መሥዋዕት አድርጎ ማቅረብ ነበረ። ብዙዎች የእስራኤልና የይሁዳ ነገሥታት የበአልን አምልኮ ይደግፉና ያስፋፉ ነበር። በተለይም ኤልዛቤልና ጎቶልያ የተባሉት ንግሥታት በዚህ ርኩስ ሥራ ስማቸውን አስጠርተዋል፤ 1ነገ. 16፥31-32፤ 2ዜ.መ. 17፥3።

ኤልያስ የእስራኤል ንጉሥ አክዓብ የፈጸመውን ክፉ ሥራ ፊት ለፊት ተናገረ፤ የበዓልንም ነቢያት አጠፋቸው፤ 1ነገ. 18፥18:40። ሆሴዕ እስራኤልን ለበአሊም መሥዋዕት በማቅረባቸው ወቀሳቸው፤ ሆሴዕ 11፥2። እግዚአብሔር «በዚያ ቀን ባሌ ብለሽ ትጠሪኛለሽ እንጂ ዳግመኛ በአሌ ብለሽ አትጠሪኝም» በማለት የሚመጣውን የተሐድሶ ዘመን አመለከተ፤ ሆሴዕ 2፥18። ኤርምያስም የይሁዳን ሕዝብ በዚህ ምክንያት ገሠጸ፤ ኤር. 9፥14።

2. በአል የሚለው ቃል የአምላክ ስም ከመሆኑም በላይ ለብቻው ወይም ደግሞ ከሌላ ስም ጋር ተያይዞ ሲገኝ፥

የሰው ወይም የአገር መጠሪያ ሊሆን ይችላል፤ ለምሳሌ የንጉሥ ሳዖል ልጅ አስበአል (የበአል እሳት) ተብላ ተጠርታለች፤ 1ዜ.መ. 8፥30:33፤ 1፥49፤ ኢያሱ 11፥17።



1500 ገደማ ከክ.በ. በከነዓን የተሠራ የበአል ቅርጽ

እስራኤላውያን በዚህ ዓይነት ልጆቻቸውን፥ የሚኖሩበትንም ቀበሌ በጣዖት ስም መሰየማቸው፥ የእግዚአብሔርን ስም መርሳታቸውንና ወደ አምልኮ ባዕድ ማዘንበላቸውን ይመሰክርባቸዋል።

**በዓለ ኀምሳ፤** በብ.ኪ. የመከር በዓል ነው፤ ዘጸ. 23፥16፤ 34፥22። ኀምሳው ቀን የተቈጠረው ከፋሲካ ጀምሮ ነው («በዓላት» ይመ.)። በአ.ኪ. ደግሞ መንፈስ ቅዱስ የወረደበት ዕለት ነው። ከትንሣኤ ጀምሮ በመቍጠር ኀምሳኛው ቀን ላይ ይውላል፤ ሐ.ሥ. 2፥1-4። «መንፈስ ቅዱስ» ይመ.

**በዓላት (የአይሁድ)፤** በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ ለአይሁድ በትእዛዝ የታወጁ በዓላት ሰባት ናቸው፤ በሳምንት አንድ፥ በዓመት ደግሞ ስድስት ሲሆኑ አንድ ሌላ በዓል (ስምንተኛ) በመቃብያን ዘመን ተጨመረ።

1. የሰንበት በዓል፤ ዘሌ. 23፥2-3። «ሰንበት» ይመ.

2. የቂጣ በዓል፥ ወይም ፋሲካ (በዓለ ናእት) የእስራኤል ከግብጽ አገር የመውጣታቸው መታሰቢያ፤ ዘጸ. 12፥1-20፤ ዘሌ. 23፥5-8። «ፋሲካ» ይመ.

3. የመከር በዓል (በዓለ ሠዊት)፥ ወይም (ሰባቱ ሱባዔ) ሰባት ሳምንት ከፋሲካ በኋላ ይከበራል። በዓሉ የስንዴ በኵራት አጨዳ መታሰቢያ፥ የምስጋና ጊዜ ነው፤ ዘጸ. 23፥16፤ 34፥22፤ ዘኍ. 28፥26። በአ.ኪ. ዘመን በዓለ ኀምሳ ተባለ (ሐ.ሥ. 2፥1)፥ ይህም በግሪክ ቋንቋ ጴንጠቆስጤ ይባላል። «መከር» ይመ.

4. የዳስ በዓል (በዓለ መጸለት)፥ ወይም የአዝመራ ማከማቻ በዓል። በሰባተኛው ወር በዐሥራ አምስተኛው ቀን እህል ከተከማቸ በኋላ የእስራኤል ልጆች ሰባት ቀን በዳስ ውስጥ እየተቀመጡ አምላካቸውን ያመሰግኑ ነበር፤ ዘሌ. 23፥39-43።

5. መለከቶች የሚነፉበት ቀን፤ ዘሌ. 23፥23-25፤ ዘኍ. 29፥1።

6. የማስተስረያ ቀን። በሰባተኛው ወር በዐሥረኛው ቀን አይሁድ ሁሉ ራሳቸውን እያዋረዱ የእግዚአብሔርን ይቅርታ ይለምኑ ነበር፤ ዘሌ. 23፥26-32። «የማስተስረያ በዓል» ይመ.

7. ፉሪም። በአስቴር ዘመን አይሁድ ከጠላቶቻቸው ዕረፍትን ያገኙባቸው ቀኖች ፉሪም ተብለው የደስታ በዓል እንዲደረግባቸው ታውጆአል፤ አስ. 9፥16-28። «ፉሪም» ይመ.

8. የመቅደስ መታደስ መታሰቢያ በዓል፤ ዮሐ. 10፥22። ከኦሪትና ከነቢያት በኋላ በመቃብያን ዘመን ተጀመረ። የሶርያ ንጉሥ አንጥዮኩስ ኤጲፋንዮስ ቤተ መቅደሱን ካረከሰ በኋላ መቃብያን እንደገና 165 ከክ.በ. ቀደሱት።

በኦሪት ሕግ እስራኤላውያን ሁሉ ሰንበትን ለማክበር ተገደዋል። ደግሞም ወንዶች ሁሉ በቂጣ በዓል፥ በበዓለ ኀምሳና በዳስ በዓል በቤተ መቅደስ መገኘት ግዴታቸው ነበረ፤ ዘዳ. 16፥16።

**በዓላት (የክርስቲያን)፤** እንደ አይሁድ በዓላት የክርስቲያን በዓላት በአ.ኪ. አልታወጁም። ሆኖም ቤ.ክ. የክርስቶስን ሥራ ለማስታወስ የምታከብራቸው በዓላት አሉ። ታላላቆቹ በዓላት ልደት፥ ጥምቀት፥ ስቅለት፥ ትንሣኤ፥ ዕርገት፥ ጰራቅሊጦስ (የመንፈስ ቅዱስ መውረድ) ናቸው፤ ራእ. 1፥10።

**በኵር፤** ከሰው ወይም ከከብት በመጀመሪያ የሚወለድ። ቃሉ ብዙ ጊዜ ለወንድ ጾታ ያደላል። በእስራኤል የበኵር መብት (ብኵርና) ትልቅ ነበርና አንድ በኵር አባቱ በሌለበት እንደ ሮቤል ለወንድሞቹ ኀላፊ ነው፤ ከርስት ሁለት እጅ ያገኛል። በቤተ መንግሥትም አልጋ ወራሽ ነው። በኵር ቢያጠፋ ብኵርናው ለሌላው ሊተላለፍ ይችላል፤ ዘፍ. 25፥29-34፤ 27፤ 37፥29:30፤ 49፥3:4፤ ዘዳ. 21፥15-17፤ 1ዜ.መ. 5፥1:2፤ 2ዜ.መ. 21፥1-3። እግዚአብሔር በመቅሠፍት የግብጽ በኵሮችን አጥፍቶ ከግብጽ ባርነት ቤት እስራኤልን ከነበኵሮቻቸው ስላዳነ የእስራኤል በኵር ሁሉ የእግዚአብሔር ሆነ። እንዲሁም በበኵር ፈንታ ሌዋውያንን ለራሱለየ፤ ዘጸ. 12፥12፤ ዘኍ. 3፥13:40:41። ከዚያም ወዲህ የሚወለደው በኵር በአምስት ሰቅል ይዋጅ ነበር። ስለ እንስሳትም በኵራት ቤዛ ልዩ ልዩ ሕግ ነበረ፤ ዘኍ. 3፥42-51፤ 18፥15-17። ኢየሱስ ለእናቱ በኵር ነውና በቤተ መቅደስ ቤዛ ተሰጠለት፤ ሉቃ. 2፥7:27። ክርስቶስ የምእመናን በኵር (ሮም 8፥29፤ ዕብ. 1፥6)፥ በትንሣኤው የሙታን በኵር (ቆላ.

1፥18፤ ራእ. 1፥5)፥ ዓለምን ፈጥሮ በዓለም ሁሉ ላይ ስለ መግዛቱ የፍጥረት በኵር ተብሏል፤ ቆላ. 1፥15። አማኞች የእግዚአብሔርን መንግሥት ስለሚወርሱ በኵራት ተብለዋል፤ ዕብ. 12፥23፤ ያዕ. 1፥18።

**በደል**፤ ጥፋት፥ ኃጢአት ማለት ነው። ብዙ ጊዜ በሰው ላይ በዕውቀትና በድፍረት የሚደረገውን ያመለክታል፤ መዝ. 51፥2:4፤ ዳን. 9፥5። «ኃጢአት» ይመ.

**በገና**፤ አውታር ያለው የዜማ ዕቃ። ብዙ ጊዜ ስምንት ወይም ዐሥር የጅማት አውታሮች ይኖሩታል፤ ዘፍ. 4፥21፤ 1ሳሙ. 16፥16:23፤ 1ዜ.መ. 15፥21፤ መዝ. 33፥2፤ ራእ. 5፥8።



**በግ**፤ ሥጋው ለመሥዋዕትና ለምግብ፥ ጠጕሩና ቆዳው ደግሞ ለልብስ የሚሆን የዋህ የቤት እንስሳ፤ ዘፍ. 4፥2፤ 38፥12፤ ዘሌ. 22፥19፤ ዘጸ. 14፥3:4፤ ዕብ. 11፥37። በግ በተለይም ለፋሲካ መሥዋዕት ይታረድ ነበር (ዘጸ. 12፥3-5)፥ ስለዚህ ክርስቶስ «የዓለምን ኃጢአት የሚያስወግድ የእግዚአብሔር በግ» ተብሏል፤ ዮሐ. 1፥29፤ ራእ. 5፥6:12።

ሰው በብዙ ምክንያት በበግ ተመስሏል በግ ወዳጅነትን ይቀበላል (2ሳሙ. 12፥3፤ ዮሐ. 10፥4:14:15)፥ ሳያስተውል በራሱ መንገድ ሄዶ ይጠፋል (ኢሳ. 53፥6፤ ማቴ. 18፥12፤ 1ጴጥ. 2፥25)፥ በራሱ የመከላከልም ኃይል የለውምና ያለ እረኛ ተስፋ አይኖረውም፤ ኢሳ. 53፥7፤ ማቴ. 9፥36፤ ዮሐ. 10፥12፤ ሮም 8፥36። በግ ንጹሕና የማይጐዳ የዋህ እንስሳ ስለሆነ፥ ሐሰተኞች የዋህ ለመምሰል የበግ ለምድ በሚለብሱ ተመስለዋል፤ ማቴ. 7፥15። በጎች ክርስቶስን የሚከተሉ ምእመናን ምሳሌ ናቸው፤ ማቴ. 25፥33።

**በጎነት**፤ ማንኛውም መልካምና ጥሩ ሥራ። እግዚአብሔር በባሕርዩና በሥራው የበጎነት ምንጭና መነሻ ነው፤ መዝ. 16፥2፤ ሮም 8፥28። በጎነት በአማኞች ሕይወት የሚገኘው ከመንፈስ ቅዱስ ነው፤ ገላ. 5፥22። ሰዎች የእግዚአብሔር ልጆች መሆናቸውን የሚገልጡት በጎነትን በማድረግና በመከታተል ነው፤ ኤፌ. 5፥8-10፤ ቲቶ 3፥8።

**በጢህ**፤ የዱባ ዓይነት ተክል፤ ዘኍ. 11፥5።

**በፍታ**፤ ጥሩ ለስላሳ ልብስ፤ በዱሮ ጊዜ ከተልባ እግር ተፈትሎ ይሠራ ነበር፤ መሳ. 14፥12፤ ኢሳ. 3፥23።

**ቡሀንት**፤ (በራነት)። «ጠጕር» ይመ.

**ቡሃቃ**፤ የቡሆ ዕቃ፥ ሊጥ የሚቦካበት፤ ዘጸ. 8፥3፤ 12፥34።

**ቡላድ**፤ ጠንካራ የድንጋይ ዓይነት። በብረት ሲመቱት እሳት ይወጣዋል፤ ኢዮብ 28፥9፤ ኢሳ. 5፥28፤ ሕዝ. 3፥9።

**ቡል**፤ «ወር» ይመ.

**ቡሩክ፥ ቡሩካን**፤ የተባረከ፥ በረከትን የተቀበለ፥ የተመሰገነ፤ ማር. 14፥61፤ ኢሳ. 65፥23።

**ቢላዋ**፤ ስለታም ካራ፤ ዘፍ. 22፥6።

**ቢረሌ**፤ ብርሌ፤ እንደ ብርጭቆ ብርሃንን የሚያስተላልፍና ብልጭታ ያለው የከበረ ድንጋይ። ነጭ፥ ቀይ ወይም አረንጓዴ ሊሆን ይችላል፤ ዘጸ. 28፥20፤ ዳን. 10፥6፤ ራእ. 21፥20።

**ቢተዋ**፤ ከማዕድን የሚሠራ፥ ወታደር በክንዱ ላይ እንደ አንባር የሚያደርገው ጌጥና የጕራዴ መከላከያ፤ 2ሳሙ. 1፥10።

**ቢታንያ**፤ የበለስ ቤት ማለት ነው። 1. ከኢየሩሳሌም በስተምሥራቅ አምስት ኪ.ሜ. ርቆ ከደብረ ዘይት ወዲያ የሚገኝ መንደር። ዛሬ ሌልአዛሪያ ይባላል። የማርያም፥ የማርታና የአልዓዛር (ዮሐ. 11፥1)፥ የለምጻሙ የስምዖንም መኖሪያ ነበር፤ ማቴ. 26፥6። ክርስቶስ ከቢታንያ ወደ ሰማይ ዐረገ፤ ሉቃ. 24፥50:51። 2. ከዮርዳኖስ በስተምሥራቅ የሚገኝ መንደር፤ ዮሐ. 1፥28። 3. ከገላትያ በስተሰሜን ያለ አገር። ዛሬ በቱርክ አገር ውስጥ ነው። ጳውሎስ ወንጌልን በዚያ እንዳይሰብክ ተከለከለ፤ ሐ.ሥ. 16፥6-10። የጴጥሮስ አንደኛ መልእክት ወደዚያ ተላከ፤ 1ጴጥ. 1፥1:2። ከ. 6በ።

**ባለ መድኃኒት**፤ «ፈውስ» ይመ.

**ባለ ቅኔ**፤ በጥንት ዘመን ባለ ቅኔዎች በየሀገሩ የታወቁና የተከበሩ ነበሩ፤ በተለይም በእስራኤልና በግሪክ ብዙ ባለ ቅኔዎች ነበሩ። ጳውሎስ አንዳንድ ጊዜ አሳቡን ለመግለጥ ከአሕዛብ ባለቅኔዎች ጠቅሷል፤ ሐ.ሥ. 17፥28። ክሊያንትስ (ቲቶ 1፥12)፥ ኢፒመንዴስ (1ቆሮ. 15፥33)፥ መናንደር የተባሉት ባለ ቅኔዎች ተጠቅሰዋል። «ቅኔ» ይመ.

**ባለጠግነት**፤ «ሀብት» ይመ.።

**ባላቅ**፤ እስራኤልን እንዲረግምለት በለዓምን የቀጠረ የሞዓብ ንጉሥ። «በለዓም» ይመ.

**ባላንድ ቀንድ**፤ አውራሪስ የሚመስል ኃይለኛ አውሬ፤ ዘኍ. 23፥22፤ 24፥8፤ መዝ. 29፥6። ቃሉ በዕብራይስጥም በግእዝም ርኤም ነው። በአማርኛ ግን ከረከንድ ይባላል። አንዳንድ ጊዜ ጐሽ ተብሎ ተተርጕሟል፤ ኢዮብ 39፥9:10፤ ኢሳ. 34፥7።

**ባላገር**፤ አገርና ርስት ያለው ስደተኛ ያልሆነ ተወላጅ። ምእመናን በእግዚአብሔር መንግሥት እንደ ባላገሮች ናቸው፤ ኤፌ. 2፥19።

**ባላጋራ**፤ ጠላት፥ ደመኛ፤ የሌላውን ሀብት በግፍ የሚጋራ። የሰይጣን ምሳሌ ነው፤ ኢሳ. 59፥18፤ 1ጴጥ. 5፥8።

**ባል**፤ የሚስት ራስ። ሚስቱን እንደራሱ መውደድ አለበት፤ ኤፌ. 5፥22-33፤ ቆላ. 3፥19፤ 1ጴጥ. 3፥7። «ጋብቻ»፥ «ወንድ» ይመ.

**ባልቴት**፤ በዕድሜዋ የገፉች አሮጊት። 60 ዓመት የሆናት ሴት ባልቴት ትባላለች። እግዚአብሔር ለባልቴት ይራራል (መዝ. 68፥5፤ ምሳ. 15፥25)፥ በሙሴም ሕግ የባልቴቶች መብት እንዲጠበቅ ተደረገ፤ ዘጸ. 22፥22፤ ዘዳ. 14፥29፤ 16፥14፤ 24፥19-21፤ 26፥12፤ 27፥19፤ ኤር. 7፥6፤ ሚል. 3፥5። በሐዋርያት ዘመን ቤ.ክ. ባልቴቶችን ትንከባከብ ነበር፤ ያዕ. 1፥27፤ 1ጢሞ. 5፥4:9:10። «መበለት» ይመ.

**ባልደራስ**፤ ፈረስ ጠባቂ፥ ፈረስ ገሪ ማለት ነው፤ 1ነገ. 9፥22።

**ባልንጀራ**፤ በብ.ኪ. ባልንጀራ የሚባል በጉርብትና የሚኖር እስራኤላዊ ነበር። ከዐሥሩ ትእዛዛት ውስጥ ከስድስተኛው እስከ ዐሥረኛው ድረስ ያለው ሰው ለባልንጀራው ያለበትን ኀላፊነት ይገልጣል፤ ዘጸ. 20፥13-17። ባልንጀራችንን መውደድ እንደሚገባን ብሉይ ኪዳንና አዲስ ኪዳን ያዝዙናል፤ ዘሌ. 19፥18፤ ምሳ. 14፥21፤ ማቴ. 19፥19። ክርስቶስ ለዓለም ሰዎች ሁሉ ስለሞተ ሰው ሁሉ ባልንጀራችን ነው፤ ሉቃ. 10፥25-37።

**ባልጩት**፤ ስለታም ድንጋይ። ምንም እንኳ ቢላዋ ቢኖርም (ዘፍ. 22፥6)፥ አንዳንድ ጊዜ ግዝረት በባልጩት ይፈጸም ነበር፤ ዘጸ. 4፥25፤ ኢያሱ 5፥2:3።

**ባሕር**፤ ታላቅ የውሃ ክምችት። እግዚአብሔር ባሕርን ፈጠረ (ዘፍ. 1፥9:10)፥ ይገዛልም፤ መዝ. 93፥3-4። በባሕሮች ተአምራትን አደረገ፤ ዘጸ. 14፤ ዮናስ 1፥4። ኢየሱስ ባሕርን ጸጥ አደረገ፤ በላዩም ተራመደ፤ ማር. 4፥33-41፤ ዮሐ. 6፥19። መ.ቅ. ምድር በባሕር ላይ የተመሠረተች ናት ይላል፤ ይህም በባሕር መከበብዋን ያሳያል፤ መዝ. 24፥1:2። ባሕር የፍርድ ምሳሌ ነው፤ ራእ. 20፥14:15። ባሕር ለእስራኤል ሰዎች አስፈሪ ነውና በመንግሥተ ሰማያት አይገኝም፤ ራእ. 21፥1። በመ.ቅ. ባሕር ሲል ብዙ ጊዜ የሜዲቴራንያንን ባሕር ያመለክታል። ካ. 1ሀ። ሜዲቴራንያን ባሕር (ዘኍ. 13፥29)፥ ታላቁ ባሕር (ኢያሱ 1፥4)፥ የምዕራብ ባሕር (ዘዳ. 11፥24)፥ የፍልስጥኤም ባሕር ይባላል፤ ዘጸ. 23፥31። ከዚህም ሌላ የኤርትራ ባሕር (ዘጸ. 13፥18፤ ካ. 1መ)፥ የጨው ባሕር (ዘፍ. 14፥3፤ ካ. 2ለ)፥ የጌኔሬት ወይም የገሊላ ባሕር (ዘኍ. 34፥11፤ ማር. 1፥16፤ ካ. 5ለ) ተጠቅሰዋል። ባሕር የኤፍራጥስን (ኢሳ. 21፥1-3) እና የዐባይን ወንዝ (ኢሳ. 18፥2) ሊያመለክት ይችላል። ነገር ግን የኢያዜር ባሕር ሲል ምን እንደሚያመለክት አይታወቅም፤ ኤር. 48፥32።

**የባሕር ልሳን**፤ የባሕር ሠላጤ፥ ወደ የብስ የወጣ ባሕር፤ ኢያሱ 15፥2-5፤ 18፥19።

**ባሕርይ**፤ የቀዋሚ ነገር ሁሉ ምክንያትና መሠረት። ባሕርይ የሚገለጠው በአካል ነው። ባሕርይ ያለ አካል ሊገኝ አይችልም። ቃሉ በሁለት መንገድ ይነገራል። 1. የሰውና የማናቸውም ፍጥረት ባሕርይ፤ የሰው ባሕርይ የሚስማማውን ትቶ የማይስማማውን ሌላ ነገር ለማድረግ ይለወጣል፤ ሮም 1፥26:27። ሰው በባሕርዩ በዋቂ ስለሆነ ያልተሰጠውን ሁሉ ከባሕርዩ አመንጭቶ ሊሠራ ይችላል፤ ሮም 2፥14። 2. የእግዚአብሔር ባሕርይ፤ በሐዋርያት የሃይማኖት ውሳኔ እንደተገለጠው ለእግዚአብሔር ባሕርይ ጥንት ምክንያት የለውም። ግን የማይታወቅ ባሕርዩ በፍጥረቱ ተገልጧል (ሮም 1፥20)፤ በባሕርይ ከእርሱ ጋር አንድ የሆነ አንድ ልጁ ኢየሱስ የባሕርዩ በጸጋና ምሳሌ ሆኖ ተገለጠ፤ ዕብ. 1፥3። ባሕርይ ክብር ተብሎ ይተረጐማል፤ 2ጴጥ. 1፥4። ከዚህም ሌላ ጠባይን፥ ግብርን ያሳያል። «መለኮት» ይመ.

**ባሪያ**፤ ነፃነትና መብት የሌለው፥ በራሱ ፈቃድ የፈለገውን ማድረግ የማይችል። በመጀመሪያ እግዚአብሔር አንዱን ለሌላው ባሪያ እንዲሆን አድርጎ አልፈጠረም። ቃሉ ለመጀመሪያ ጊዜ በሰካር ኃጢአት ከወደቀው ከኖኅ አንደበት ተገኘ፤ ዘፍ. 9፥26። በጥንት ዘመን በየአገሩ ባሪያዎች ነበሩ። የእስራኤል ሕዝብ በግብጽ አገር ባሪያዎች ሆነው ኖረዋል፤ ዘጸ. 20፥2። በእስራኤል ዘንድ ስለ ባሪያዎች ሕግ ነበረ። «ባርነት» ይመ.

ክርስቲያን ባሪያ ቢሆን ነፃነት ማግኘት ይገባዋል፤ 1ቆሮ. 7፥21። ባሪያ ጌታውን እንዲያከብር ጌታም ባሪያዎቹን በእውነትና በቅንነት እንዲያስተዳድር ታዝዘዋል፤ ኤፌ. 6፥5-9፤ ቆላ. 3፥22፤ 1ጴጥ. 2፥18። አንዳንድ ሰዎች ሐዋርያት ፦ «ጌቶች ባሮችን ነፃ አውጡ፤ ለባሪያዎች መብት ስጡ» ብለው ለምን እንዳላስተማሩ ይጠይቃሉ። መ.ቅ. ባርነት ብዙ ጉዳት እንደሚያመጣ ይገልጣል፤ ጌቶች ባሪያዎችን እንዳይጐዱ የሚከለከል በሙሴ ሕግ ብዙ ትእዛዝ አለ፤ በአ.ኪ.ም እንዳይገቱባቸው ተከልክለዋል፤ ኤፌ. 6፥9። በሰዎች መካከል መጥፎ እንደሆነ ይገልጣል፤ 1ጢሞ. 1፥9-11፤ ራእ. 18፥13። ነገር ግን ሐዋርያት እንደ ክርስቶስ ማናቸውንም ዓይነት አገዛዝ አይደግፉም፤ አይቃወሙም። ነገር ግን ሰዎች በሚገኙበት ሁኔታ በፍቅር እንዲኖሩ ያዝዛሉ። በክርስቶስ ጌታና ባሪያ ወንድሞች ይሆናሉና ወንጌል በዚህ መንገድ ባርነትን ያስቀራል፤ ዘጸ. 21፥5:6፤ ዮሐ. 15፥15፤ ገላ. 3፥28፤ ፊልሞና 15፥17።

በሌላ አስተሳሰብ እንአብርሃም የእግዚአብሔር ባሮች ተብለዋል። ይህም የእግዚአብሔር ፍጡርና ታዛዥ መሆንን ያመለክታል። እግዚአብሔርም አስፈላጊውን ሁሉ ለባሪያዎቹ ያደርጋል፤ ዘፍ. 26፥23:24፤ ዘኍ. 12፥7፤ ኢሳ. 20፥3፤ 37፥35፤ ሉቃ. 17፥7-10፤ ሮም 1፥1:2።

**ባርሰነት**፤ ቅጠሉ ጥሩ ሽታ ያለው ዛፍ። እንደ አደስ ከቅቤ ጋር ተለውሶ ይቀባል፤ ነህ. 8፥ 14:15፤ ኢሳ. 55፥13።

**ባርቅ**፤ መብረቅ ማለት ነው። ነቢይቱ ዲቦራ በእስራኤል ፈራጅ በነበረችበት ጊዜ በእርስዋ ትእዛዝ በእግዚአብሔር መሪነት ዐሥር ሺህ ሰዎችን አሰልፎ ሲሣራ ከተባለው የከነዓናውያን የሠራዊት አለቃ ጋር ተዋግቶ ያሸነፈ መሪ ነው። እግዚአብሔር የሲሣራን ሠራዊት ሰረገላዎች እንዳይሄዱ ከባድ ዝናብ በማውረድ አስደንግጦ ሁሉም በሰይፍ ስለት ከባርቅ ፊት እንዲወድቁ አደረገ፤ መሳ. 4፥1-24፤ 5፥19-22። በዕብራውያን መልእክት ፦ በጦርነት ኃይለኞች ሆኑ የባዕድ ጭፍሮችን አባረሩ ተብለው ከተጠቀሱት የእምነት ጀግኖች አንዱ ባርቅ ነው፤ ዕብ. 11፥32-34።

**ባርነት**፤ በብ.ኪ. ዘመን ባርነት የተለመደ ነበር። ሰው ወደ ባርነት ሊገባ የቻለው በልዩ ልዩ መንገድ ነው፤ ይኸውም በገንዘብ ሲገዛ (ዘሌ. 25፥44)፥ በጦርነት ጊዜ ሲማረክ (ዘኍ. 31፥7-9)፥ ዕዳ ሲኖርበት (ዘሌ. 25፥39)፥ በባርነት በመወለድ (ዘጸ. 21፥4)፥ በሌብነት (ዘጸ. 22፥2:3)፥ በገዛ ራሱ ፈቃድ፤ ዘጸ. 21፥5:6። የሙሴ ሕግ ስለ ባርነት አያሌ ትእዛዛትን ሰጥቷል። ከባርነት አርነት የሚወጣበትንም መንገድ ያመለክታል፤ ዘጸ. 20፥10፤ 21፥2-27፤ ዘሌ. 25፥25-55፤ ዘዳ. 15፥12-18። በአ.ኪ. ባርነት መኖሩ ተጠቅሷል። ለባሪያዎች ትእዛዝ ተሰጥቷል፤ ኤፌ. 6፥5-9፤ ገላ. 3፥28፤ ቆላ. 3፥22-25፤ 1ጢሞ. 6፥1። ክርስቶስ ኃጢአተኛ «የኃጢአት ባሪያ ነው» ብሎ አስተማረ፤ ዮሐ. 8፥34። ጳውሎስም በመልእክቶቹ ስለ ሕግ ባርነት (ገላ. 5፥1፤ ሮም 8፥15) እና ስለ ሞት ፍርሃት ባርነት ጽፏል፤ ዕብ. 2፥15። «ባሪያ» ይመ.

**ባሮክ**፤ ቡሩክ ማለት ነው። የኔርያ ልጅ፥ የነቢዩ ኤርምያስ ታማኝ ወዳጅና ጸሐፊ፤ ኤር. 32፥12። በይሁዳ ንጉሥ በኢዮአቄም ዘመነ መንግሥት እግዚአብሔር ለኤርምያስ የተናገረውን ቃል ሁሉ በመጽሐፍ ክርታስ ጽፎ በጾም ቀን በእግዚአብሔር ቤት ለተሰበሰበው ሕዝብ አነበበው፤ ለንጉሥ ኢዮአቄምም ተነበበ። ኢዮአቄም ግን የእግዚአብሔርን ቃል በመናቅ ክርታሱን በካራ ቈርጦ አቃጠለው። ባሮክም በኤርምያስ ትእዛዝ ሌላ ክርታስ ወስዶ ለሁለተኛ ጊዜ ቃሉን ጻፈ፤ ኤር. 36፥1-32።

ኤርምያስ በንጉሥ ሴዴቅያስ ዘመን በታሰረ ጊዜ፥ ባሮክ የንጉሡን ቍጣ ሳይፈራ ነቢዩን ይረዳው ነበር፤ ኤር. 32፥12-16። በመጨረሻም ነቢዩ ከጥቂቶቹ አይሁድ ጋር ወደ ግብጽ አገር እንዲጓዝ በተገደደ ጊዜ ባሮክ አብሮት ሄደ፤ ኤር. 43፥1-7።

**ባሮክ፥ መጽሐፈ ባሮክ**፤ ባሮክ በተማረከበት አገር በባቢሎን ሳለ ለኢየሩሳሌም ነዋሪዎች ጽፎ ላከላቸው የተባለው መጽሐፍ ነው። የኦርቶዶክስና የካቶሊክ አብ.ክ. ከብ.ኪ. መጻሕፍት ጋር ቈጥረው ይቀበሉታል። መጽሐፉ በኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤ.ክ. ባለ አምስት ምዕራፍ ብቻ ነው።

**ባሳን**፤ ከገሊላ ባሕር በስተምሥራቅ ከአርሞንዔም እስከ ገለዓድ ያለው የከብት መሰማሪያ ለም አገር፤ ዘኍ. 21፥33-35፤ ዘዳ. 32፥14።

**ባቢሎን**፤ ባቤል፤ የቃሉ መሠረታዊ ትርጕም የእግዚአብሔር በር ማለት ሲሆን፥ ሕዝቡ «ድብልቅልቅ» ብለው ይተረጕሙት ነበር። ናምሩድ የባቢሎን ገዥ ነበር፤ ዘፍ. 10፥10። በአብርሃም ዘመን ባቢሎን ታላቅ መንግሥት ሆነ፤ በኋላ ግን ደከመ፤ ከአሦር በታችም ሆነ። ከለዳውያን ከባቢሎን ሰዎች ጋር ተባብረው አሦርን አሸነፉ፤ ነነዌንም ያዙ። ከለዳዊው ናቡከደነፆር የባቢሎን ንጉሥ ሲሆን መንግሥቱ ከግብጽ እስከ ፋርስ መንግሥት ተስፋፋ። በናቡከደነፆር ጊዜ የባቢሎን ከተማ በብዙ ሕንፃ ያጌጠች፥ በትልቅ ቅጥር የተከበበች ምሽግ ነበረች፤ ዳን. 4፥30። እነዳንኤል የተማረኩት ወደዚያ ነበር፤ ዳን. 1። ነቢያት ስለ ባቢሎንና ስለ ውድቀቷ ትንቢት ተናገሩ፤ ኢሳ. 13፤ 14፤ 46፤ 47፤ ኤር. 50፤ 51። እንደታላቸውም በ539 ከክ. ል. የባቢሎን ንጉሥ ብልጣሶር ተገደለ፥ የፋርስ ንጉሥ ቂሮስም ባቢሎንን ያዘ፤ ዳን. 5፥30። በአ.ኪ. ባቢሎን እግዚአብሔርን ለሚቃወም ኀያል መንግሥት የምሳሌ ስም ሆኖ ተጠቅሷል (ራእ. 14፥8)፥ በ1ጴጥ. 5፥13 «ባቢሎን» ማለት ምናልባት ሮምን፥ ወይም በግብጽ የሚገኝ አንድን ከተማ ያመለክት ይሆናል። ካ. 1ሬ።

**የባቢሎን ግንብ**፤ ከጥፋት ውሃ በኋላ ሰዎች ስማቸውን ለማስጠራት ትልቅ ግንብ መሥራት ጀመሩ። እግዚአብሔርን ሳይፈሩ ይህን ስላደረጉ፥ እግዚአብሔር ቋንቋቸውን ደባለቀ። ከዚያም በምድር ላይ በተናቸው፤ ያም ቦታ «ባቢሎን» ተባለ፤ ዘፍ. 11፥1-9።

**ባኦስ**፤ ከ909-886 ከክ. ል. በእስራኤል የነገሠ ሦስተኛ ንጉሥ። የኢዮርብዓምን ዘር አጠፋ፤ ከይሁዳ ንጉሥ ከአሳ ጋር በተከታታይ ብዙ ጦርነት አደረገ። ከሞተ በኋላ ዘምሪ የባኦስን ቤት አጠፋ፤ 1ነገ. 15፥16-16፥13፤ 2ዜ.መ. 16፥1-6።

**ባዓል**፤ «በአል» ይመ.

**ባዘቶ**፤ በጣም የለሰለሰ ነጭ ጥጥ ወይም የበግ ጠጕር፤ መሳ. 6፥37፤ ኢሳ. 1፥18።

**ባዶ**፤ ምንም ነገር የሌለበት፤ ዘፍ. 31፥42። ወልድ ሰው ሲሆን ሰማያዊ ክብሩን ሳያሳይ በሰዎች መካከል ሲገኝ እንኳን ክብር ባለመፈለጉ ራሱን «ባዶ» አደረገ ተባለ፤ ዮሐ. 17፥5፤ ፊል. 2፥7።

**ባዶስ**፤ የውሃ፥ የወይን፥ የዘይት መስፈሪያ፤ 1ነገ. 7፥26፤ ኢሳ. 5፥10፤ 2ዜ.መ. 2፥10። «መስፈሪያ» ይመ.

**ቤል**፤ የባቢሎን ጣዖት ስም፤ ኢሳ. 46፥1። «በአል» ይመ.

**የቤል ታሪክ**፤ ፋርሳውያን ያመልኩት የነበረ ጣዖት በዳንኤል አስተዋይነት እንዴት እንደጠፋ የሚተርክ ነው። በትልቁ የአማርኛ መ.ቅ. በዳንኤል 13 ታትሟል።



በናቡክደነፆር ዘመን የነበረው ታላቁ የባቢሎን በር

**ቤልሆር፤** «ስይጣን» ይመ.

**ቤርሳቤህ፤** የንጉሥ ዳዊት ወታደር የኬጢያዊው የኦርዮ ሚስት። ግሪኮች ቤርሳቤህ እያሉ ይጠሩአት ነበር፤ በቀንታውያን አይሁድ አጠራር ግን ባትሺባ ትባላለች። ንጉሥ ዳዊት ከእርስዋ ጋር አመነዘረ፤ 2ሳሙ. 11። ኦርዮንን በጦር ሜዳ ካስገደለ በኋላ አግብቶአት ልጅ ወለደችለት፤ 2ሳሙ. 5፥14፤ 1ዜ.መ. 3፥5። የመጀመሪያው ልጅ ግን ሞተ። በኋላ ሌሎች አራት ልጆች ከእርስዋ ተወለዱ። ከእነርሱም አንዱ በእስራኤል ላይ የነገሠው ሰሎሞን ነው፤ ማቴ. 1፥6።

**ቤርሳቤህ፤** ከኬብሮን በስተደቡብ በኩል አርባ ኪ.ሜ. ርቆ የሚገኝ ከተማ። ለመጀመሪያ ጊዜ በአብርሃም ተሰየመ፤ ዘፍ. 21፥30:31። የይስሐቅም የውሃ ጉድጓድ ሳቢህ ከተባለ በኋላ ቤርሳቤህ ተብሏል፤ ዘፍ. 26፥33። ግን ሁሉም አንድ ቦታ ይመስላል። ቤርሳቤህ የእስራኤል ደቡብ ዋና ከተማ ስለነበረ፥ የእስራኤል ምድር ብዙ ጊዜ «ከዳን እስከ ቤርሳቤህ» እየተባለ ተጠቅሷል፤ መሳ. 20፥1፤ 2ዜ.መ. 30፥5። አብርሃም፥ ይስሐቅና ያዕቆብ በዚያ ተቀመጡ፤ ዘፍ. 22፥19፤ 26፥23፤ 46፥1። ኤልያስ በዚህ በኩል ወደ ደብረ ሲና ሄደ፤ 1ነገ. 19፥3። ይህ ቦታ ዛሬ ትልቅ ከተማ ነው። ካ. 3በ።

**ቤርዜሊ፤** ዳዊትን የረዳ ሀብታም የገለዓድ ሽማግሌ፤ 2ሳሙ. 17፥27-29፤ 19፥31-40።

**ቤርያ፤** በመቄዶንያ አገር የምትገኝ ከተማ። በሐዋርያው ጳውሎስ ሁለተኛ የስብከት ጉዞ ወቅት በቤርያ ቤ.ክ. ተመሠረተች፤ ሐ.ሥ. 17፥10-14፤ 20፥4። ካ. 6ሸ።

**ቤተ ልሔም፤** የእንጀራ ቤት ማለት ነው። ከኢየሩሳሌም ወደ ደቡብ 9 ኪ.ሜ. ርቆ የሚገኝ ከተማ። በያዕቆብ ዘመን ኤፍራታ ይባል ነበር። እዚህም የያዕቆብ ሚስት ራሔል ሞተች፤ ተቀበረችም፤ ዘፍ. 35፥16:19። በመሳፍንት ዘመን የኢብጻንና የቦዔዝ (መሳ. 12፥8-10፤ ሩት 2፥4)፥ የእሴይና የዳዊት ከተማ ነበር፤ 1ሳሙ. 17፥12-14፤ ሉቃ. 2፥4:5:11። ዳዊት በቤተ ልሔም ሳለ በነቢዩ ሳሙኤል ተቀባ፤ 1ሳሙ. 16፥13። በዛብሎን ቤተ ልሔም የተባለ መንደር ስለነበረ (ኢያሱ 19፥15)፥ አንዳንድ ጊዜ ይህ የዳዊት ከተማ የይሁዳ ቤተ ልሔም ይባል ነበር፤ ሩት 1፥1። ነቢዩ ሚክያስ መሲሑ ወይም ክርስቶስ በዚህ እንደሚወለድ ተነበየ፤ ሚክ. 5፥2። ካ. 5ሠ።

ክርስቶስ በዚህ ተወለደ፤ ማቴ. 2፥1:2፤ ሉቃ. 2፥4-7። እረኞቹ (ሉቃ. 2፥15-17)፥ በኋላም ሰብአ ሰገል በቤተ ልሔም ጐበኙት፤ ማቴ. 2፥1-12። ከዚያም በኋላ ንጉሡ ሄሮድስ ዕድሜአቸው እስከ ሁለት ዓመት የሆኑትን ሕፃናት ሁሉ በዚህ ቦታ አስፈጀ፤ ማቴ. 2፥16። ዛሬ በቤተ ልሔም ከ30 ሺህ የሚበልጥ ሰው ይኖራል።

**ቤተ መቅደስ**፤ በኢየሩሳሌም የተሠራ አይሁድ ለእግዚአብሔር የሚሰግዱበት ልዩ ቤት። ሰሎሞን አባቱ ዳዊት እንዳሰበ ቤተ መቅደስን ሠራ። ከሕዝቡ ኃጢአት የተነሣ ናቡከደነፆር ቤተ መቅደሱን አፈረሰው፤ 2ነገ. 25፥8-17። ከባቢሎን ምርኮ በኋላ በዘሩባቤል ዘመን እንደገና ተሠራ፤ በሄሮድስ ዘመን ታደሰ፤ ተስፋፍቶም ተሠራ። የሄሮድስ መቅደስ በተሠራበት ቦታ ዛሬ የእስላሞች መስጊድ ቆሟል። «ኢየሩሳሌም» ይመ.። ቤተ መቅደስ የተሠራበት ቦታ አብርሃም ይስሐቅን ለመሥዋዕት ያቀረበበትና ዳዊት የገዛው ነው፤ ዘፍ. 22፤ 2ዜ.መ. 3፥1።

1. የሰሎሞን ቤተ መቅደስ፤ እስራኤል በምድረ በዳ ሲጓዙ፥ ሃይማኖታዊ ሥርዓት ሁሉ በመካከላቸው ባለው በእግዚአብሔር ድንኳን ይፈጸም ነበር። ነገር ግን አገራቸው ሲገቡ ዳዊት ለእግዚአብሔር ድንኳን እንጂ ቤት ስለሌለው፥ ቤተ መቅደስ ለመሥራት ሲፈልግ እግዚአብሔር ከለከለው፤ 1ዜ.መ. 22፥8። ነገር ግን የሚያስፈልገውን ድንጋይና እንጨት፥ ወርቅና የከበረ ድንጋይ፥ ሌላውንም ሁሉ ሰብስቦ፥ ለልጁ ለሰሎሞን እንዲሠራው አደራ ሰጠው፤ 1ዜ.መ. 22፥3-5። ሰሎሞንም እንደ አባቱ ትእዛዝ ቤተ መቅደሱን እጅግ ውብ አድርጎ ሠራ። በመጨረሻም በምስጋና፥ በጸሎትና በመሥዋዕት በእስራኤል ጉባኤ ፊት ቤቱን ቀደሰ፤ 1ነገ. 8። በቤተ መቅደሱ ግራና ቀኝ ሁለት አዕማድ ቆመው ነበር፤ 2ዜ.መ. 3፥4:15።



ስለ ሰሎሞን ቤተ መቅደስ የአንድ ሠዓሊ አሳብ

ውስጡም ለሁለት ተከፍሏል። ውስጠኛው ክፍል ቅድስተ ቅዱሳን፥ ሌላውም መቅደስ ይባላል፤ 1ነገ. 8፥6:10።




1. ግምጃ ቤቶች
2. ታቦት
3. የወርቅ መሠዊያ
4. ገበታ
5. መቅረዞች
6. ወለል
7. ዐምዶች
8. ደረጃዎች
9. የናስ መሠዊያ
10. መታጠቢያ

የሰሎሞን ቤተ መቅደስ ንድፍ



ስለ ሄሮድስ ቤተ መቅደስና ስለ ሮም መንግሥት ግንብ የአንድ ሠዓሊ አሳብ

በውስጥ የነበሩ ዋና ዋና ዕቃዎች ፦ በቅድስተ ቅዱሳን ታቦት፥ በመቅደስም ከወርቅ የተሠሩ ዐሥር መቅረዞች፥ የወርቅ መሠዊያ፥ ኅብስት የነበረበት የወርቅ ገበታ ናቸው፤ 1ነገ. 7፥48:49። ከቤቱ ፊት ለፊት የካህናት መታጠቢያና የናስ መሠዊያ ነበሩ፤ 1ነገ. 7፥23-26:39፤ 8፥64። ደግሞም ለግምጃ ቤትና ለሹሞች መኖሪያ ክፍሎች ነበሩ። ከ300 ዓመት በኋላ የቤተ መቅደሱ መቃጠል ምን ያህል ከባድ እንደነበረ በዳንኤል ጸሎት ይታያል፤ ዳን. 9፥11-17።

2. ዘሩባቤል ቤተ መቅደስን እንደሠራ፤ የእስራኤል ሰዎች ተሸንፈው ወደ ባቢሎን ከተማረኩ ከሰባ ዓመት በኋላ ወደ ኢየሩሳሌም ተመለሱ፤ በዘሩባቤል መሪነት ቤተ መቅደሱን እንደገና ሠሩ፤ ዕዝ. 3-6።

3. ሄሮድስ ቤተ መቅደስን እንዳስፋፋ፤ 19 ከክ. በ. ሄሮድስ ቤተ መቅደስን እንደገና አስፋፍቶ አሠራው። ይህ ቤተ መቅደስ ለካህናት፥ ለአይሁድ ወንዶችና ሴቶች፥ ለአሕዛብም የሚሆኑ አራት አደባባዮች ነበሩት። ጌታችን ኢየሱስ እንደተነበየው በ70 ዓ.ም. ሮማውያን ኢየሩሳሌምን በሙሉ አፈረሱ፤ ማቴ. 24፥2፤ ሉቃ. 19፥41-44።

4. የቤተ መቅደስ ምሳሌነት፤ በሄሮድስ ቤተ መቅደስ አጥር ላይ አሕዛብ ወደ መቅደስ እንዳይገቡ የሞት ማስጠንቀቂያ በድንጋይ ቅርጽ ተጽፎ ነበር፤ ሐ.ሥ. 21፥27-29፤ ኤፌ. 2፥14:15።

በዮሐ. 2፥20-22 ክርስቶስ ሥጋውን በቤተ መቅደስ መስሎ ተናገረ። ጳውሎስ በ1ቆሮ 6፥19:20 የምእመናንን ሥጋ በቤተ መቅደስ መሰለ። በኤፌ. 2፥22 ላይም ምእመናን በአንድነት በቤተ መቅደስ ተመስለዋል። የእስራኤል ሕዝብ በባቢሎን ምርኮኞች ሆነው ሳሉ፥ ሕዝቅኤል ስለ አዲስ ቤተ መቅደስ በዝርዝር በጻፈላቸው ጊዜ ተጽናኑ፤ ነገር ግን ቤቱ



የሰሎሞን ደጅ መመላለሻ በሄሮድስ ቤተ መቅደስ




የሄሮድስ ቤተ መቅደስ ንድፍ

አልተሠራም፤ ሕዝ. ም. 40-43። አንዳንዶች ይህ መንፈሳዊ ምሳሌ እንጂ በድንጋይ የሚሠራ የመቅደስ ትንቢት አይደለም ብለው ሕዝቅኤልን ይተረጉማሉ። በዕብራውያን መልእክትና በዮሐንስ ራእይ የተጻፈው ስለ ሰማያዊ ቤተ መቅደስ ነው፤ ዕብ. 9፥12፤ ራእ. 11፥1:2:19። ከዚህም ጋር ጸሐፊዎች ለቤተ መቅደስ መንፈሳዊ ትርጉም የሰጡ ይመስላል። ቢሆንም ዮሐንስ በአዲሲቱ ኢየሩሳሌም ቤተ መቅደስ እንደሌለ ገልጦ ሲጽፍ፥ እግዚአብሔርና በጉ ቤተ መቅደስ መሆናቸውን ያስታውቃል፤ ራእ. 21፥22።

**ቤተ መዛግብት**፤ የአንድ ድርጅት ወይም የአንድ ቤተሰብ ንብረት የሚቀመጥበት ዕቃ ቤት፤ ነህ. 7፥70:71፤ ኢዮብ 38፥22።

**ቤተሰብ**፤ ያንድ ቤት ሰዎች፤ ባንድ ባለቤት ስም የሚተዳደሩ። ሰው ብቸኛ እንዲሆን የእግዚአብሔር ፈቃድ ባለመሆኑ በእስራኤል ዘንድ ማናቸውም ሰው በቤተሰብ ይኖር ነበር። ቤተ ሰብ ማለት በአንድ ቤት ውስጥ የሚኖሩትን ሁሉ ያጠቃልላል፤ ዘጸ. 12፥4። ሆኖም እንደ አብርሃም ቤተሰብ በአንድ «አባት» የሚመሩ ሁሉ አንድ ሺህ የሚያህሉ በአንድ ቤተሰብ ይገኛሉ፤ ዘፍ. 14፥14። ከእነርሱም መካከል አገልጋዮችና ዘመዶች ይቈጠራሉ። ምድራዊ አባትነት በአብ አባትነት የተመሠረተ ነውና አባት ለቤተሰቡ ኀላፊ ነው። ልጆችም ሊታዘዙለት ይገባቸዋል፤ ኤፌ. 3፥14፤ 6፥1-4። እግዚአብሔር በአንድ ሰው በኩል ብቻ ሳይሆን፥ በቤተሰብም በኩል የደኅንነትን መንገድ ለመግለጥ ለአብርሃምና ለዘሩ ቃል ኪዳንን፥ ለቤተ እስራኤል ሕግን፥ ለምእመናንና ለልጆቻቸው ወንጌልን ሰጠ፤ ዘፍ. 17፥9፤ ኤር. 31፥31፤ ሐ.ሥ. 2፥39፤ ኤፌ. 2፥19። ምንም እንኳን በቤተሰብ ውስጥ የሚኖሩ ሁሉ የእግዚአብሔር ወገኖች ባይሆኑም፥ እግዚአብሔር በቤተሰብ በኩል ፈቃዱን ይፈጽማል፤ ሮም 9፥6-13። «አባት»፥ «እናት»፥ «ወላጅ»፥ «ልጅ»፥ «በኵር» ይመ.

**ቤተ ሳይዳ**፤ የዓሣ አጥማጅ ቤት ማለት ነው።

1. ከገሊላ ባሕር በስተሰሜን የዮርዳኖስ ወንዝ ወደሚገባበት አቅራቢያ ያለ ከተማ፤ የጴጥሮስና የእንድርያስ የፊልጶስም አገር፤ ዮሐ. 1፥44-50፤ 12፥21። ክርስቶስ በቤተ ሳይዳ ዕይነ ስውሩን ፈወሰ፤ ማር. 8፥22-26። ነገር ግን ከተማው ትምህርቱን አልተቀበለም፤ ሉቃ. 10፥13።

2. ሄሮድስ ፊልጶስ ምናልባት ይህን ከተማ፥ ወይም ቤተ ሳይዳ የተባለ ሌላውን ከተማ እንደገና በስተምሥራቅ ሠራ፤ ክርስቶስ በዚህ ከተማ አቅራቢያ

ባለው በምድረ በዳ አምስት ሺህ ሰው መገበ፤ ሉቃ. 9፥10-17።

3. በኢየሩሳሌም ውስጥ ደግሞ ቤተ ሳይዳ የምትባል የበሽተኞች መጠመቂያ በታ ነበረች፤ ዮሐ. 5፥2። ግን ስምዋ ቤተ ሳይዳ ሳይሆን፥ ቤተ ሐሰዳ፥ ወይም ቤተ ዛታ የነበረ ይመስላል፤ ትርጉሙም «የምሕረት ቤት» ማለት ነው።

**ቤተ ክርስቲያን፤** «ቤተ ክርስቲያን» ተብሎ የተተረጐመው «አቅሌስያ» የሚለው የግሪክ ቃል ነው። «አቅሌስያ» ማኅበር ወይም ጉባኤ ተብሎ ሊተረጐም ይችላል፤ ሐ.ሥ. 7፥38። ቃሉ በመ.ቅ. ሰዎችን እንጂ ሕንፃን አያመለክትም። በአ.ኪ. ምእመናን በመጀመሪያ በሰው ቤት፥ በትምህርት ቤት፥ በወንዝ ዳር፥ በሚመቻቸውም በታ ለጸሎትና ለአምልኮ ይሰበሰቡ ነበር፤ ሐ.ሥ. 16፥13፤ 19፥9፤ ሮም 16፥5። በማኅበሩ የሚገኙት የክርስቶስ ተከታዮች ስለሆኑ ቤ.ክ. የቅዱሳን ማኅበር ናት፤ 1ቆሮ. 1፥2። ቃሉ አንዳንድ ጊዜ ተለይቶ በታወቀ በአንድ ስፍራ (1ቆሮ. 16፥19:20፤ ራእ. 2፥1)፥ በሌላ ጊዜ በጠቅላላ በየቦታው የሚገኙትን ቅዱሳን ያመለክታል፤ 1ቆሮ. 12፥28፤ ኤፌ. 5፥23-25። ከሁሉ በላይ መገንዘብ የሚገባን የቤ.ክ. መሥራች ክርስቶስ ራሱ መሆኑን ነው፤ ማቴ. 16፥16-18፤ 1ቆሮ. 3፥11።

ቤ.ክ. በአካል (1ቆሮ. 12፥12፤ ኤፌ. 1፥23)፥ በቤተ መቅደስ (ኤፌ. 2፥21)፥ በሚስት (ኤፌ. 5፥21-33)፥ በዐምድና መሠረት (1ጢሞ. 3፥15)፥ በኢየሩሳሌም ተመስላለች፤ ገላ. 4፥26፤ ዕብ. 12፥22፤ ራእ. 21፥2። ስለ ቤ.ክ. የተገለጡ ዋና ዋና ነገሮች የሚከተሉት ናቸው ፦

1. ከክርስቶስ ዕርገት በኋላ በመንፈስ ቅዱስ መውረድ ተቋቋመች፤ ኤፌ. 1፥20-23።

2. ከቤተ እስራኤል ተገኘች፤ ሐ.ሥ. 2፥14:36:41፤ ሮም 11፥13-24።

3. ቅድስት እንድትሆን በክርስቶስ ደም ተዋጀች ወይም ተገዛች፤ 1ቆሮ. 6፥19፤ ሐ.ሥ. 20፥28።

4. የእግዚአብሔር መኖሪያ ናት፤ ኤፌ. 2፥20-22።

5. አንዲት ናት፤ ኤፌ. 4፥4።

6. ኀይል እንዲኖራት ልዩ ልዩ ስጦታ ተሰጣት፤ ሮም 12፥3-8፤ 1ቆሮ. 12፥4-11።

7. አገባብና ሥርዓት እንዲኖራት ልዩ ልዩ መሪዎች ተሰጡአት፤ ኤፌ. 4፥11-13።

8. ወንጌልን ለሰዎች ሁሉ ለመስበክ ታዝዛለች፤ ማር. 16፥15።

9. ሰዎች የወንጌልን ቃል ሲያምኑ በጥምቀት ትቀበላቸዋለች፤ ማቴ. 28፥18:19።

10. ዋና የኅብረትዋ ምሥጢር ቅዱስ ቍርባን ነው፤ 1ቆሮ. 10፥14-17፤ 11፥23-26።

11. ለማሰር (ለማውገዝ) ለመፍታትም ሥልጣን አላት፤ ማቴ. 18፥15-20።

12. ተስፋዋ የክርስቶስ ዳግም ምጽአትና ትንሣኤ ሙታን ነው፤ 1ቆሮ. 11፥26፤ 15፥20-22።

**የቤተ ክርስቲያን አስተዳደር፤** አ.ኪ. ለቤ.ክ. አስተዳደር አንዳንድ መሠረታዊ መመሪያን እንጂ ረጅም የሆነውን የትእዛዛት ዝርዝር አይሰጥም። ክርስቶስ ሳያርግ ለሐዋርያት ኀላፊነትን ሰጠ። ሐዋርያት በአይሁድ መካከል ስላደጉ፥ የቤተ መቅደስንና የምኵራብን አስተዳደር ለምደው ነበር። ሆኖም የቤተ መቅደስን አስተዳደር ትተው የምኵራብን አስተዳደር የተከተሉ ይመስላል፤ «ካህናት»፥ «ሊቀ ካህናት»፥ «ቤተ መቅደስ»፥ «ምኵራብ» ይመ.። በመጀመሪያ ሐዋርያት ሁሉንም አገልግሎት ይፈጽሙ ነበር። በኋላም ደቀ መዛሙርት ሲበዙ ሰባት ሰዎች እንዲያገለግሉ በሕዝብ ተመረጡ፤ ሐዋርያትም እጃቸውን ጫኑባቸው፤ ሐ.ሥ. 6፥1-6። ሐዋርያት በየቦታው ቤ.ክ. ካቋቋሙ በኋላ ግን እንዲያስተዳድሩ ሽማግሌዎችን ሾሙላቸው። የቤ.ክ. አባሎች ሁሉ ስጦታና አገልግሎት አላቸው፤ 1ጴጥ. 4፥10። ስጦታና አገልግሎትም ብዙ ዓይነት ነው (ሮም 12፥3-8፤ 1ቆሮ. 12፥4-11)፥ ስለዚህ ሁሉም በአግባብና በሥርዓት እንዲፈጸም መሪዎች አስፈላጊ ናቸው፤ 1ቆሮ. 14።

የቤ.ክ. መሪዎች በ1ቆሮ. 12፥28 ላይ ተዘርዝረዋል። በዝርዝሩ ሐዋርያትና ነቢያት 1ኛና 2ኛ ሆነው የተጠቀሱት ሲሆኑ፥ እነርሱም የቤ.ክ. መሥራቾች ናቸው። ሦስተኛ አስተማሪዎች ናቸው። ቀጥሎም ልዩ ልዩ አገልጋዮች ተዘርዝረዋል። በተመሳሳይ ጥቅስ በኤፌ. 4፥11 ሰዎችን እሳምነው ወደ ቤ.ክ. የሚያስገቡ የወንጌል ሰባኪዎች ተጠቅሰዋል። በዚህም ዝርዝር አስተማሪዎች ጠባቂዎች እንደሆኑ ግልጥ ነው። እነዚህ መሪዎች ምእመናን ሁሉ አገልግሎታቸውን እንዲፈጽሙ እንጂ ራሳቸው ሁሉን እንዲያደርጉ አልተሾሙም፤ ኤፌ. 4፥11-16።

መሪዎች ብዙ ጊዜ ሽማግሌዎችና ጳጳሳት፥ ረዳቶችም ዲያቆናት ይባላሉ (በየአርእስቱ ይመ.)። አስተዳዳሪዎች የክርስቶስን አርአያ ተከትለው በግዴታ ሳይሆን በውዴታ፥ በኵራት ሳይሆን በትሕትና፥ እንደ ገዥ ሳይሆን እንደ አገልጋይ፥ ለገንዘብም ሳይሆን ለክርስቶስ ፍቅር መሥራት አለባቸው፤ ማር. 10፥42-45፤ 1ጴጥ. 5፥1-4። ምእመናን የሚያስተዳድሩአቸውን ሊወዱአቸው፥ ሊታዘዙአቸው፥ ሊደግፉአቸውም ታዝዘዋል፤ 1ተሰ. 5፥12፤ 1ጢሞ. 5፥17፤ ዕብ. 13፥7:17። እያንዳንድዋ ቤ.ክ. ራስዋን የቻለች ናት ቢባልም ሁሉም የሐዋርያትን መሪነት ተቀብለዋል፤ 1ቆሮ. 14፥33፤ 16፥1። መለያየትም በቤ.ክ. ሲገኝ በኢየሩሳሌም ጉባኤ ተደርጎ ውሳኔው ለአብ.ክ. ተላለፈ፤ ሐ.ሥ. 15፥23-29።

ከሐዋርያት በኋላ አንድ ዓይነት አስተዳደርና አመራር ነበረ ማለት ያስቸግራል። የቤ.ክ. ምሥጢራት በማን እንደሚፈጸሙ፥ መሪዎች እንዴት

እንደሚመረጡና እንደሚሾሙ፥ ሰዎች በማን ሥልጣን እንደሚወገዙ ሌላም ... እያንዳንድዋ ቤ.ክ. ለራስዋ ደምብና ሥርዓት አውጥታለች።

ዋና ዋና መሠረታውያን የቤ.ክ. አስተዳደር ነገሮች ተገልጠዋል፤ እነርሱም የሚከተሉት ናቸው ፦

1. ሥልጣን ሁሉ ከክርስቶስ ነው፤ 1ጴጥ. 5፥4።

2. የክርስቶስ ትሕትና ለአገልጋዮች ሁሉ መመሪያ ነው፤ ማቴ. 20፥26-28።

3. አስተዳደር በአንድ ሰው ብቻ ሳይሆን ከተሾሙት ሁሉ ጋር በአንድነት የሚከናወን ነው፤ ማቴ. 23፥8፤ 28፥19፤ ሐ.ሥ. 14፥23፤ 15፥6:23።

4. ማስተዳደርና ማስተማር የተያያዙ ናቸው፤ 1ተሰ. 5፥12፤ 1ጢሞ. 3፥2-7።

5. የቤ.ክ. ትምህርት ከሐዋርያት ስብከት የሚወጣ አይደለም፤ ገላ. 1፥8:9፤ ይሁዳ 3።

6. የእግዚአብሔርን ቃል ለሚያስተምሩና ጸሎትን ለሚመሩ ረዳቶች ያስፈልጉአቸዋል፤ ሐ.ሥ. 6፥2:3።

7. ቤተ ክርስቲያንን ለማስተዳደር ብቁነት ያላቸው እንዲሾሙ ያስፈልጋል፤ ቲቶ 1፥5-9።

8. ቤ.ክ. በእግዚአብሔር ቃል መሠረት የመጨረሻ ዳኝነት የመስጠት ሥልጣን አላት፤ ማቴ. 16፥16-20፤ 18፥15-20፤ 1ቆሮ. 5፥3-5፤ 6፥3-7።

**ቤተ ፋጌ**፤ ከኢየሩሳሌም ሁለት ኪ.ሜ. ርቆ በደብረ ዘይት ተራራ ላይ ያለ መንደር። ኢየሱስ ከቤተ ፋጌ በአህያ ላይ ተቀምጦ በሕዝቡ እልልታ ታጅቦ ወደ ቤተ መቅደስ ገባ፤ ሉቃ. 19፥28-40።

**ቤቴል**፤ የእግዚአብሔር ቤት ማለት ነው። ከኢየሩሳሌም በስተ ሰሜን የነበረ ከተማ። ከኢየሩሳሌም ርቀቱ 18 ኪ.ሜ. ነው። ይህ ከተማ ከኢየሩሳሌም በስተቀር ከሌሎች ከተሞች የበለጠ ብዙ ጊዜ በመ.ቅ. ተጠቅሷል። አብርሃም በዚህ ቦታ መሠዊያ ሠራ፤ ዘፍ. 12፥8። በኋላም ስለ ዘሩና ስለ መሬቱ ከእግዚአብሔር ተስፋ ተቀበለ፤ ዘፍ. 13፥3:14። ያዕቆብ በዚህ ቦታ መሰላል በሕልም አየ፤ ተስፋም ተቀበለ፤ ዘፍ. 28፥10-22፤ 35፥7። ታቦቱ በመሳፍንት ዘመን መጀመሪያ በቤቴል ነበረ፤ መሳ. 20፥26-28።

በነገሥታት ዘመን የሰሜናዊው የእስራኤል መንግሥት ዋና የአምልኮ ስፍራ በኢየሩሳሌም በመሆን ፈንታ በቤቴል ሆነ፤ 1ነገ. 12፥26-13፥34። የሰሜን ነገሥታት በዚህ ቦታ ጣዖትን ስለሠሩ ነቢዩ አሞጽ ወቀሳቸው፤ አሞጽ 3፥14፤ 7፥10-17። በዚህ ምክንያት ሆሴዕ ስሙን ቤትአዌን (የኃጢአት ቤት) ብሎ ጠራው፤ ሆሴዕ 4፥15። የእውነተኞች ነቢያት ትምህርት ቤት ደግሞ በቤቴል ነበረ፤ 2ነገ. 2፥2:3። ከአሦር ምርኮ በኋላ ሳምራውያን ስለ እስራኤል አምላክ በዚህ ተማሩ፤ 2ነገ. 17፥24-28። የይሁዳ ንጉሥ ኢዮስያስ በቤቴል የነበረውን የጣዖቱን መስገጃ አፈረሰ፤ 2ነገ. 23፥15-20። ዛሬ ከተማው የለም፤ ቦታው ግን ቤይቲን ተባለ። ካ. 3ሰ።

**ቤት**፤ ለሰው ብዙ ዓይነት መኖሪያ አለው፤ አብርሃም በድንኳን ኖረ። እንደ ሉጥም በዋሻ የሚኖሩ ሰዎች ነበሩ። ግን ብዙ ሰዎች በተመሸገ ከተማ ውስጥ ቤት ይሠሩ ነበር። በእስራኤል አገር ልዩ ልዩ የቤት አሠራር ነበር። ብዙ ጊዜ ቤቶችን በሁለት ደረጃ ይሠራሉ። ምድር ቤቱን በድንጋይ፥ ደርቡን ደግሞ በጡብ ይሠሩ ነበር። ጣራው በማዕዘን እንጨት ይደገፋል። በዚያ ላይ በቅርንጫፍ ይረበረባል።



በአብርሃም ዘመን በዑር የነበረ ፎቅ ቤት

ከርብራቡ በላይ ከሸንበቆ የተሠራ ሳጠራ ያነጥፉበታል፤ ከዚያም በላይ በብዙ ጭቃ ይደመድሙታል። በታችኛው ደረጃ ጉተራ፥ የውሃ ዕቃ፥ ሌላም መሣሪያ ያስቀምጣሉ። ከብቶቻቸውንም ያሳድሩበታል። በሁለተኛው ደረጃ (በፎቅ) ግን ሰዎች ይኖራሉ። እንግዶችንም ይቀበሉበታል። አየሩ ሲመች ደግሞ በጣራው ላይ ያድሩ ነበር። ሰው እንዳይወድቅ በጣራው ዙሪያ መከታ ያደርጉበታል፤ ዘዳ. 22፥8፤ ኢያሱ 2፥6። የጣራው መውጫ ከቤት በስተ ውጭ ነበረ። የታላላቅ ሰዎች ቤት ብዙ ክፍል የሚኖረው ሲሆን በአደባባይ ዙሪያ ይሠራ ነበር። ሀብታሞቹ ቤታቸውን በወርቅ፥ በብር፥ በተቀረፀ ድንጋይና እንጨት በዝሆን ጥርስም ያስጌጡ ነበር። መስኮቶች ከመሬት ከፍ ያሉና ጠባብ ሆነው ይሠሩ ነበር። «መስኮት» ይመ.



መደብ (ወለል) መሰል ጣራ ያለው ቤት

**ቤት ሳሚስ፤** «የፀሐይ ቤት» ማለት ነው። ከኢየሩሳሌም በስተምዕራብ ሀያ ኪ.ሜ. ርቆ የሚገኝ በታ። የእግዚአብሔር ታቦት ከፍልስጥኤም ወደ ቤት ሳሚስ ተመለሰ፤ 1ሳሙ. 6፥12-21። የእስራኤል ንጉሥ ዮአስ የይሁዳን ንጉሥ አሜስያስን እዚህ ቦታ ላይ ያዘው፤ 2ነገ. 14፥11-13። ሁለት ሌላ ቤት ሳሚስ የተባሉ ሰፈራዎች በስተሰሜን ነበሩ፤ ኢያሱ 19፥22:37:38።

**ቤትሳን፤** ከገሊላ ባሕር በስተደቡብ በኩል በዮርዳኖስ ወንዝ አቅራቢያ የነበረ የተመሸገ ከተማ። ከገሊላ ባሕር 20 ኪ.ሜ. ይርቃል። ፍልስጥኤማውያን የንጉሥ ሳኦልን ሬሳ በቤትሳን ቅጥር ላይ አንጠለጠሉት፤ 1ሳሙ. 31፥8-10።

**ቤዛ፤** የተያዘን ወይም የተወሰደን ነገር ለማስመለስ የሚከፈል ዋጋ፥ ካሣ፥ ለውጥ። ገንዘብ የሕይወት ቤዛ ነው፤ ምሳ. 13፥8። የእስራኤል ሕዝብ መሬታቸውን ወይም ቤታቸውን ከሸጡ በኋላ ለመቤዠት ይችሉ ነበር፤ ዘሌ. 25፥24-34። ኢየሱስ ለሚያምኑበት ሁሉ በሞቱ ቤዛ ሆነላቸው፤ ማር. 10፥45፤ ኤፌ. 1፥7፤ 1ጢሞ. 2፥5:6፤ ዕብ. 9፥12። ለሰው የተደረገለት ቤዛነት የሚፈጸመው ከሙታን ትንሣኤ በኋላ ነው፤ ሮም 8፥23፤ ኤፌ. 4፥30። «ዋጀ» ይመ.

**ብሉይ ኪዳን፤** እግዚአብሔር ለእስራኤል ሕዝብ በሙሴ አማካይነት የሰጣቸው ቃል ኪዳን፤ ዘጸ. 20፥1-17፤ 34፥28፤ ዘዳ. 4፥13። ሕዝቡ እግዚአብሔር የተናገራቸውን ቃሎች ሁሉ እናደርጋለን ሲሉ ሙሴ መሥዋዕትን ሠውቶ ደሙን በሕዝቡ ላይ በመርጨት ቃል ኪዳኑን አጸና፤ ዘጸ. 24፥1-8። ቃል ኪዳኑም እንዲፈጸም ትእዛዝ፥ ሥርዓትና ፍርድ ተሰጡ፤ ዘዳ. 5፥31። ከሙሴ ዘመን በፊት ግዝረት ለአብርሃምና ለዘሩ በቃል ኪዳን እንደ ምልክት ተሰጥቶ ነበር (ዘፍ. 17፥11)፥ ከሙሴ በኋላም በተጨማሪ የቃል ኪዳኑ ምልክት ሰባተኛው ቀን ሆነ፤ ዘጸ. 31፥13:16። ይህም ቃል ኪዳን ከመጀመሪያ ጀምሮ ጊዜያዊ መሆኑ ታወቀ (ዘዳ. 18፥15፤ ኤር. 31፥31)፥ አዲስ ኪዳንም ስለገባ ብሉይ ኪዳን «አሮጌና ውራጅ» ተባለ፤ ዕብ. 8፤ 2ቆሮ. 3። «ቃል ኪዳን» ይመ.

**የብሉይ ኪዳን መጻሕፍት፤** ከክርስቶስ በፊት የተጻፉ እስራኤል የተቀበሉአቸው፥ በክርስቶስም የጸደቁ ቅዱሳት መጻሕፍት በአንድነት ሲገኙ፥ «ብሉይ ኪዳን» ይባላሉ፤ 2ቆሮ. 3፥14። የክርስቶስ መምጣት ብ.ኪ. የሰጠውን ተስፋ ፈጽሞ የተሻለውን አዲስ ኪዳን አቋቋመ፤ ዕብ. 8፥6-7። ይሁን እንጂ በዚህ ዘመን የሚገኝ ምእመን በብ.ኪ. የተመለከተውን ብዙ ጠቃሚ አሳብ መማር አለበት፤ ሉቃ. 24፥44:47፤ ሮም 15፥4፤ 1ቆሮ. 10፥11።

ኢየሱስ ክርስቶስ ራሱ «ሙሴ፥ ነቢያት»፥ በሌላ ጊዜም «የሙሴ ሕግ፥ ነቢያትና መዝሙራት» በማለት የብ.ኪ.ን ክፍሎች በትምህርቱ ጠቅሷል፤ ሉቃ. 24፥27:44።

ሀ. «የሙሴ ሕግ» 5ቱን የኦሪት መጻሕፍት የሚያመለክት ሲሆን፥ እነርሱም «መጀመሪያ»፥ «አባቶች» እና «ሕዝብ» በመባል የተጠቀሱትን ዘመኖች ያጠቃልላሉ፤ ንድፉንና «የኦሪት ጸሓፊ» ይመ.

ለ. «ነቢያት» 17ቱን የነቢያት መጻሕፍት፥ ደግሞም የነቢያት ንግግር ስለሚያተኩርባቸው ስለ «አገር»፥ «ነገሥታት»፥ «መከፋፈል»፥ «ምርኮ» እና «ከምርኮ መመለስ» የሚተርኩ 12 መጻሕፍትን

| ዘመን | ዋና ዋና ድርጊቶች | ዓመት ከክርስቶስ ልደት በፊት | ታላላቅ ሰዎች | የአምልኮና የሃይማኖት ሁኔታዎች |
|---|---|---|---|---|
| መጀመሪያ | ፍጥረት<br>በኃጢአት መውደቅ<br>የጥፋት ውሃ<br>የባቢሎን ግንብ | 10000 (5500?)<br>5000(?)<br>3500(?) | አዳም<br>ኖኅ | በገነት የነበሩ ሁለቱ ዛፎች<br>ቀስተ ደመና |
| አባቶች | ከዑር ወደ ከነዓን<br>ከከነዓን ወደ ግብጽ | 1900(?) (2085?)<br>1710(?) (1870?) | አብርሃም<br>ይስሐቅ<br>ያዕቆብ<br>ዮሴፍና ወንድሞቹ | ተስፋ ስለ ምድርና ስለ ዘር<br>ቃል ኪዳን - ግዝረት |
| ሕዝብ | ፋሲካ ÷ ከግብጽ መውጣት | 1280(?) (1445?) | ሙሴ | በሥርቱ ቃላት<br>ሕግ ÷ ታቦት<br>መገናኛ ድንኳን |
| አገር | ወደ ከነዓን መግባትና<br>አገሩን መያዝ | 1240(?) (1400?) | ኢያሱ<br>መሳፍንትና ሩት<br>ሳሙኤል | ሲታዘዙ በረከት<br>ሲያጠፉ ቅጣት<br>ታቦት በቤቴል |
| ነገሥታት | ኢየሩሳሌም<br>መናገሻ ከተማ ሆነች | 1051(?) - 1011<br>1011 - 971<br>971 - 931 | ሳኦል<br>ዳዊት<br>ሰሎሞን | መዝሙራት<br>ታቦት ወደ ቤተ መቅደስ መግባት |
| መከፋፈል | 1. እስራኤል<br>መናገሻ<br>ሰማርያ<br>ወደ አሦር መሰደድ | 931-722<br>722 | ኢዮርብዓም<br>አክዓብ<br>ኤልያስ ÷ ኤልሳዕ<br>ሆሴዕ ÷ አሞጽ<br>ሰናክሬም | የወርቅ ጥጃዎች<br>በቤቴልና በዳን<br>የበዓል ጣዖታት |
| | 2. ይሁዳ<br>መናገሻ<br>ኢየሩሳሌም<br>ወደ ባቢሎን<br>መሰደድ | 931 - 587<br>(ሀ) 605 (ለ) 597<br>(ሐ) 587 | ሮብዓም<br>ሕዝቅያስ ÷ ኢሳይያስ<br>ኢዮስያስ ÷ ኤርምያስ<br>ናቡከደነፆር | ባዕድ አምልኮትና<br>ኃጢአት እየበዛ ሄደ<br>ቤተ መቅደስ ፈረሰ |
| ምርኮ | በባቢሎን በስደት መኖር | 607 - 538 | ሕዝቅኤል ÷ ዳንኤል | በምኩራብ መሰብሰብ ተጀመረ |
| ከምርኮ መመለስ | የፋርስ መንግሥት ወደ ኢየሩሳሌም መመለስ | 539 - 330 | አስቴር (480 ?)<br>ዘሩባቤል<br>ሐጌ ዘካርያስ (520)<br>ዕዝራ (458)<br>ነህምያ (445)<br>ሚልክያስ (400?) | ቤተ መቅደስ ተሠራ<br>ትምህርትና ሥነ ሥርዓት ተጠበቀ |
| | የግሪክ መንግሥት<br>የሮም መንግሥት | 330 - 63<br>63 | አንጥያኮስ÷መቃብያን<br>ሄሮድስ (40) | ፈሪሳውያን<br>ሰዱቃውያን<br>ቤተ መቅደስ ታደሰ |

ያጠቃልላሉ። ነቢያት ወይም የነቢያት ደቀ መዛሙርት በየዘመናቸው መልእክታቸውን ጽፈዋል። ከመጽሐፈ ኢያሱ እስከ መጽሐፈ አስቴር ያሉ መጻሕፍት ብዙ ጊዜ በእነማን እንደተጻፉ ባይገለጥም፥ በታላላቅ ሰዎች ማለትም፥ በሳሙኤል፥ በኢሳይያስ፥ በዕዝራና በሌሎች የተጻፉ መሆናቸውን ከአይሁድ ትውፊት መረዳት ይቻላል። ንድፉንና አርእስቱን ይመ.

ሐ. «መዝሙራት» መዝሙረ ዳዊት ብቻ ሳይሆን፥ ከመጽሐፈ ኢዮብ እስከ «መኃልየ መኃልይ ዘሰሎሞን» 5ቱ የጥበብ ወይም የግጥም መጻሕፍት ከንጉሥ ዳዊትና ከሰሎሞን ዘመን የተገኙ ናቸው። በየአርእስቱና «የቅዱሳት መጻሕፍት ዝርዝር» ይመ.

«አሮጌና ውራጅ» የሚለው፥ «አሮጌና እያለቀ ያለ» ሲል መገረዝን ... መዘተ የመሳሰሉ የተሻሩ የሙሴ ሕጎችን እንጂ የብ.ኪ. መጻሕፍትን የሚመለከት አይደለም፤ ማቴ. 5፥17፤ ዕብ. 8፥13። «ዐሠርቱ ቃላት» ይመ.

**የብሉይ ኪዳን ስፍረ ዘመን፤** ከዘጠኝ መቶ ዓመት ከክርስቶስ ልደት በፊት የሆኑትን የድርጊቶች ዓመት በትክክል ለመወሰን እንችልም፤ «ዓመት» ይመ.። ለምሳሌ የእስራኤል ሕዝብ ከግብጽ አገር የወጡበት ዐመቱ አንዳንዶች 1445 ሌሎች 1280 ከክ.በ. መሆኑን ይገምታሉ። አብርሃም ከ2ሺህ-1850 ገደማ ከክ.በ. እንደኖረ ይታሰባል። ከአብርሃም በፊት የኖሩት ሰዎች ምን ያህል ጊዜ እንደኖሩ አይታወቅም። አቈጣጠሩ የተለያየ በመሆኑ አንዳንድ ሊቃውንት ከአዳም እስከ ክርስቶስ ድረስ አምስት ሺህ አምስት መቶ ዓመት ይሆናል ይላሉ። ሌሎች ደግሞ ዐሥር ሺህ ዓመታት ያህል ይሆናል ይላሉ። ከአዳም ጀምሮ የብ.ኪ. ታሪክ አከፋፈል ልዩ ልዩ ይሆናል፤ እኛም ስምንት ክፍለ ዘመን አድርገነዋል። በሰንጠረዡ ከአዳም ጀምሮ የነበሩ ዋና ዋና ሰዎች፥ አምልኮና ድርጊቶች በቅደም ተከተል ተገልጠዋል። በዘመኑ አቈጣጠር ላይ ጥርጣሬ ስላለ ካጠገቡ የጥያቄ ምልክት ተጨምሯል።

**ብሌን፤** ብርሃንን የሚቀበል ጥቁሩ የዐይን ክፍል። ሰው ከፍ ባለ ጥንቃቄ ስለሚጠብቀው በምሳሌነት እግዚአብሔር ለሚጠብቃቸው ሁሉና ለሌላም ይነገራል፤ ዘዳ. 32፥10፤ መዝ. 17፥8፤ ምሳ. 7፥2፤ ዘካ. 2፥8።

**ብል፤** ተፈጥሮው እንደ ቢራቢሮ ያለ፥ ልብስንና ቆዳን የሚበላ ትል፤ ኢዮብ 13፥28፤ ኢሳ. 51፥8፤ ማቴ. 6፥19፤ ያዕ. 5፥2።

**ብልት፤** ማናቸውም የአካል ክፍል። «ክፍል» ይመ.

**ብልጣሶር፤** ትርጉሙ ቤል (የባቢሎን ጣዖት) ንጉሥን ይጠብቀው ማለት ነው፤ ኢሳ. 46፥1።

1. የናቡከደነፆር የልጅ ልጅ፥ የናቦኒዶስ ልጅ። የአዲሲቱ ባቢሎን መንግሥት የመጨረሻ ንጉሥ።

በመጠጥ ግብዣ ጊዜ በቤቱ ግንብ ላይ ጽሕፈት የምትጽፍ እጅ ታየችው። ጽሕፈቱም ፦ «ማኔ ቴቄል ፋሬስ» የሚል ነበረ። ንጉሡም ደንግጦ ትርጉሙን ሲፈልግ ዳንኤል እንዲህ ብሎ ተረጐመለት ፦ «እግዚአብሔር መንግሥትህን ቈጠረው፤ ፈጸመው፤ በሚዛን ተመዘንህ፥ ቀልለህም ተገኘህ፤ መንግሥትህም ተከፈለ፥ ለሜዶንና ለፋርስ ሰዎችም ተሰጠ»፤ ዳን. 5፥25-28። በዚያ ሌሊት የባቢሎን መንግሥት በፋርስ እጅ ወደቀ። ይህም የሆነው 539 ከክ. በ. ነው፤ ዳን. 5፥1-30፤ 8፥1።

2. ለዳንኤል የተሰጠ ስም፤ ዳን. 1፥7።

**ብሖር፤** ከፍየል ወገን የሆነ የዱር እንስሳ፤ መዝ. 18፥33።

**ብር፤** ከሌሎች ማዕድናት በውድነቱ በሁለተኛ ደረጃ የሚቈጠር። ወርቅ አብዛኛውን ጊዜ ለከበረ ዕቃ ሲሆን፥ ብር ከጥንት ጀምሮ የተለመደ ገንዘብ ነው፤ ዘፍ. 23፥16፤ ኤር. 32፥9። ኢየሱስ ክርስቶስ ለሠላሳ ብር ተሸጠ፤ ማቴ. 26፥15። ብር ደግሞ ለጌጥና ለዕቃ ይጠቅም ነበር፤ ዘፍ. 44፥2፤ ዘጸ. 12፥35።

**ብርሃን፤** እግዚአብሔር ብርሃን ነው (1ዮሐ. 1፥5፤ 1ጢሞ. 6፥16)፤ ብርሃንን ፈጠረ፤ ዘፍ. 1፥3። ኢየሱስ የዓለም ብርሃን ነው፤ ዮሐ. 1፥4-9፤ 9፥5። እግዚአብሔር በሰው ልብ ብርሃንን ያበራል (2ቆሮ. 4፥6፤ ኤፌ. 5፥14)፤ ምእመናን የዓለም ብርሃን ይሆናሉ (ማቴ. 5፥14-16)፤ ብርሃንም የሚሆኑት በተለይ የእግዚአብሔርን ቃል በመፈጸምና በማሳወቅ ነው፤ ፊል. 2፥15:16። የእግዚአብሔር ሕግ ብርሃን ነው፤ መዝ. 119፥105። «ጨለማ» ይመ.

**ብርኩማ፤** የእግር መዘርጊያና መቀመጫ፤ 2ዜ.መ. 9፥18።

**ብርጉድ፤** እንደ ዕጣን ያለ፥ ከአንድ ዓይነት እንጨት የሚገኝ ጥቁር ሙጫ። ሲያጤሱት ሽታው ደስ ያሰኛል፤ ዘጸ. 30፥24፤ ሕዝ. 27፥19።

**ብርጭቆ፤** ግብፃውያን ከሁለት ሺህ አምስት መቶ ዓመታት ከክ. በ. ብርጭቆን ከአሸዋ ይሠሩ ነበር። በተለይ ለጌጥ ይጠቀሙበት ነበር፤ ኢዮብ 28፥17፤ ራእ. 21፥18:21።

**ብቃት፥ በቃ፤** የደስታ (ዘፍ. 45፥28)፥ የምግብ (ምሳ. 25፥16)፥ የክፋት (ማቴ. 6፥34)፥ የቅጣትም መጠን አለው፤ 2ቆሮ. 2፥6። በእግዚአብሔር ፊትና በክርስቲያናዊ ሕይወት ብቃት የሚገኘው ከእግዚአብሔር ጸጋ እንጂ ከሰው አይደለም፤ 2ቆሮ. 2፥16-17፤ 3፥5፤ 12፥9።

**ብብት፤** የደረትና የክንድ መካከል መታቀፊያው አካል፤ ኢሳ. 40፥11። ቃሉ ጥልቅ ስሜትን ሊያመለክት ይችላል፤ መዝ. 35፥13፤ መክ. 7፥9።

**ብንያም**፤ የስሙ ትርጉም፥ የቀኝ እጅ ልጅ ማለት ነው፤ ወይም የደቡብ ልጅ ተብሉ ሊተረጐም ይችል ይሆናል። የያዕቆብ የመጨረሻ ልጅ። እናቱ ራሔል ተጨንቃ ሕፃኑን ከወለደች በኋላ ልትሞት ስትል ቤንኦኒ ብላ ጠራችው፤ ትርጉሙም የጭንቀቴ ልጅ ማለት ነው። አባቱ ያዕቆብ ግን ስሙን ብንያም ብሉ ለወጠው፤ ዘፍ. 35፥16-20። ብንያም ከእስራኤል ነገዶች አንዱ፥ ይኸውም የነገደ ብንያም አባት ሆነ (ዘፍ. 46፥21)፥ ያዕቆብ ነጣቂ ተኵላ አለው፤ ዘፍ. 49፥27። የከነዓን ምድር በዐሥራ ሁለቱ ነገዶች መካከል በተከፈለች ጊዜ የብንያም አገር በስተሰሜን በኤፍሬም በስተደቡብም በይሁዳ አገር የሚዋሰን ሆነ፤ ኢያሱ 18፥11-20። ካ. 3ሰ። በኋላም በጣም የሚያስጸይፍ ኃጢአት ስለሠሩ ተቀጡ፤ መሳ. 19-21። ከዚህ ወገን ንጉሥ ሳኦልና ሐዋርያው ጳውሎስ ተገኙ፤ 1ሳሙ. 9፥1:2፤ ፊል. 3፥5። «ነገድ» ይመ.

**ብኤር ለሃይሮኢ**፤ ትርጉሙ ሕያው የሆነውን፥ የሚያየኝንም ያየሁበት የውሃ ጕድጓድ ማለት ነው። በዚህ የውሃ ጕድጓድ አጠገብ የእግዚአብሔር መልአክ ለሣራ ገረድ ለአጋር ተገልጦ ለአብርሃም ስለምትወልደው ልጅ ስለ እስማኤል ነገራት፤ ዘፍ. 16፥7-14።

**ብኵርና**፤ «በኵር» ይመ.

**ብዔልዜቡል (ብዔልዜቡብ)**፤ የዝንብ ጌታ ማለት ነው። በአቃሮን የሚኖሩ ፍልስጥኤማውያን ያመልኩት የነበረ የጣዖት ስም፤ 2ነገ. 1፥2-6። ይህ በኣል የዝንብ ጌታ መባሉ በፍልስጥኤማውያን እምነት ዝንብ የሚፈጥር ስለሆነ ነው። እንደ እምነታቸውም የዝንብ ጌታ በመሆኑ በዝንብ አማካይነት በሕዝብ ላይ በሽታን ሊያመጣ፥ ወይም ደግሞ ዝንብን ከአገር በማጥፋት በሽታን ሊያስወግድ ይችላል። በአ.ኪ. ግን ብዔል ዜቡል ሰይጣን ወይም የአጋንንት አለቃ የሚጠራበት ስም ነው፤ ማቴ. 12፥24፤ ሉቃ. 11፥15።

**ብዙ፥ ብዙዎች**፤ ጥቂቶች ያይደሉ። «ብዙዎች» ክርስቶስ የሞተላቸውን ሰዎች ሊያመለክት ይችላል፤ ኢሳ. 53፥11፤ ማር. 10፥45፤ ሮም 5፥15:16:19፤ ዕብ. 9፥28።

**ብድራት**፤ በክፋት ወይም በመልካም ሥራ ሳቢያ የሚመለስ ዋጋ። ገንዘብ ያበደረ እንደሚቀበል ክፉ ወይም መልካም የሠራም ብድራትን በፈንታው ይቀበላል፤ መዝ. 91፥8፤ ኢሳ. 34፥8፤ 2ቆሮ. 5፥10፤ ቆላ. 3፥25።

**ብድር**፤ በአራጣ፥ በወለድ ወይም እንዲሁ ተሰጥቶ የሚመለስ ገንዘብ። እስራኤላውያን ለወንድም ሲያበድሩ የተቸገረውን ለመርዳት እንጂ ለማትረፍ አልነበረም። ሆኖም ለእንግዳ ወይም ለባዕድ በወለድ ያበድሩ ነበር፤ ዘጸ. 22፥25፤ ዘዳ. 23፥19:20። በአ.ኪ. ለነጋዴዎችና ለገንዘብ ለዋጮች በወለድ ማበደር ይፈቀዳል፤ ሉቃ. 19፥23። ነገር ግን ሰው በግል ሲያበድር ለእርዳታ እንጂ ሌላ ጥቅም ለማግኘት ተስፋ ማድረግ አይገባውም (ሉቃ. 6፥32-38)፥ በእስራኤል ለብድር መያዣ መቀበል ይፈቀድ ነበር። ሆኖም ድሆች እንዳይጐዱ ልዩ ልዩ ሕግ ተደንግጎ ነበር፤ ዘዳ. 15፤ 24፥10-13። «ዋስ»፥ «ዕዳ»፥ «መያዣ» ይመ.

**ብጉር**፤ በመ.ቅ. እንደተገለጠው ቃሉ በፊት ላይ በሌላም ቆዳ ላይ የሚገኝ መግል የሚይዝ አንድ ዓይነት በሽታን ያመለክታል፤ ዘሌ. 13፥2። «በሽታ» ይመ.

**ብፁዕ፥ ብፅዕት፥ ብፁዓን**፤ የተባረከ ደስተኛ ማለት ነው፤ ሐ.ሥ. 20፥35፤ ሉቃ. 1፥48-49፤ ማቴ. 5፥3-12።

**ቦዔዝ**፤ በመሳፍንት ዘመን የነበረ ሀብታም የቤተ ልሔም ሰው። ከሞዓብ ወገን የሆነችውን ሩትን በውርስ አግብቶ ከእርስዋ ኢዮቤድን ወለደ፤ ሩት 2፥1፤ 4፥13-22። ኢዮቤድ የንጉሥ ዳዊት አያት ስለሆነ፥ ቦዔዝ በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ የትውልድ ሐረግ ውስጥ ይቈጠራል፤ ማቴ. 1፥5-6፤ ሉቃ. 3፥32።

**የተልባ እግር**፤ የተልባ እግር ወይም የአገዳው ልጥ ጭረትነት ያለው፥ ያው ጭረቱ በጥበብ ተሠርቶ ጥሩ ጨርቅ ወይም በፍታ የሚሆን፤ ኢያሱ 2፥6፤ ኢሳ. 19፥9፤ ራእ. 18፥16። «በፍታ» ይመ.



ተልባ

**ተመመ**፤ ኃይለኛ የባሕር፥ የጐርፍ ድምፅ የባሕር ሞገድ በኃይል ሲናወጥ፥ ጐርፍ ነጋሪት በኃይል ሲጮኽ ተመመ ይባላል። በምሳሌ የእግዚአብሔርን ታላቅ ክብር፥ የሠራዊትን ብዛት ያመለክታል፤ ኢሳ. 5፥30።

**ተመስጦ**፤ ሳያንቀሳቅሱ በዙሪያ ያለውን ሁሉ ረስቶ በልዩ አሳብ ውስጥ መዋጥ፥ ሕሊናን ወደ አንድ ነገር ብቻ መስቀል። ጴጥሮስ በዚህ ሁኔታ ሲጸልይ

ራእይ አየ (ሐ.ሥ. 10፥9-16፤ 11፥5)፤ እንደዚሁም ጳውሎስ በተመስጦ ከጌታችን ከኢየሱስ ጋር ተነጋገረ፤ ሐ.ሥ. 22፥17-21።

**ተሙዝ፤** የባቢሎን የግብርና አምላክ (ጣዖት)፤ ሕዝ. 8፥14። ቃሉ ለእስራኤል አራተኛ የዓመት ወር ሆኗል። «ወር» ይመ.

**ተማለለ፤** ለመነ፥ ወደ እግዚአብሔር የምህላ ጸሎት አደረገ፤ ኤር. 27፥18።

**ተማፀነ፤** ሸሸቶ ተጠጋ። የሙጥኝ አለ፤ አደራ ሰጠ፤ መዝ. 143፥9። «መማፀኛ ከተማዎች» ይመ.

**ተምር፤** ፍሬው እንደ ማር የሚጣፍጥ፥ መልኩ ዘንባባን የሚመስል ረጅም ዛፍ። ወንዴውና ሴቴው ዛፍ የተለያዩ ሲሆኑ፥ ፍሬ የሚገኘው ከሴቴው ዛፍ ብቻ ነው፤ ሰሌን ግን ከሁለቱም ይሠራል፤ ዘፍ. 43፥11።



የዘንባባ ዛፍና የቴምር ፍሬ

**ተምሳሊት፤** ምሳሌ፥ አምሳል፥ አምሳያ፥ የነገር አንጻር፥ ተረት፤ መዝ. 78፥2።

**ተምች፤** ጠጉራም ተንቀሳቃሽ በዕብራይስጥ ቋንቋ «ጋዛም» ይባላል። ይህም ትል ሳይሆን በመሬት የሚሽከረከር አንበጣ ማለት ነው፤ ኢዩ. 1፥4።

**ተረት፤** እውነት ነገርን በውስጡ ያዘለ ልብ ወለድ፥ እንቆቅልሽ ወይም ምሳሌ፤ መሳ. 9፥7-15፤ 2ነገ. 14፥9። ሐዋርያት ስለ ከንቱ ተረት ማስጠንቀቂያ ሰጥተዋል፤ 1ጢሞ. 1፥4፤ 4፥7፤ 2ጢሞ. 4፥4፤ ቲቶ 1፥14፤ 2ጴጥ. 1፥16። በሰው ላይ የሚሰነዘር ቀልድና ስድብ መሳቂያና መተረቻ ተረት ይባላል፤ ዘዳ. 28፥37፤ 1ነገ. 9፥7።

**ተረፈ ባሮክ (መጽሐፈ ባሮክ)፤** እግዚአብሔር ለባሮክ፥ ለአቤሜሌክና ለኤርምያስ ገልጦላቸው፥ እስራኤላውያንን በባቢሎን በምርኮ በነበሩበት ዘመን እንዴት ጠብቆ እንዳሳለፋቸውና በኤርምያስ መሪነት ምርኮኞቹ ወደ ኢየሩሳሌም እንዴት እንደተመለሱ የሚተርክ መጽሐፍ ነው። በትልቁ የአማርኛ መ.ቅ. በሰቆቃወ ኤርምያስ 7፥6-11፥63 ታትሟል። የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤ.ክ. ከትንቢተ ኤርምያስ ጋር ጨምራ ከብ.ኪ. መጻሕፍት ጋር ቈጥራ ትቀበለዋለች። ይህ መጽሐፍ በብሉይ ኪዳን 2ኛ የቀኖና መጻሕፍት ውስጥ «ተረፈ ኤርምያስ» በሚል ስያሜ ተጽፎ ይገኛል።

**ተራራ፤** በጥንት ዘመን ብዙ ሰዎች ተራራን እንደ ቅዱስ ቦታ አድርገው ይቈጥሩት ነበር። በእስራኤላውያን ዘንድ የሲና ተራራ (ዘዳ. 33፥2፤ መሳ. 5፥4:5) እና የጽዮን ተራራ (መዝ. 48፥1:2)፥ እግዚአብሔር እንደተገለጠባቸው ቦታዎች ይቈጠሩ ነበር። በመ.ቅ. ተራራ የልዩ ልዩ ነገር ምልክት ወይም ምሳሌ ነው (ዘኁ. 4፥7)፥ ዘላለማዊነት (ዘፍ. 49፥26)፥ ብርታትና ጽናት (መዝ. 121፥1:2)፥ የክርስቶስ መንግሥት (ዳን. 2፥35፤ ኢሳ. 2፥2) በተራራ ተመስለዋል። የተራራ ስብከት የተባለው የክርስቶስ ትምህርት (ማቴ. 5-7፤ ሉቃ. 6፥17-49) የተሰማበት ተራራ የትኛው እንደሆነ አልተረጋገጠም።

**ተራዳ፤** የድንኳን ማቆሚያ ምሰሶ፤ ዘኁ. 3፥36፤ 4፥31።

**ተራፊም፤** በእስራኤል አገር የቀድሞ ሰዎች የሚያመልኩበት፥ የአምላካቸውን ፈቃድ የሚጠይቁበት፥ በየቤቱ የሚቀመጥ ምስል። ደግሞም ተራፊምን የያዘ ወራሽ ነበር፤ ዘፍ. 31፥19:30-32፤ መሳ. 17፥5፤ 18፥14-20፤ ሕዝ. 21፥21። ተራፊም ለእስራኤል እንቅፋት ነበሩ፤ 1ሳሙ. 15፥23፤ 2ነገ. 23፥24። «ምስል» ይመ



ከዑር የተገኘ የጭቃ ምስል

**ተርሴስ፤** የኖኅ ልጅ የያፌት ልጅ የያዋን ልጅ ስምና የኖረበት አገር ስም፤ ዘፍ. 10፥4። አገሩ ከታላቁ ባሕር በስተምዕራብ ያለ፥ ብዙ ማዕድን የሚገኝበት ስፍራ ነው፤ ዮናስ 1፥3፤ ኢሳ. 66፥19፤ ኤር. 10፥9። የተርሴስ መርከቦች ብዙ ሀብት የሚያመጡ ትልልቅ መርከቦች ነበሩ፤ 1ነገ. 10፥22፤ 2ዜ.መ. 9፥21፤ መዝ. 48፥7።

**ተርበተበተ**፤ ተንቀጠቀጠ፥ ተፋጠነ፤ ኢሳ. 8፥14።

**ተርብ**፤ ሽንጠ ረዥም፥ የሚናደፍ ዝንብ። ተፈጥሮው እንደ ንብ ሲሆን፥ ማር በመጠኑ ይሠራል። የእስራኤል ልጆች ወደ ከነዓን ሲገቡ እግዚአብሔር አረማውያንን የሚያባርሩ ተርቦችን ሰደደ፤ ዘጸ. 23፥28፤ ዘዳ. 7፥20፤ ኢያሱ 24፥12።

**ተርታን**፤ በአሦር መንግሥት ከንጉሡ ቀጥሎ ያለው የአስተዳዳሪው ዋና የማዕረግ ስም፤ 2ነገ. 18፥17፤ ኢሳ. 20፥1።

**ተሰሎንቄ**፤ ሐዋርያው ጳውሎስ በ2ኛ የስብከት ጉዞው ከሲላስና ከጢሞቴዎስ ጋር ወደ ተሰሎንቄ ሄደ። ከተማይቱ በግሪክ አገር የመቄዶንያ አውራጃ ዋና ከተማና ታላቅ ወደብ ስትሆን፥ ወደ ምሥራቅ በሚወስደው በታላቁ የሮም መንገድ ላይ ትገኝ ነበር። ጳውሎስ በፊልጵስዩስ ከተማ ስደት ከደረሰበት በኋላ ወደ ተሰሎንቄ ደረሰ፤ እዚያም 3 ሳምንት ያህል አስተማረ፤ ሐ.ሥ. 17፥1-10፤ 1ተሰ. 2፥2። ካ. 6 ሸ.።

**የተሰሎንቄ መልእክቶች**፤ እነዚህ መልእክቶች የተጻፉት ቅዱስ ጳውሎስ ከተሰሎንቄ ከወጣ ከጥቂት ወራት በኋላ ነው። ዘመኑ 50 ወይም 51 ዓ.ም. ሊሆን ይችላል። ጳውሎስ ከተሰሎንቄና ከቤርያ በአይሁድ ተሰድዶ እንዲወጣ በመደረጉ አቴና ሄዶ ረዳቱ የነበረው ጢሞቴዎስ ወደ አቴና ሲመጣ፥ ጳውሎስ ስለ ተሰሎንቄ ቤ.ክ. እጅግ ተጨንቆ ስለነበረ ምእመናኑን ሄዶ እንዲጎበኛቸው ላከው። ጢሞቴዎስም የተሰሎንቄን ምእመናን በደህና አግኝቶ ከጎበኛቸው በኋላ ተመልሶ በመሄድ በቆሮንቶስ ከጳውሎስ ጋር ተገናኘ፤ ሐ.ሥ. 17፥10:14-15፤ 18፥1:5፤ 1ተሰ. 3፥1-6። ሐዋርያው ከጐበኘቱ የመጣለትን መልካም ወሬ ከሰማ በኋላ ሁለት መልእክቶቹን ለዚች አዲስ ቤ.ክ. አከታትሎ ጻፈ።

በሁለቱ መልእክቶች ውስጥ ጳውሎስ በሚከተሉት ነጥቦች ላይ አተኩሯል ፦

ሀ) ለደኅንነት እግዚአብሔር በቃሉ አማካይነት በኃይል ይሠራል፤ 1ተሰ. 1፥4-5፤ 2፥1:13፤ 2ተሰ. 1፥3-5፤ 3፥1።

ለ) ምእመናን መከራ ቢቀበሉም በመከራው እየጸኑ ወንጌልን ማስፋፋት ታላቅ ደስታ ነው፤ 1ተሰ. 1፥6-8፤ 2፥14፤ 2ተሰ. 1፥3-5፤ 3፥1።

ሐ) የወንጌል አገልጋይ ከአገልግሎቱ የተነሣ ያመኑትን ይወዳቸዋል፤ ይንከባከባቸዋልም፤ 1ተሰ. 2፥7-9:11-12:17-20፤ 3፥1:5-6፤ 2ተሰ. 3፥8-9።

መ) አማኞች የመሪዎቻቸውን አርአያ ተከትለው በፍቅርና በቅድስና በሥራም ማደግ ይገባቸዋል፤ 1ተሰ. 1፥5-7፤ 3፥12-13፤ 4፥3-7:9:11፤ 5፥12-15:23፤ 2ተሰ. 1፥3፤ 3፥6-13።

ሠ) በክርስቶስ ትንሣኤ ላይ የተመሠረተው የክርስቲያን ተስፋ ፍጻሜ የሚያገኘው በዳግም ምጽአት ነው፤ 1ተሰ. 1፥2-3:9-10፤ 2፥19፤ 3፥13፤ 5፥10:23። ዳግም ምጽአቱ ድንገተኛ ይሆናል፤ 4፥13-17፤ 5፥1-11፤ 2ተሰ. 1፥5-10። በድንገት ቢመጣም ከመምጣቱ በፊት በዓለም ብዙ ምልክቶች ይታያሉ፤ 2ተሰ. 2፥1-12። ስለዚህ አማኞች እየተጽናኑ በፍቅር፥ በቅድስናና በሥራ ዳግም ምጽአቱን መጠበቅ ይገባቸዋል፤ 1ተሰ. 4፥18፤ 5፥23፤ 2ተሰ. 2፥15-17።



የተሰሎንቄ የወደብ ከተማ በጳውሎስ ዘመን

የመጀመሪያው መልእክት አከፋፈል ፦

1. ስለ ተሰሎንቄ ቤ.ክ. የሐዋርያው፥ ሀ) ምስጋና (ም.1)፥ ለ) ገድል (2፥1-16)፥ ሐ) ስጋት፤ 2፥17-3፥13።

2. ስለ ምእመናን ቅድስናና ፍቅር፤ 4፥1-12።

3. ስለ ክርስቶስ ዳግም ምጽአት፤ 4፥13-5፥11።

4. ስለ ምእመናን በኅብረት መኖር፤ 5፥12-28።

የሁለተኛው መልእክት አከፋፈል ፦

1. ክርስቲያንና መከራ፤ ም. 1።

2. ክርስቲያንና ዳግም ምጽአት፤ ም. 2።

3. ክርስቲያንና ዕለታዊ ተግባሩ፤ ም. 3።

**ተስፋ**፤ ምኞትና ናፍቆት ብቻ ሳይሆን፥ እለኝታና መተማመን የሚገኝበት ነው፤ ሮም 15፥13። የክርስቲያን ተስፋ በክርስቶስ ትንሣኤ ላይ የተመሠረተ የእግዚአብሔር ስጦታ ነው፤ 1ጴጥ. 1፥3-5። ተስፋ በዚህ ዓለም አይወሰንም፤ 1ቆሮ. 15፥9። በሚመጣው ዓለም የእግዚአብሔር መንግሥት ተካፋዮች እንድንሆን ለእኛም ለሌሎችም ተስፋ አለን፤ ኤፌ. 1፥18፤ 1ተሰ. 2፥19። ተስፋችን ምንም እንኳን አሁን ባይታይም የተረጋገጠና የማይጠፋ ነው፤ ዕብ. 11፥1፤ ሮም 5፥5። እግዚአብሔር በክርስቶስ ተስፋ ሰጥቷልና እርሱ ስለማይዋሽ ተስፋችን ከንቱ አይሆንም፤ 1ጢሞ. 1፥1፤ ቲቶ 1፥1-2። ተስፋ ከእምነትና ከፍቅር ጋር የተያያዘ ነው፤ 1ቆሮ. 13፥13። ተስፋ እማኙን በቅድስና እንዲኖርና መከራን እንዲታገሥ ያበረታታዋል፤ 1ዮሐ. 3፥3፤ ሮም 8፥18። እግዚአብሔር ለሰጠው ተስፋ ተካፋዮች መሆናችንን በመንፈስ ቅዱስ አረጋግጧል፤ ሮም 8፥14-16፤ ኤፌ. 1፥13:14። ሆኖም ተስፋው ፈቃዱን ለሚያደርጉ መሆኑን ዐውቀን የእግዚአብሔርን ፈቃድ ለመፈጸም መትጋት አለብን፤ ማቴ. 7፥21-23፤ 2ጴጥ. 1፥10።

**የተስፋ ቃል**፤ የተስፋ ቃል እግዚአብሔር ለዓለም ሁሉ የሚሆን መድኀኒት እንደሚልክ የገለጠው ቃል ነው። በመጀመሪያ የተሰጠው ለአዳም ነው፤ ዘፍ. 3፥15። ቀጥሎም ለአብርሃም ተሰጠ፤ ዘፍ. 12፥2:7። ዙፋኑ ለዘለዓለም እንደሚነግሥ የተስፋ ቃል ለዳዊት ተሰጠ፤ 2ሳሙ. 7፥12:13:28። የተሰጠው የተስፋ ቃል በጠቅላላው በክርስቶስ እንደተፈጸመ አ.ኪ. ይነግረናል፤ ሉቃ. 1፥67-79፤ 2ቆሮ. 1፥19-20፤ ኤፌ. 3፥5:6። መንፈስ ቅዱስ ይመጣል በማለት ክርስቶስ የሰጠው የተስፋ ቃል በበዓለ ኀምሳ (በጰንጠቆስጤ ቀን) ተፈጸመ፤ ሐ.ሥ. 2። ለአብርሃም ዘር የተሰጠው የተስፋ ቃል እንደ አብርሃም እምነት ላላቸው ሁሉ እንደሆነ ጳውሎስ አረጋገጠ፤ ሮም 4፥13-17። ለአማኞች የተሰጡ ብዙ የተስፋ ቃላት አሉ፤ ያዕ. 1፥5፤ 2፥5፤ 1ጢሞ. 4፥8፤ 2ጴጥ. 3፥9፤ ሮም 16፥20፤ 1ቆሮ. 10፥13፤ 1ተሰ. 4፥13-18።

**ተቀለበሰ**፤ ታጠፈ፥ ተቀነፈ፤ ሕዝ. 40፥43።

**ተቀረቀረ**፤ ጠልቆ ገባ፥ ተሰነቀረ፤ 1ሳሙ. 17፥49።

**ተቃዋሚ**፤ ባላንጣ። የክርስቶስ ተቃዋሚ፤ ይህ የዐመፅ ሰው (ሐሳዊ መሢሕ) በዓለም መጨረሻ የሚገለጥ ክርስቶስን የሚቃወም ነው። የእርሱ መንፈስ አሁን በዓለም ይሠራል። ወደ መጨረሻውም በአንድ ሰው ወይም ምናልባት በአንድ ፍልስፍና የተቃውሞ መንፈሱ ጉልህ ሆኖ ይታያል። ዋና ሐሰቱ «ኢየሱስ የእግዚአብሔር የባሕርይ ልጅ አይደለም» ብሎ መናገርና ራሱን አምላክ አድርጎ ማወጅ ነው፤ 1ዮሐ. 2፥18:22፤ 4፥3፤ 2ዮሐ. 7፤ 2ተሰ. 2፥4። ዮሐንስ ተቃዋሚው ብሎ ሲናገር፥ ጳውሎስ ደግሞ የዐመፅ ሰው ብሎ ይገልጠዋል። የዐመፅ ሰው ከሚመለክ ሁሉ በላይ ራሱን ከፍ ከፍ አድርጎ በሰይጣን ኃይል ብዙዎችን ያስታል። ግን ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ሲመጣ ይህን የዐመፅ ሰው ያጠፋዋል፤ 2ተሰ. 2፥1-12። ተቃዋሚው ወይም የዐመፅ ሰው ማን ነው? ቢባል በዓለም መጨረሻ የሚገለጠው አሁን በስውር እየሠራ ያለው መንፈስ ነው። «ርኵሰት»፥ «የጥፋት ርኵሰት» ይመ.

**ተቅማጥ**፤ ከአንጀት ደም ሊወጣ እስከሚችል ድረስ የሚያም በሽታ፤ ሐ.ሥ. 28፥8። «በሽታ» ይመ.

**ተቆራቆሰ**፤ የጨበጣ ውጊያ ወይም ጦርነት ተጋጠመ፤ 2ሳሙ. 2፥14።

**ተቈጠረ**፤ ሰው ሳይሠራ የአንዱ ድርጊት ለሌላው ሲታሰብ «ተቈጠረ» ይባላል። የአዳም ኃጢአት ለዘሩ ሁሉ ተቈጠረ፤ የሰው ኃጢአት በክርስቶስ ተቈጠረ፤ የክርስቶስም ጽድቅ ለምእመናን ተቈጠረ፤ ኢሳ. 53፥12፤ ሮም 4፥3፤ 5፥12:18፤ 2ቆሮ. 5፥21።

**ተትጐለጐለ**፤ በብዛት ወጣ፤ በዝቶ ታየ። ብዙ ጊዜ ለጢስ ይነገራል፤ ኢሳ. 30፥27።

**ተቸ**፤ ፈረደ፥ ነገሩን መረመረ፤ አስረዳ፤ ሐ.ሥ. 26፥10።

**ተነጠጠ**፤ ለዘበ፥ ተፋቀ ወይም ጥሩ ሆኖ ተቀረጸ፤ ቃሉ ከቀንድ ለሚሠራ ነገር ሁሉ ይነገራል፤ መ.መ. 7፥3።

**ተንቀሳቃሾች (ተባይ)**፤ እግዚአብሔር ተንቀሳቃሾችን በስድስተኛው ቀን ፈጠረ፤ ዘፍ. 1፥25። በመ.ቅ. የተጠቀሱ የተባይ ዓይነቶች የሚከተሉት ናቸው ፦ ሸረሪት (ኢዮብ 8፥14)፥ ቁንጫ (1ሳሙ. 24፥14)፥ ቅማል (ዘጸ. 8፥16)፥ ብል (ኢዮብ 13፥28)፥ ተምች (ኢዩ. 1፥4)፥ ተርብ (ዘጸ. 23፥28)፥ ትል (ኢዮብ 7፥5)፥ ትንኝ (ማቴ. 23፥24)፥ ንብ (መሳ. 14፥8)፥ አልቅት (ምሳ. 30፥15)፥ አንበጣ (ዘጸ. 10፥4)፥ ኩብኩባ (ኢዩ 1፥4)፥ ዝንብ (ዘጸ. 8፥21)፥ ደጎብያ (ኢዩ. 1፥4)፥ ጉንዳን (ምሳ. 30፥25)፥ ጊንጥ (ሕዝ. 2፥6)።

**ተንትናይ፤** የፋርስ ንጉሥ ዳርዮስ በኤፍራጥስ ወንዝ ማዶ በነበረው በሰማርያ ላይ የሾመው ገዥ፤ ዕዝ. 4፥24፤ 5፥3:6፤ 6፥6:13። የኢየሩሳሌም ቤተ መቅደስ መታደስ ተጀምሮ ዐሥራ ስድስት ዓመት ከተቋረጠ በኋላ፥ አይሁድ እንደገና የእግዚአብሔርን ቤት ሊሠሩ በጀመሩ ጊዜ፥ ተንትናይ ሥራው የተጓተለበትን ምክንያት መርምሮ ወደ ዳርዮስ ጻፈ። የፈቃድም ደብዳቤ ተቀብሎ አይሁድን ረዳቸው፤ ዕዝ. 5 እና 6።

**ተንኰል፤** ሰወርዋራ ዘዴ። በዚህ ረገድ ሰውም ሆነ እንስሳ የተለየ ዘዴ አለው። ለመልካምም ለክፋም ሊጠቀምበት ይችላል። ሰው ሰይጣንን ተከትሎ ዘዴውን ለክፋት ስለተጠቀመበት፥ ተንኰለኛ ሆኗል፤ ዘፍ. 3፥1፤ ኤር. 17፥9፤ ማር. 7፥22፤ ሐ.ሥ. 13፥10። ክርስቶስ ግን ተንኰል አልነበረበትም (1ጴጥ. 2፥22)፥ የተከታዮቹም አካሄድ ግልጥና ተንኰል የሌለበት ሊሆን ይገባል፤ ዮሐ. 1፥48፤ 1ተሰ. 2፥3፤ 1ጴጥ. 2፥1።

**ተንዶለዶለ፤** በብዛት ወረደ፤ ፈሰሰ፤ መነጨ፤ 2ዜ.መ. 32፥4፤ ኢዮብ 38፥27።

**ተአምር፤** ተአምራት። አድራጊውን የሚያሳስብ አስደናቂ ድርጊት። ተአምር ብዙ ጊዜ በዓለም ጥንተ ተፈጥሮ የማይሆነውንና ያልተለመደውን ማድረግ ነው። ለምሳሌ ኢየሱስ ውሃውን ወደ ወይን ለወጠ፤ ሳይሰጥምም በባሕር ላይ ተራመደ። አንዳንድ ጊዜ ተአምር ለዓለም የተፈጥሮ ጠባይ እንደሚስማማ ሆኖ ይደረጋል። ለምሳሌ በግብጻውያን ላይ የደረሱት የመጀመሪያ 9 መቅሠፍቶች አልፎ አልፎ በዓለም ታሪክ ታይተዋል፤ ሆኖም ተአምራት ሆነው የተገኙት ሙሴ በተናገረበት ጊዜ ስለተፈጸሙ ነው። እንደ መ.ቅ. አሳብ የሆነ ነገር ሁሉ የእግዚአብሔር ሥራ ነው፤ ለምሳሌ መዝ. 104 ይመ.። ተአምር ወይም ድንቅ፥ እግዚአብሔር ብዙ ጊዜ የሚያደርገው ነገር ነው። ተአምራት የአምላክነቱን ሥራ ያስታውሳሉ፤ የእግዚአብሔርን ፈቃድ ይፈጽማሉ፤ የመልእክተኞችንም ከእርሱ ኃይል መቀበል ያረጋግጣሉ (1ነገ. 18፥36-39፤ ሐ.ሥ. 10፥38)፤ ብዙ ጊዜም የሰዎችን ችግር ለማቃለል ተደርገዋል።

ሰይጣንና ተከታዮቹም ተአምራትን ያደርጋሉ፤ ዘጸ. 7፥11-13:22፤ ማቴ. 24፥24፤ 2ተሰ. 2፥9። በእግዚአብሔርና በሰይጣን ተአምራት መካከል ያለውን ልዩነት እንዴት ማሳየት ይቻላል? ክርስቶስ ለታይታ ያህል በድርጊቱ ጥቅም የሌለውን ተአምር ለማድረግ ፈቃደኛ አልነበረም፤ ማቴ. 4፥6-7፤ 12፥39። የክርስቶስ ተአምራት ለሰዎች ጥቅም ከመሆናቸውም በላይ ምልክቶች ናቸው። ምክንያቱም ከእግዚአብሔር መምጣቱንና የባሕርይ አምላክነቱን ያመለክታሉና፤ ዮሐ. 20፥30:31።

በብ.ኪ. እንደተጻፈው ተአምራት በተለይ በሙሴና በኢያሱ፥ እንደዚሁም በኤልያስና በኤልሳዕ ዘመን ተፈጽመዋል። በአ.ኪ.ም ክርስቶስ ብዙ ተአምራት እንዳደረገ ተገልጿል («ኢየሱስ» 3መ ይመ.)። ክርስቶስ ተስፋ እንደሰጣቸው፥ ሐዋርያት በመንፈስ ቅዱስ ኃይል ብዙ ተአምራትን አደረጉ፤ በእነዚህም ምልክቶች ሐዋርያነታቸው ተረጋገጠ፤ ዮሐ. 14፥12-14፤ ማር. 16፥16-20፤ ሐ.ሥ. 4፥30:31፤ 2ቆሮ. 12፥12፤ ዕብ. 2፥4። ሐዋርያት ሰዎችን ቀሥፉ (ሐ.ሥ. 5፥1-11፤ 13፥8-12)፤ ሙታንንም አስነሡ፤ በተለይም ሰዎችን ከጋኔን እስራትና ከበሽታ ፈወሱ («ፈውስ» ይመ.)። ተአምራትን በማድረጋቸው ብዙ ሰዎች ንግግራቸውን አዳመጡ፤ ሐ.ሥ. 3፥9-12፤ 14፥11-15። ተአምራትን ማድረግ ከመንፈስ ቅዱስ ስጦታዎች አንዱ ነው፤ 1ቆሮ. 12፥10:28፤ ገላ. 3፥5። ዛሬ ተአምራት እንደቀድሞው ዘመን በብዛት አለመታየታቸው በእምነት፥ በጸሎትና በሌላም ጉድለት ምክንያት ሊሆን ይችላል፤ ማቴ. 17፥14-21። በብ.ኪ. ዘመን እንዲሁም በአ.ኪ. ዘመን ተአምራት በብዛት የተሠሩባቸው ልዩ ጊዜአት መኖራቸው ግልጥ ነው፤ ዛሬም ቢሆን ወንጌል ለመጀመሪያ ጊዜ በአንድ አገር ሲሰበክ ቃሉን ለማረጋገጥ ተአምራት የሚታዩባቸው ጊዜአት አሉ፤ ማር. 16፥20፤ ዕብ. 2፥4።

1. <u>ተአምራት በብ.ኪ. ዘመን፤</u>

እግዚአብሔር በብ.ኪ. ዘመን ደጋግሞ የበረከትም ሆነ የፍርድ እርምጃዎችን ወስዷል። ከዚህ በታች በተዘረዘሩት ክሥተቶች ግን የሰው ድርሻም ስለነበረ የብ.ኪ. ዘመን ክሥተቶችን በ3 ክፍል፥ ማለትም በመቅሠፍት (መ)፥ በበረከት (በ) እና በፈውስ (ፈ) ልንከፍላቸው እንችላለን ፦

ሀ) <u>ከሙሴ ዘመን በፊት</u>

የሄኖክ መወሰድ፤ ዘፍ.5፥21-24 (በ)

የጥፋት ውሃ፤ ም. 6-7 (መ)

የሰዶምና የገሞራ መደምሰስ፤ 19፥24 (መ)

የሎጥ ሚስት ወደ ጨውነት መለወጥ፤ 19፥26 (መ)

የይስሐቅ መፀነስና መወለድ፤ 21፥1-3 (ፈ)

የርብቃ ማኅፀን መከፈት፤ 25፥21 (ፈ)

ለ) <u>በሙሴ ዘመን</u>

የበትር ወደ እባብነት መለወጥ፤ ዘጸ.4፥3፤ 7፥10(በ)

በሙሴ እጅ ለምጽ ያለበት መምሰሉ፤ 4፥6-7 (በ)

መቅሠፍት በግብጽ ላይ፤ ም. 7-12 (መ)

የቀይ ባሕር መከፈል፤ 14፥21-25 (በ)

የቀይ ባሕር መመለስ፤ 14፥26-31 (መ)

የመራራው ውሃ መለወጥ፤ 15፥23-25 (በ)

የመናና የድርጭት መገኘት፤ ም.16 (በ)

ውሃ በማሳህ መፍለቁ፤ 17፥5-7 (በ)

የናዳብና የአቢሁ ሞት፤ ዘሌ. 10፥1-2 (መ)

የእሳት ቃጠሎ በእስራኤል፤ ዘኍ. 11፥1 (መ)

ሰኦን ቆሬ ሞት፤ ም. 16 (መ)
የአሮን በትር ልምላሜ፤ ም. 17 (በ)
ውሃ በመሪባ መፍለቁ፤ 20፥7-11 (በ)
የነሐስ እባብ፤ 21፥5-9 (ፈ)
አህያ መናገሩ፤ 22፥21-30 (በ)

ሐ) በኢያሱ ዘመን

ዮርዳኖስን መሻገራቸው፤ ኢያሱ 3፥14-17 (በ)
የኢያሪኮ አወዳደቅ፤ ም.6 (መ)
የበረዶ አወራረድ፤ 10፥11 (መ)
የፀሐይ መቆም፤ 10፥13 (በ)

መ) በመሳፍንት ዘመን

የሶምሶን ኃይል፤ መሳ. ም. 14-16 (በ)
ውሃ በሌሒ መፍለቁ፤ 15፥19 (በ)
የዳጎን መውደቅ፤ 1ሳሙ. ም. 5 (መ)
የላሞች ወደ ቤትሳሚስ መሄድ፤ 6፥7-12 (በ)
የቤትሳሚስ ሰዎች መገደል፤ 6፥19 (መ)
የፍልስጥኤማውያን መሸበር፤ 7፥10-12 (መ)
የመከር ጊዜ ዝናብ፤ 12፥17-18 (መ)

ሠ) ከዳዊት እስከ ኤልያስ ዘመን

በዛፎች የተሰጠ ድምፅ፤ 2ሳሙ. 5፥23-25 (በ)
የዖዛ መገደል፤ 6፥7 (መ)
የኢዮርብዓም ክንድ መሰለል፤ 1ነገ. 13፥4 (መ)
መሠዊያው መሰባበሩ፤ 13፥5 (መ)

ረ) በኤልያስ ዘመን

ለ42 ወራት ዝናም መጥፋቱ፤ 1ነገ. ም. 17 (መ)
ኤልያስ በቍራዎች መመገቡ፤ 17፥4-6 (በ)
የመበለቲቱ ምግብ መበርከት፤ 17፥8-16 (በ)
የመበለቲቱ ልጅ ከሞት መነሣት፤ 17፥17-24 (በ)
ከሰማይ እሳት መውረዱ፤ 18፥30-39 (በ)
የአፈቅ ቅጥር መውደቁ፤ 18፥30-39 (በ)
ወታደሮች በእሳት መሞታቸው፤ 2ነገ. ም. 1 (መ)
የዮርዳኖስ ወንዝ መከፈል፤ 2፥7-8 (በ)
የኤልያስ መነጠቅ፤ 2፥11 (በ)

ሰ) በኤልሳዕ ዘመን

የዮርዳኖስ ወንዝ መከፈል፤ 2ነገ. 2፥14 (በ)
የኢያሪኮ ውሃ መንጻት፤ 2፥21-22 (በ)
የ42ቱ ልጆች መረገም፤ 2፥23-24 (መ)
ውሃ በምድረ በዳ መገኘቱ፤ 3፥16-20 (በ)
ለመበለቲቱ ዘይት መገኘቱ፤ 4፥2-7 (በ)
የሱነማዊቷ ሴት ልጅ መወለድ፤ 4፥16-17 (ፈ)
ልጅዋ ከሞት መነሣቱ፤ 4፥32-36 (ፈ)
የወጡ መራራነት መወገድ፤ 4፥38-41 (በ)
የመቶ ሰዎች መመገብ፤ 4፥42-44 (በ)
የንዕማን መፈወስ፤ 5፥8-14 (ፈ)
የግያዝ መቀጣት፤ 5፥20-27 (መ)
መጥረቢያው መንሳፈፉ፤ 6፥5-7 (በ)
የአገልጋዩ ዐይኖች መከፈት፤ 6፥15-17 (በ)
የጦር ሠራዊት መታወር፤ 6፥18-20 (መ)
ሬሳ ነፍስ መዝራቱ፤ 13፥21 (ፈ)

ሸ) ከኤልሳዕ ዘመን በኋላ

የዮናስ ከዓሣ መዳን፤ ዮናስ 2፥10 (በ)
የአሦራውያን መቀጣት፤ 2ነገ. 19፥35 (መ)
የጥላ ወደ ኋላ መመለስ፤ 20፥9-11 (በ)
የዖዝያን መቀጣት፤ 2ዜ.መ. 26፥16-21 (መ)
የሠለስቱ ደቂቅ መዳን፤ ዳን. 3፥19-27 (በ)
ዳንኤል በአንበሳዎች ጕድጓድ፤ 6፥16-24 (በ)

2. የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ተአምራት፤

ክርስቶስ ብዙ ሰዎችን ፈወሰ (ማቴ 4፥23-24፤ 9፥35፤ 10፥1፤ 12፥15፤ 15፥30፡ 19፥2፤ 21፥14)፥ እንደዚሁም ከብዙ ሰዎች አጋንንትን አወጣ፤ ማቴ. 4፥24፤ 8፥16፤ 10፥1። በዝርዝር የተመዘገቡትን የኢየሱስ ተአምራት በአራት ልንከፍላቸው እንችላለን። ሰንጠረዡን ይመ.

3. በሐዋርያት የተሠሩ ተአምራት፤

በ«የሐዋርያት ሥራ» ውስጥ የተመዘገቡ ተአምራትን በ5 ክፍል ልንመዘግባቸው እንችላለን ፦

1. ከልዩ ልዩ ደዌ የተፈወሱ ሰዎች፤

አንካሳ ሆኖ የተወለደው ሰው፤ ም. 3
ሳውል እንደገና ማየት መቻሉ፤ 9፥17-18
ሽባው ኤንያ፤ 9፥33-34
በልስጥራን እግሩ የሰለለው ሰው፤ 14፥8-10
የመላጥያ አለቃ አባት፤ 28፥8

እያሌ ሕሙማን በኢየሩሳሌም፥ ሽባዎችና አንካሶች በሰማርያ፥ እንደዚሁም በኤፌሶንና በመላጥያ ብዙ በሽተኞች እንደተፈወሱ ተጽፏል፤ 5፥16፤ 8፥7፤ 19፥12፤ 28፥9።

2. አጋንንት የወጡላቸው ሰዎች ፦

የፊልጵስዩስዋ ምዋርተኛ ገረድ፤ 16፥16-18
በኢየሩሳሌም፥ በሰማርያና በኤፌሶን ከሰዎች አጋንንት

| የኢየሱስ ተአምራት | ማቴዎስ | ማርቆስ | ሉቃስ | ዮሐንስ |
|---|---|---|---|---|
| 1. ከልዩ ልዩ ደዌ የተፈወሱ ሰዎች | | | | |
| ለምጻሙ ሰው | 8÷2-4 | 1÷40-42 | 5÷12-13 | |
| የመቶ አለቃው አገልጋይ | 8÷5-13 | | 7÷1-10 | |
| የጴጥሮስ ዐማት | 8÷14-15 | 1÷30-31 | 4÷38-39 | |
| ሽባው | 9÷2-7 | 2÷3-12 | 5÷18-25 | |
| ደም የሚፈስሳት ሴት | 9÷20-22 | 5÷25-29 | 8÷43-48 | |
| ሁለት ዐይነ ስውሮች | 9÷27-31 | | | |
| እጁ የሰለለበት ሰው | 12÷10-13 | 3÷1-5 | 6÷6-10 | |
| በርጤሜዎስና ጓደኛው | 20÷29-34 | 10÷46-52 | 18÷35-43 | |
| ደንቆሮና ዲዳ የነበረ ሰው | | 7÷31-37 | | |
| የቤተ ሳይዳው ዐይነ ስውር | | 8÷22-26 | | |
| ሙሉ ሰውነቱ ያበጠበት ሰው | | | 14÷1-4 | |
| ዐሥር ለምጻሞች | | | 17÷11-19 | |
| የሊቀ ካህናቱ አገልጋይ | | | 22÷50-51 | |
| የሹሙ ልጅ | | | | 4÷46-54 |
| 38 ዓመታት ታሞ የኖረ ሰው | | | | 5÷1_9 |
| ዕውር ሆኖ የተወለደ ሰው | | | | 9÷1-7 |
| 2 አጋንንት የወጡላቸው ሰዎች | | | | |
| ሌጌዎንና ጓደኛው | 8÷28-34 | 5÷1-15 | 8÷27-35 | |
| ጋኔን ያደረበት ዲዳ ሰው | 9÷32-33 | | | |
| ጋኔን ያደረበት ዕውርና ዲዳ ሰው | 12÷22 | | 11÷14 | |
| የከነዓናዊቷ ሴት ልጅ | 15÷21-28 | 7÷24-30 | | |
| ጋኔን የሚጥለው ሰው ልጅ | 17÷14-18 | 9÷17-29 | 9÷38-43 | |
| ርኩስ መንፈስ ያደረበት ሰው | | 1÷23-26 | 4÷33-35 | |
| ጉባጣዋ ሴት | | | 13÷11-13 | |
| 3. በተፈጥሮ ላይ | | | | |
| ነፋስንና ባሕርን በመገሠጽ | 8÷3-27 | 4÷37-41 | 8÷22-25 | |
| በውሃ ላይ በመራመድ | 14÷25 | 6÷48-51 | | 6÷19-21 |
| 5000 ሺህ ሰዎችን በመመገብ | 14÷15-21 | 6÷35-44 | 9÷12-17 | 6÷5-13 |
| 4000 ሺህ ሰዎችን በመመገብ | 15÷32-38 | 8÷1-9 | | |
| ከዓሣ አፍ ገንዘብ በማግኘት | 17÷24-27 | | | |
| በለስን በማድረቅ | 21÷18-22 | 11÷12-25 | | |
| ዓሣ በማጥመድ | | | 5÷4-11 | |
| ውሃ ወደ ወይን በመለወጥ | | | | 2÷1-11 |
| እንደገና ዓሣ በማጥመድ | | | | 21÷1-11 |
| 4. ሙታንን በማስነሣት | | | | |
| የኢያኢሮስ ልጅ | 9÷18-25 | 5÷22–42 | 8÷41-56 | |
| የናይኗ መበለት ልጅ | | | 7÷11-15 | |
| አልዓዛር | | | | 11÷1-44 |

እንደወጡ ተጽፏል፤ 5፥16፤ 8፥7፤ 19፥12።

3. በተፈጥሮ ላይ ፦

ሐዋርያት ከወኅኒ መውጣታቸው፤ 5፥19፤ 12፥6-11

ጳውሎስ በእፉኝት አለመጐዳቱ፤ 28፥3-5

4. ሰዎችን በመቅጣት፤

ሐናንያና ሰፊራ በሞት መቀጣታቸው፤ 5፥1-11

የንጉሥ ሄሮድስ መሞት፤ 12፥20-23

የቆጵሮስ ጠንቋይ መታወሩ፤ 13፥11

የሰባቱ ልጆች ቍስል፤ 19፥14-16

5. ሙታንን በማስነሣት፤

የኢዮጴዋ ዶርቃ፤ 9፥36-41

የጢሮአዳው አውጤኪስ፤ 20፥9-12

**ተከነበለ**፤ ውሃ በብዛትና በፍጥነት ፈሰሰ፤ ወረደ፤ ተደፋ፤ ሰ.ኤ. 3፥54።

**ተካፋይ**፤ አብሮ የሚካፈል፥ አንድነት ያለው፤ ዕብ. 3፥1። በበረከት የሚካፈሉ በሥራ፥ በድካምና በመከራ አብረው መካፈል አለባቸው፤ 1ቆሮ. 9፥10-13፤ 10፥17:21፤ 2ቆሮ. 1፥7፤ ፊል. 1፥7፤ ዕብ. 3፥14፤ 12፥8:10፤ 1ጴጥ. 4፥13፤ 5፥1። ክርስቶስም ይህን አሳይቷል፤ ዕብ. 2፥14-15።

**ተክሎች**፤ እግዚአብሔር በሦስተኛው ቀን ተክሎችን ፈጠረ፤ ዘፍ. 1፥11-13። በመ.ቅ. የተጠቀሱ ተክሎች የሚከተሉት ናቸው ፦ ሒሶጵ (ሁሶፕ፤ ዘጸ. 12፥22)፥ ለውዝ (ዘፍ. 43፥11)፥ ሊብን (ዘፍ. 30፥37)፥ መርዛም ሣር (ሆሴዕ 10፥4)፥ መቃ (ማቴ. 27፥29)፥ የሚሸት እንጨት (ራእ. 18፥12)፥ ምስር (ዘፍ. 25፥34)፥ ሣር (ዘፍ. 1፥11)፥ ሮማን (መ.መ. 6፥11)፥ የሰሌን ዛፍ (ዘሌ. 23፥40)፥ ሰናፍጭ (ማቴ. 13፥31)፥ ሰንደል (2ዜ.መ. 2፥8)፥ ሱፍ (መ.መ. 2፥16)፥ ሳማ (ምሳ. 24፥31)፥ ስንዴ (ዘፍ. 30፥14)፥ ሸምበቆ (1ነገ. 14፥15)፥ የሽቱ ሣር (መ.መ. 4፥14)፥ ሽንብራ (2ሳሙ. 17፥28)፥ ሾላ (ሉቃ. 19፥4)፥ ቀረፋ (ዘጸ. 30፥23)፥ ቀይ ሽንኩርት (ዘኍ. 11፥5)፥ ቀጋ (መ.መ. 4፥14)፥ ቁጠማ (ዘጸ. 2፥3)፥ ቅል (ዮናስ 4፥6)፥ በለሳን (ዘፍ. 37፥25)፥ በለስ (ማር. 11፥13)፥ የበረሃ ቅል (የምድረ በዳ ሐረግ፤ 2ነገ. 4፥39)፥ በጢህ (ዘኍ. 11፥5)፥ ባርሰነት (ነህ. 8፥14-15)፥ ባቄላ (2ሳሙ. 17፥28:29)፥ ብርጕድ (ሕዝ. 27፥19)፥ የተልባ እግር (ኢያሱ 2፥6)፥ ተምር (ዘፍ. 43፥11)፥ ትርንጎ (መ.መ. 7፥14)፥ ነጭ ሽንኩርት (ዘኍ. 11፥5)፥ ናርዶስ (ማር. 14፥3)፥ እሆማ (ኡሁማ፤ ሆሴዕ 4፥13)፥ እሚከላ (ኢሳ. 34፥13)፥ እስታ (ኢሳ. 41፥19:20)፥ አኻያ (መዝ. 137፥2)፥ እዝሙድ (ኢሳ. 28፥25)፥ አጃ (ዘጸ. 9፥32)፥ ኤርሞን (ዘፍ. 30፥37)፥ ሬት (ዘኍ. 24፥6)፥ እሾህ (መሳ. 8፥7)፥ እንክርዳድ (ማቴ. 23፥23)፥ እንክርዳድ (ማቴ. 13፥25)፥ እንኩይ (ኢዩ. 1፥12)፥ እንግጫ (ኢሳ. 58፥5)፥ ከሙን (ኢሳ. 28፥25)፥ ከርቤ (ዘጸ. 30፥23)፥ ኩራት (ዘኍ. 11፥5)፥ ክትክታ (1ነገ. 19፥4)፥ ኮምበል (ሆሴዕ 4፥13)፥ ኲርንችት (ኢሳ. 9፥18)፥ ወይራ (ነህ. 8፥14:15)፥ ወይን (ዘኍ. 13፥23)፥ ዓልሙን (ምሳ. 7፥17)፥ ዕጣን (ዘጸ. 30፥34)፥ ዘንባባ (ዘጸ. 15፥27)፥ ዝግባ (ዘሌ. 14፥4)፥ ዘጺ (ሕዝ. 27፥15)፥ ደንገል (ኢዮብ 8፥11)፥ ዱባ (ዘኍ. 11፥5)፥ ድንብላል (ዘኍ. 11፥7)፥ ገብስ (ዘሌ. 27፥16)፥ ገውዝ (መ.መ. 6፥11)፥ ግራር (ኢሳ. 41፥19-20)፥ ጎፈር (ዘፍ. 6፥14)፥ ጕሙን (ምሳ. 15፥17)፥ የጠጅ ሣር (ዘጸ. 30፥23)፥ ጤና አዳም (ሉቃ. 11፥42)፥ ጤፍ (ሕዝ. 4፥9)፥ ጥድ (ኢሳ. 41፥19:20)፥ ጥጥ (ሆሴዕ 2፥7)፥ ጨው ጨው የሚል አትክልት (ኢዮብ 30፥4)፥ ጽጌ ረዳ (ኢሳ. 35፥1)።

**ተኲላ**፤ ሥጋ የሚበላ የቀበሮና የውሻ ዘር። በግና ፍየል እየነጠቀ የሚበላ የዱር አውሬ፤ መዝ. 91፥13፤ ማቴ. 10፥16።



**ተዘለለ**፤ ያለ ስጋት፥ ያለ ፍርሃት፥ በሰላምና በጸጥታ ኖረ፥ ተቀመጠ፤ ኤር. 23፥6።

**ተደሰተ**፤ እግዚአብሔር በሥራው (መዝ. 104፥31)፥ በሕዝቡ (ዘዳ. 10፥15፤ ዕብ. 11፥6)፥ ክርስቶስ በሚያድናቸው (ኢሳ. 53፥10-11፤ ዕብ. 12፥1-2)፥ መላእክትም ኃጢአ በሚገቡት (ሉቃ. 15፥7:10)፥ ሰዎችም በብዙ ነገር ቢደሰቱም፥ አማኞች በክርስቶስ፥ በሰማያዊ ርስታቸውና በመከራቸውም ሳይቀር ይደሰታሉ፤ ማቴ. 5፥12፤ ሉቃ. 10፥20፤ ፊል. 4፥4፤ 1ጴጥ. 1፥6-7፤ ያዕ. 1፥2-3። «ደስታ» ይመ.

**ተገዳደረ**፤ ተፎካከረ፥ ናቀ፤ 1ሳሙ. 17፥10።

**ተገጠገጠ**፤ በመስመር ተሠራ። የከተማ ቤት በአንድ ዓይነት በዝቶ ሲሠራ ተገጠገጠ ይባላል፤ መዝ. 122፥3።

**ተግሣጽ**፤ መጽሐፈ ምሳሌ ም. 25-31 ለብቻው ተነጥሎ መጽሐፈ ተግሣጽ ተብሎ ይጠራል።

የሰሎሞን መጻሕፍት ከሚባሉት ውስጥ አንዱ ነው። አምስቱ መጻሕፍትም ምሳሌ ም. 1-24፥ ተግሣጽ፥ መክብብ፥ መኃልየ መኃልይና ጥበብ ናቸው።

**ተግባረ ዕድ፤** የእጅ ሥራ። በከነዓን የነበሩ ሕዝብ እንደ ጐረቤቶቻቸው ብዙ ዓይነት የቤትና የሥራ መሣሪያ ለራሳቸው ይሠሩ ነበር። ዕብራውያንም ከልዩ ልዩ ሕዝብ ልዩ ልዩ የተግባረ ዕድ ጥበብን ቀሰሙ። ለምሳሌ የብረት ሥራን ከፍልስጥኤማውያን ተማሩ፤ 1ሳሙ. 13፥19:20። ተራው ሕዝብ ብዙ ዓይነት ተግባረ ዕድ ይችል ነበር። ሆኖም የተለየ ችሎታ ያላቸው በከተሞች ይኖሩ ነበር። የተለየ ሰፈርም ነበራቸው። ለምሳሌ ጸሓፊዎች በያቤጽ ይኖሩ ነበር (1ዜ.መ. 2፥55)፥ በኢየሩሳሌም ያጣቢዎች (2ነገ. 18፥17)፥ የሸክላ ሠሪዎችም ሰፈሮች ነበሩ፤ ማቴ. 27፥7።



በ2000 ዓመታት ከክ.በ. የአናጺ መሣሪያዎች

ሰዎች ከመጀመሪያ ጀምሮ በባልጩትና በናስ፥ እንዲሁም ባገኙት ብረት ሁሉ ይሠሩ ነበር፤ ዘፍ. 4፥22። በተለይ ብረትን ማቅለጥ ከተለማመዱ በኋላ ግን ብዙ መሣሪያዎች ነበሩአቸው፤ 1ነገ. 6፥7። በመ.ቅ. ከተጠቀሱ የተግባረ ዕድ መሣሪያዎች አንዳንዶቹ የሚከተሉት ናቸው ፦ መራጃ፥ መጥረቢያ (1ነገ. 6፥7)፥ መቅረጫ (ኢሳ. 44፥13)፥ መዶሻ (መሳ. 5፥26)፥ መጋዝ (2ሳሙ. 12፥31)፥ ምሳር (ዘዳ. 19፥5፤ 2ነገ. 6፥5)፥ ቢላዋ (ዘፍ. 22፥6)፥ ካራ (ምሳ. 30፥14)፥ ማጭድ፥ ማረሻ (ኢሳ. 2፥4)፥ ወስፌ (ዘጸ. 21፥6)፥ መርፌ (ማቴ. 19፥24)። በተግባረ ዕድ ሕይወታቸውን የሚመሩ ብዙ ዓይነት ሠራተኞች ነበሩ። በመ.ቅ. የተጠቀሱትን በሰባት አርእስት ማጠቃለል ይቻላል።

1. ወርቅና ብር ሠሪዎች። ሀ) አንጥረኞች (ዘኍ. 31፥21-23)፥ ለ) ቀራጺዎች፤ ኢሳ. 40፥19።

2. የዕንቍ ድንጋይን የሚቀርጹ፤ ዘጸ. 31፥5።

3. ብረታ ብረት ቀጥቃጮች። ሀ) ናስን፥ መዳብን፥ ቆርቆሮን፥ ብረትን፥ እርሳስን የሚያነጥሩ (ዘኍ. 31፥22:23፤ ሕዝ. 22፥18:20)፥ ለ) የሚቀርጹ፤ ኢሳ. 44፥12።

4. ድንጋይ ወቃሪዎችና ግንበኞች። (2ነገ. 12፥13)፥ የሚቀርጹ፤ ዘጸ. 28፥10:11።

5. ቤትና የቤት ዕቃ ሠሪዎች። ሀ) አናጢዎችና ጸራቢዎች (2ሳሙ. 5፥11)፥ ለ) ቀለም ቀቢዎች፤ ኤር. 22፥14።

6. ልብስ ሠሪዎች። ሀ) ፈታዮች (ዘጸ. 35፥25:26)፥ ለ) ሸማኔዎች፤ ዘጸ. 35፥35። ሐ) አጣቢዎች (2ነገ. 18፥17)፥ መ) ቀለም አግቢዎች (2ዜ.መ. 2፥7)፥ ሠ) ጠላፊዎች፤ ዘጸ. 35፥35።

7. ልዩ ልዩ ባለሙያዎች። ሸክላ ሠሪ (ኤር. 18፥3)፥ ቀማሚ (ዘጸ. 30፥22-38)፥ ቁርበት ፋቂ (ሐ.ሥ. 9፥43)፥ ቀንድ አንጣጪ፤ መ.መ. 7፥3።



ጥንታዊ የሴቶች ተግባረ ዕድ

**ተፈጥሮ፤** የተፈጠረ፥ የአንድ ነገር መጀመሪያ ባሕርይ፤ ሮም 11፥24። «ፍጥረት» ይመ.

**ቱሚም፤** «ኡሪም» ይመ.

**ቱንቢ፤** ሕንጻ በትክክል መቆሙ የሚለካበት ድንጋይ፥ ወይም ብረት የታሰረበት ክር። በምሳሌነት የሕዝብ ጠባይ የተፈተነ መሆኑን ያመለክታል፤ 2ነገ. 21፥13፤ ኢሳ. 28፥17፤ አሞጽ 7፥7-9።



ቱንቢ ግንብ ሲሠራበት

**ቲቶ፤** ቲቶ እንደ ጢሞቴዎስ ለሐዋርያው ጳውሎስ የመንፈስ ቅዱስ ልጁ ነው። በሐዋርያት ሥራ ውስጥ ስሙ አልተጠቀሰም፤ ቢሆንም የግሪክ ሰው መሆኑ፥ እንደዚሁም ጳውሎስና በርናባስ በአይሁድ ክርክር ምክንያት ወደ ኢየሩሳሌም በወጡ ጊዜ ቲቶ አብሮአቸው መሄዱ ተገልጿል፤ ሐ.ሥ. 15፥1:2፤ ገላ. 2፥1-3። ቀጥሎም ድሆች ለሆኑት ቅዱሳን ገንዘብ ለመሰብሰብ ቲቶ ወደ ቆሮንቶስ ተልኳል። በኋላም በቆሮንቶስ ቤ.ክ. ለተፈጠረው ችግር ጢሞቴዎስ ተልኮ ሳይሳካ በመቅረቱ ቲቶ እንዲሆን ተደርጓል፤ 2ቆሮ. 7፥5-7:13:14፤ 8፥6:16-24። ስለ ቲቶ የምናውቀው የመጨረሻ አሳብ ቤ.ክ.ን ያደራጅ ዘንድ ጳውሎስ በቀርጤስ የተወው መሆኑን ነው፤ ቲቶ 1፥5:6። ወደ ኒቆጵልዮን እንዲሄድ ጳውሎስ ነግሮት ነበር፥ የሄደ ስለ መሆኑ ግን የሚታወቅ ነገር የለም። ሐዋርያው በጻፈው የመጨረሻ መልእክቱ ላይ «ወደ ድልማጥያ ሄዶአል» ይላል፤ ቲቶ 3፥12፤ 2ጢሞ. 4፥10። «ጳውሎስ፤ እስራቱ» ይመ.

**ወደ ቲቶ የተላከ መልእክት፤** ቅዱስ ጳውሎስ ለጢሞቴዎስ የመጀመሪያ መልእክቱን ሲጽፍ በ63 ዓ.ም. ገደማ ወደ ቲቶም ጽፏል። የቀርጤስ ሰዎች አጉል ጠባያቸውን እንደያዙ ወደ ቤ.ክ. ገብተው ነበርና ቲቶ ጠንካራና አስተዋይ ሰው በመሆን እነዚህን ሰዎች መቈጣጠር ነበረበት፤ 1፥10-12፤ 2፥15፤ 3፥9-11። በዚህም መልእክት ሐዋርያው ፦ ሀ) በቤ.ክ. ሽማግሌዎች የብቃት መስፈርት (1፥5-9)፥ ለ) መልካም ሥራ (1፥16፤ 2፥7-8:14፤ 3፥1:8:14)፥ ሐ) መልካም ሥራን ለመሥራት በአጫጭር አንቀጾች በተሰጠ ትምህርተ መለኮት ላይ አተኩሯል፤ 2፥11-14፤ 3፥4-7።

አከፋፈል ፦

1. ቲቶ በቀርጤስ የቤ.ክ.ን አስተዳደር የማስተካከሉ ኀላፊነት፤ ም. 1።

2. ቲቶ በቤ.ክ. መሪነት መልካም አርአያ የማሳየቱ አስፈላጊነት፤ ም. 2።

3. ቲቶ ግብረ ገብነትን በጥንቃቄ የማስተማሩ ጠቃሚነት፤ ም. 3።

**ቲኪቆስ፤** የተወደደና የታመነ የጳውሎስ ጓደኛ፤ ሐ.ሥ. 20፥4፤ ኤፌ. 6፥21:22፤ ቆላ. 4፥7-9፤ 2ጢሞ. 4፥12፤ ቲቶ 3፥12።

**ታላንት፤** የሮም መንግሥት የክብደት መለኪያ፤ ራእ. 16፥21። «ክብደት» ይመ.

**ታማኝ፤** ቃሉን የሚፈጽም፥ እንደጠባዩ የሚኖር። እግዚአብሔር ታማኝ ነው፤ ክርስቲያን ታማኝ መሆን ይገባዋል፤ 2ቆሮ. 1፥18፤ 2ጢሞ. 2፥2:11-13፤ ያዕ. 5፥12። ሰው በጥቂት ነገር ላይ ኀላፊነት ሲሰጠው ታማኝ እንዲሆን ያስፈልጋል፤ ሉቃ. 12፥42፤ 16፥10:11።

**ታሸበ፤** ተጌጠ፤ ተለበጠ፤ ሕዝ. 27፥6።

**ታቦር፤** ከገሊላ ባሕር በምዕራባዊ ደቡብ በኩል 10 ኪ.ሜ. ርቆ የሚገኝ ተራራ። ተራራው እስከ 572 ሜትር ከባሕር ጠለል (ወለል) ከፍ ይላል። ባርቅ ሲሣራን በታቦር አሸነፈ፤ መሳ. 4፥6-14። ሳኦል በሳሙኤል ትንቢት መሠረት ከ3 ሰዎች ጋር በታቦር ተገናኘ፤ 1ሳሙ. 10፥3። ክርስቶስ በዚህ ተራራ ላይ ክብሩን እንደገለጠ ብዙ ክርስቲያኖች ያምናሉ፤ ማቴ. 17፥1-8። ታቦር በዛብሎን ዕጣ ውስጥ ያለ ለሜራሪ ልጆች የተሰጠ ቦታ ነው፤ 1ዜ.መ. 6፥77። ካ. 5ለ። «አርሞንዔም» ይመ.

**ታቦት፤** ሙሴ ከግራር እንጨት ታቦትን እንዲሠራ ታዘዘ። አሠራሩም ሣጥን ዓይነት ነበረ። ርዝመቱ 125፥ ወርዱም 75፥ ቁመቱ 75 ሳንቲ ሜትር ያህል ነበረ። ታቦቱ በወርቅ የተለበጠ፥ መከደኛውም ከወርቅ የተሠራ ነበር፤ በላዩም ሁለት ኪሩቤል ተቀርጸዋል። የታቦቱ አገልግሎት 1. ዐሠርቱ ቃላት የተጻፉባቸው የሁለቱ ጽላት ማኖሪያ፥ 2. ከእስራኤል መሪዎች ጋር የእግዚአብሔር መገናኛ ነበረ። ስለዚህ ታቦቱ እግዚአብሔር ከሕዝቡ ጋር የመኖሩ ምልክት ነበር፤ ዘጸ. 25፥1-22፤ 40፥20። ሙሴ ታቦቱን አሠርቶ ሲያበቃ በመገናኛው ድንኳን ውስጥ አኖረው። የእስራኤልም ሕዝብ ይዘውት ይጓዙ ነበር። በተለይም ዮርዳኖስን ሲሻገሩና ኢያሪኮን ሲዞሩ ካህናት ተሸክመውት ፊት ፊት ይሄዱ ነበር፤ ኢያሱ 3፥6። የእስራኤል ሕዝብ ከኃጢአታቸው ሳይመለሱ በጦርነት እንደ መከላከያ መጠሪያ ሲሸከሙት፥ ታቦቱ በመሳፍንት ዘመን በፍልስጥኤማውያን ተማረከ። ታቦቱ በእግዚአብሔር ስም የተጠራ ስለነበረ፥ እግዚአብሔር በፍልስጥኤማውያን ላይ ብዙ ተአምር አደረገ፤ ፍልስጥኤማውያንም መለሱት፤ 1ሳሙ.



4-6። በኋላም ዳዊት ወደ ኢየሩሳሌም አመጣው። ሲያመጣውም ዖዛ የተባለው ሰው በድፍረት ስለነካው ተቀሠፈ (2ሳሙ. 6)፥ ሰሎሞንም ራሱ በሠራው ቤተ መቅደስ አኖረው፤ 1ነገ. 8። ታቦቱ በኢዮስያስ ዘመን በቤተ መቅደስ ነበረ፤ 2ዜ.መ. 35፥3። በዚያን ጊዜ ነቢዩ ኤርምያስ ወደፊት የእስራኤል ሕዝብ ስለ ታቦቱ ምንም እንደማያስብ ትንቢት ተናገረ፤ ኤር. 3፥16። ናቡከደነፆር ኢየሩሳሌምን ሲያፈርስ ታቦቱ የጠፋ ይመስላል። ምክንያቱም ዘሩባቤል በሠራው ቤተ መቅደስ ታቦት አልነበረምና። በአ.ኪ. የቃል ኪዳኑ ታቦት በእግዚአብሔር ሰማያዊ መቅደስ እንደታየ ተጠቅሷል፤ ራእ. 11፥19።

**ታች፥ በታች፤** «ላይ፥ በላይ» ይመ.

**ታነቀ፤** በገመድ ወይም በሌላ ነገር ታንቆ መሞት። አኪጦፌል በገዛ እጁ ታንቆ ሞተ፤ 2ሳሙ. 17፥23። ይሁዳም ታንቆ ሞተ፤ ማቴ. 27፥5። በወጥመድም ሆነ በሌላ ዓይነት ዘዴ ታንቆ የተገደለ የእንስሳ ሥጋ እንዳይበላ ሐዋርያት በጉባኤአቸው ውሳኔ ከለከሉ፤ ሐ.ሥ. 15፥20።

**ታካች፤** ለመሥራት የማይወድ ደካማ፥ ሰነፍ። መተኛት ይወዳል፤ እንዳይሠራ ምክንያት ይፈጥራል፤ ይኰራል፤ ከጠባዩም መጥፎነት የተነሣ የፈለገውን አያገኝም፤ ምሳ. 6፥6-11፤ 10፥26፤ 13፥4፤ 20፥4፤ 21፥25፤ 22፥13፤ 26፥14-16።

**ታዳጊ፤** «መድኃኒት» ይመ.

**ታዴዎስ፤** ከሐዋርያት አንዱ ነው፤ ማቴ. 10፥3። በሉቃስ 6፥16 እና በሐ.ሥ. 1፥13 «የያዕቆብ ልጅ ይሁዳ» ተብሎ ተጠርቷል። «ይሁዳ» ይመ.

**ቴልጌልቴልፌልሶር፤** ቴግላት ፐሌሴር፤ ከ745-727 ከክ.ል. የነገሠ የአሦር ንጉሥ። ደግሞም ፎሐ ተብሎ ይጠራል። ከእስራኤል ንጉሥ ከምናሔም ገንዘብ ተቀበለ። በኋላም በፋቁሔ ዘመን ከእስራኤል ብዙ ሰዎችን ወደ አሦር አፈለሰ፤ 2ነገ. 15፥19:20:29። ይሁዳን ለመርዳት እስራኤልንና ሶርያን እንዲቃወም ከአካዝ ገጸ በረከት ተቀበለ። ሆኖም አልረዳውም፤ 2ነገ. 16፥5-10፤ 2ዜ.መ. 28፥16-21። ሥዕሉን በገጽ 130 ይመ.



ከድንጋይ ቅርጽ የተገኘ የቴልጌልቴልፌልሶር ሥዕል

**ቴርሳ፤** ከሰማርያ በስተምሥራቅ 10 ኪ.ሜ. ርቆ የሚገኝ ከተማ። ለተወሰኑ ዓመታት የሰሜን መንግሥት መናገሻ ከተማ ነበር፤ 1ነገ. 15፥21፤ 16፥9-24። ካ. 4ሀ።

**ቴቁሔ፤** ከቤተ ልሔም በስተደቡብ 8 ኪ.ሜ. ርቆ የሚገኝ ከተማ። ኢዮአብ ዳዊትንና አቤሴሎምን ለማስታረቅ ከቴቁሔ ብልሀተኛ ሴት አስመጣ፤ 2ሳሙ. 14፥2። ቴቁሔ የአሞጽ ከተማ ነበረ፤ አሞጽ 1፥1።

**ቴዎፍሎስ፤** «የእግዚአብሔር ወዳጅ» ማለት ነው። ሉቃስ ወንጌሉንና የሐዋርያትን ሥራ የጻፈው ለቴዎፍሎስ ነው፤ ሉቃ. 1፥1፤ ሐ.ሥ. 1፥1።

**ትሎት፤** ፐሎሽ፥ በጋብቻ ጊዜ የሴቲቱ ወላጆች ለእርስዋ የሚያበረክቱት ስጦታ፤ 1ነገ. 9፥16። «አጪ» ይመ.

**ትሑት፤** ራሱን የሚያዋርድ፤ ያዕ. 4፥6። «ትሕትና» ይመ.

**ትሕትና፤** ራስን ዝቅ ማድረግ፥ ሌላው ሰው እንዲጠቀም መፈለግ፥ ከራስ ይልቅ ሌላ ሰው እንደሚሻል መቍጠር። እግዚአብሔር ትሕትናን ይወዳል፤ 2ዜ.መ. 7፥14፤ ምሳ. 15፥33፤ 18፥23፤ 22፥4፤ ያዕ. 4፥6። ሙሴ እጅግ ትሑት ሰው ነበረ፤ ዘኁ. 12፥3። ክርስቶስ ፍጹም ትሑት ነው፤ ማቴ. 11፥28-30፤ ዮሐ. 13፥1-20፤ ፊል. 2፥1-11፤ 2ቆሮ. 8፥9። ትሕትናንም ያመሰግናል፤ ማቴ. 23፥12። አማኞች በትሕትና እንዲመላለሱ ታዝዘዋል፤ 1ጴጥ. 3፥8፤ 5፥5:6፤ ሮም 12፥16፤ ፊል. 2፥3:4። ጳውሎስ ከአስመሳይ ትሕትና እንድንጠበቅ ያስጠነቅቀናል፤ ቆላ. 2፥18:23።

**ትምህርት፤** «አስተማሪ» ይመ.

**ትምክህት፤** የሠሩትን ሥራ ማጋነን፥ ራስን ማክበር፥ በሥራ፥ በኃይልና በችሎታ መታመን፥ ራስንም ማመስገን። ሰው በጌታ እንጂ በራሱ መመካት አይገባውም፤ ኤር. 9፥23:24፤ 2ቆሮ. 10፥15-18፤ 11፥10-12፥11፤ ገላ. 6፥14፤ ኤፌ. 2፥9።

**ትሥጉት፤** ሥጋ መሆን፥ ሥጋን መዋሐድ። ከዘለዓለም የነበረ እግዚአብሔር ቃል ከቅድስት ድንግል ማርያም ሥጋና ነፍስ ነሥቶ ሰው ሆነ፤ ዮሐ. 1፥14፤ ገላ. 4፥4፤ ዕብ. 2፥14:15። ሥጋን በነሣ ጊዜ ባሕርዩ ወይም መለኮቱ አልተለወጠም። ሥጋ ሆነ ሲባልም የሰውነትን ባሕርይ ሁሉ ገንዘብ አደረገ ማለት ነው፤ ዕብ. 2፥17:18፤ 4፥15። ስለዚህ ክርስቶስ ፍጹም አምላክ፥ ፍጹም ሰው ነው። «ኢየሱስ»፥ «ወልድ»፥ «ሥላሴ» ይመ.

**ትርጓሜ፤** ስለ እግዚአብሔር ቃል ትርጕም ብቻ ሳይሆን ሐተታና ማብራሪያ ያለበት፤ 2ጴጥ. 1፥20-21። በሕልም የሚገኘው የምሥጢር ፍች፤ ዘፍ. 40፥5-8።

**ትርጕም፤** ቃል ከተገለጸበት አንድ ቋንቋ ወደ ሌላ ቋንቋ ሲለወጥ የሚኖረው አሳብ፤ ዕዝ. 4፥18፤ ዮሐ. 1፥42፤ 1ቆሮ. 12፥10፤ 14፥27:28።

**ትናጋ፤** በጉረሮ ውስጥ ላይኛው ክፍለ አካል፤ ላንቃም ይባላል፤ ሰ.ኤ. 4፥4፤ ሕዝ. 3፥26።

**ትንሣኤ፤** ትንሣኤ ማለት ከሞት በኋላ በነፍስ ብቻ ሳይሆን፥ በሥጋና በነፍስ ሕይወት ማግኘት ማለት ነው።

<u>ትንሣኤ በብሉይ ኪዳን፤</u>

አንዳንድ ጥቅሶች ሰዎች በሥጋ እንደሚነሡ ያሳያሉ፤ መዝ. 16፥9-11፤ ኢሳ. 26፥19፤ ዳን. 12፥2። ሰዱቃውያን በትንሣኤ አያምኑም፤ ክርስቶስ ግን ብ.ኪ.ን በመጥቀስ ስሕተታቸውን አጋለጠ፤ ማቴ. 22፥23-33።

<u>የኢየሱስ ትንሣኤ፤</u>

ጌታ ከተገለጠላቸው በኋላ ሐዋርያት በኢየሱስ ትንሣኤ አልተጠራጠሩም፤ ትንሣኤው ዋና የስብከታቸው መሠረት ነበረ፥ ከዚህም የተነሣ መከራን ተቀበሉ፤ ሐ.ሥ. 4፥1-3። ትንሣኤውን በሦስት ነገሮች አረጋገጡ ፦

ሀ) ብሉይ ኪዳን፤ ሐ.ሥ. 2፥25-28። ኢየሱስም ራሱ አስቀድሞ ስለ ትንሣኤው ተናግሮ ነበር፤ ማር. 8፥31፤ 9፥30:31፤ 10፥34፤ 14፥28፤ ዮሐ. 2፥19-21።

ለ) ምንም እንኳን ጠባቂ ዘብ ቢደረግበትም፥ መቃብሩ ባዶ ሆኖ ተገኘ፤ ማቴ. 27፥62-28፥15፤ ዮሐ. 20፥1-10።

ሐ) ኢየሱስ በአርባ ቀን ውስጥ ለወንዶችና ለሴቶች፥ ለብዙ ሰዎችም በአንድነትና በየግላቸው፥ በቀንና በሌሊት፥ በቤትም በውጭም እየታየ ተናገረ፤ ተራመደ፤ ተዳሰሰ፤ ከእነርሱም ጋር በላ። ከተገለጠባቸው ጊዜያት መካከል ዐሥሩ እንዲህ ተዘርዝረዋል ፦

1-5. በተነሣበት ዕለት ለመግደላዊት ማርያም (ዮሐ. 20፥11-18)፥ ለሴቶች (ማቴ. 28፥9:10)፥ ለጴጥሮስ (ሉቃ. 24፥34፤ 1ቆር. 15፥5)፥ ለቀለዮጳና ለሌላው ሰው በኤማሁስ መንገድ (ሉቃ. 24፥13-35)፥ ከቶማስ በቀር ለሐዋርያት በአንድነት ታየ፤ ሉቃ. 24፥36-43፤ ዮሐ. 20፥19-25።

6. በስምንተኛው ቀን ለሐዋርያት ሁሉ ታየ፤ ዮሐ. 20፥26-29።

7. ከዚያም በኋላ ለሰባቱ ሐዋርያት በገሊላ ባሕር ዳር፤ ዮሐ. 21።

8. ለአምስት መቶ ሰዎች፤ ማቴ. 28፥16-20፤ 1ቆሮ. 15፥6።

9. ለያዕቆብ ታየ፤ 1ቆሮ. 15፥7።

10. ሲያርግ ለሐዋርያት ታየ፤ ሉቃ. 24፥44-53፤ ሐ.ሥ. 1፥6-11፤ 1ቆሮ. 15፥7።

11. ካረገ በኋላ ለጳውሎስ በደማስቆ መንገድ ታየ፤ ሐ.ሥ. 9፥1-9፤ 1ቆሮ. 15፥8።

ትንሣኤው ኢየሱስ የእግዚአብሔር ልጅ መሆኑን፥ ምእመናንም በእርሱ መጽደቃቸውን ያረጋግጣል፤ ሮም 1፥3:4፤ 4፥25።

<u>የትንሣኤ ሁኔታ፤</u>

ሙታን በአዲስ ሁኔታ ይነሣሉ። ኢየሱስ ከተነሣ በኋላ ታየ፤ ተሰወረ። ወደ ላይ በማረጉ፥ ወደ ተቆለፈ ቤትም በመግባቱ፥ በዚህ ዓለም ሕግ አለመወሰኑ ተገልጿል፤ ሉቃ. 24፥31:51፤ ዮሐ. 20፥19። ነገር ግን መንፈስ ብቻ አልነበረም፤ የችንካሩ ምልክቶች ነበሩበት፤ ሰዎች ዳሰሱት፤ በፊታቸውም መብልን በላ። ጳውሎስ ስለ ትንሣኤ ሁኔታ በ1ቆሮ. 15፥35-50 በሰፊው ያስተምራል። ሰው ከተነሣ በኋላ አካል ይኖረዋል፤ አካሉ ግን መንፈሳዊና የማይበሰብስ ይሆናልና ሥጋዊ ነገር አያስፈልገውም፤ ማቴ. 22፥30። ምእመናን በትንሣኤ ጊዜ እንዴት እንደሚሆኑ ሙሉ በሙሉ ገና አያውቁም፤ ነገር ግን ሥጋቸው የኢየሱስን ሥጋ እንዲመስል ይለወጣል፤ ፊል. 3፥21፤ 1ዮሐ. 3፥2። በክርስቶስ ዳግም ምጽአት መልካም ያደረጉ ለሕይወት ትንሣኤ፥ ክፉ ያደረጉ ደግሞ ለፍርድ ትንሣኤ ይነሣሉ፤ ዮሐ. 5፥28:29፤ 1ተሰ. 4፥13-18፤ ራእ. 20፥11-15። አማኝ በምድር ላለ በክርስቶስ ሆኖ የትንሣኤው ተካፋይ ሆኗልና በአዲስ ሕይወት ይኖራል፤ ሮም 6፥4-11፤ ቆላ. 3፥1። ይህም «ፊተኛው ትንሣኤ» ይባላል። «ሺህ ዓመት» ይመ.

**ትንቢት፤** ነቢያት ያስተማሩት ትምህርት ትንቢት ተብሏል፤ ነቢያት ሕዝቡን ሁሉ ከነበረበት ሁኔታ ለማላቀቅ በእግዚአብሔር ስም የተናገሩት የወቀሳም ሆነ የማጽናኛ ቃል ነው። ይህም ገና ያልተፈጸመውንና እንደየወቅቱ ሁኔታ የተሰጠውን የእግዚአብሔር ቃል ያጠቃልላል፤ 2ጴጥ. 1፥19-21። እግዚአብሔር በብዙ ዓይነትና በብዙ መንገድ በነቢያት በኩል ተናገረ፤ ዕብ. 1፥1። ነገሮች ሲተነበዩ መሠረታዊ ሁኔታቸው እንጂ በጋዜጣ እንደሚጻፉ ድርጊቶች አይደሉም። ስለዚህ ትንቢት ከመፈጸሙ በፊት እንዴት እንደሚሆን አይታወቅም፤ ከተፈጸመ በኋላ ግን ድርጊቱ የትንቢቱ ፍጻሜ መሆኑን የእግዚአብሔር ሰዎች ያስተውላሉ። የአ.ኪ. ጸሐፊዎች «በነቢይ ... የተባለው ይፈጸም ዘንድ ይህ ሁሉ ሆነ» እያሉ ደጋግመው ብ.ኪ.ን ይጠቅሳሉ፤ ማቴ. 1፥21-23፤ 1ጴጥ. 1፥10-12።

የትንቢትን ቃል መተርጐም ከባድ ነው፤ ሆኖም የሚከተሉትን ነገሮች ማስተዋል ይረዳል ፦

1. ነቢይ እንደ ሰሚዎች ሁኔታና ዕውቀት ይናገራል፤ የትንቢት ፍጻሜ ግን እንደሚፈጸምበት ዘመንና ሁኔታ የሚታይ ነው። ለምሳሌ ስለ ዳዊት ድንኳን የተተነበየው አሕዛብ ባሉባት በቤ.ክ. ተፈጸመ። መሠረታዊው ነገር የእግዚአብሔር ሕዝብ በረከት ነው፤ አሞጽ 9፥11፤ ሐ.ሥ. 15፥14-19።

2. አንዳንድ ጊዜ ትንቢት ቃል በቃል ሳይሆን መሠረታዊ ግቡን ተመርኵዞ ሊፈጸም ይችላል። ለምሳሌ ስለ ኤልያስ የተተነበየው በመጥምቁ ዮሐንስ ተፈጸመ። መሠረታዊው ነገር ሕዝብን ለእግዚአብሔር ማዘጋጀት ነው፤ ሚል. 4፥5፤ ማቴ. 17፥10-12።

3. ትንቢት ከአንድ በላይ በሆነ ጊዜ ወይም መንገድ ሊፈጸም ይችላል። ለምሳሌ ከቤቱ ንጉሥ እንዳይጠፋ ለዳዊት የተሰጠ ተስፋ መጀመሪያ በሰሎሞን በኋላም በኢየሱስ ክርስቶስ ተፈጸመ፤ 2ሳሙ. 7፥12-17፤ ራእ. 22፥16።

4. በአንድ ትንቢት ውስጥ የሚገኙ ነገሮች በተለያዩ ጊዜያት ሊፈጸሙ ይችላሉ። ለምሳሌ የክርስቶስ የመጀመሪያና የሁለተኛ መምጣት (ኢዩ. 2:28-32)፥ የኢየሩሳሌም ውድቀትና የዓለም መጨረሻ፤ ማቴ. 24፥1-3:15-31።

5. ስለ ሰው የተነገረ ትንቢት በሰው አድራጎት ሊቀር ይችላል፤ ኤር. 18፥7-10። ለምሳሌ የነነዌ ሰዎች ንስሐ ስለገቡ የዮናስ ቃል አልተፈጸመም፤ ዮናስ 3፥4:10። «ነቢይ» ይመ.

6. በቤ.ክ. ትንቢትና መገለጥ በሥርዓት መነገር ስላለበትና ቤ. ክ. በንቃቱ መመርመር የሚገባት ስለመሆኗ ሐዋርያው ጳውሎስ በሰፊው ጽፏል፤ 1ቆሮ. 14፤ 1ተሰ. 5፥19-21።

**ትንኝ፤** የምትበርር፥ የሰውን ደም የምትመጥ በጣም ትንሽ ፍጥረት፤ ማቴ. 23፥24።

**ትእዛዝ፤** ዘፍ. 2፥16። «ሕግ» ይመ.

**ትእዛዝ**፤ 71 ወይም 72 ቀኖና (አንቀጽ) ያለበት የሲኖዶስ መጽሐፍ ክፍል። «ሲኖዶስ» ይመ.

**ትኩሳት**፤ እንደ ንዳድ ያለ በሽታ፤ ዘሌ. 26፥16። «በሽታ» ይመ.

**ትካዜ**፤ ጽኑ ኀዘን፥ ጭንቀት። ትካዜ ብዙ ከማሰብና ከመመርመር ሊመጣ ይችላል፤ መክ. 1፥18፤ 2፥23። የልብ ዕረፍት ከማጣት የተነሣም ትካዜ በሰው ላይ ይደርሳል፤ ኢዮብ 30፥28።

**ትውልድ**፤ 1. የአንድ ሰው ታሪክና ከእርሱ የተወለዱ ሰዎች ስም ታሪክ፤ ዘፍ. 5፥1፤ 6፥9። 2. በተራ የሚቈጠር የዘር አወራረድ፤ ማቴ. 1፥17። 3. በአንድ ዘመን የሚኖሩ ሁሉ፤ መሳ. 3፥2። 4. በአንድ አሳብ የሚመራ ሕዝብ፤ ማቴ. 16፥4።

**የትውልድ ሐረግ**፤ ከላይ ወደ ታች፥ ከታች ወደ ላይ የሚቈጠር የዘር ስም ዝርዝር። የትውልድ ሐረግ፥ ሰዎች ከማን እንደተወለዱ፥ የርስት መብታቸውን፥ የማዕረግ ወይም የሹመት ቅደም ተከተላቸውን፥ የወገንና የነገድ ግንኙነታቸውን ሊያሳይ ይችላል። በመ.ቅ. ብዙ የትውልድ ሐረግ አለ፤ በተለይ የአዳም (ዘፍ. 5)፥ የኖኅ (ዘፍ. 10)፥ የሴም (ዘፍ. 11፥10-32)፥ የያዕቆብ (ዘፍ. 46፥8-27)። የእስራኤል ትውልድ ሐረግ እስከ ባቢሎን ምርኮ በ1ዜ.መ. 1-9 ይገኛል፤ ከባቢሎን ምርኮ በኋላ የተመለሱት የትውልድ ሐረግ በዕዝ. 2፥1-63፤ 8፥1-20፤ ነህ. 7፥7-63 ተጽፏል።

ማቴዎስ የክርስቶስን ትውልድ ሐረግ ከአብርሃም ጀምሮ ይዘረዝራል፤ ማቴ. 1፥1-17። ይህም በሦስት ክፍል የተከፈለ ሲሆን፥ እያንዳንዱ ክፍል ዐሥራ አራት ትውልድ ይገኝበታል። ማቴዎስ ከአይሁድ ደምብ ውጭ አምስት ሴቶችን በትውልድ ሐረጉ ውስጥ ጽፏል፤ ከኢዮራም በኋላ ሦስት ትውልድ፥ ማለትም አካዝያስን፥ ኢዮአስንና አሜስያስን አልጻፋቸውም፤ ማቴ. 1፥8፤ 1ዜ.መ. 3፥11:12። በሐረግ ውስጥ «ወለደ» ወይም «ልጅ» የሩቅ ግንኙነትን ወይም የወራሽነትን መብት ሊያመለክት ይችል ነበር።

ሉቃስ የክርስቶስን ትውልድ ሐረግ እስከ አዳም ድረስ ጻፈ፤ ሉቃ. 3፥23-38። ከአዳም እስከ አብርሃም ያለው የትውልድ ሐረግ ከ1ዜ.መ. 1፥1-4:24-28 ጋር ይስማማል። የሉቃስ ሐረግ አቈጣጠር ከአብርሃም እስከ ዳዊት ድረስ ከማቴዎስ ጋር ይገናኛል። ከኢየሱስ እስከ ዳዊት ድረስ ግን ይለያያል። ልዩነቱ በምን ምክንያት እንደሆነ አልተገለጠም። የሆነው ሆኖ ሉቃስ በሥጋ ትውልድ ሐረግ፥ ማቴዎስ ደግሞ በሕግና በመብት ትውልድ ሐረግ ላይ ያተኰሩ ይመስላል። በኢየሱስ ትውልድ ሐረግ የታወቁ ዋና ዋና ሰዎች የሚከተሉት ናቸው ፦




**ትዕቢት**፤ ኵራት፥ የትሕትና ተቃራኒ። እግዚአብሔር ስለሚቃወማቸው ትዕቢተኞች ይወድቃሉ፤ ምሳ. 8፥13፤ 16፥18፤ 21፥4:24፤ ኢሳ. 13፥11፤ 1ጢሞ. 3፥6፤ 1ጴጥ. 5፥5፤ ያዕ. 4፥16። «ኵራት»፥ «ትምክህት» ይመ.

**ትዕቢት (የዮርዳኖስ)**፤ በክረምት ጊዜ የውሃውን ሙላት ያመለክታል። ውሃው ሞልቶ በዳርና በዳር ሲፈስ ጫካው ትልቅ ይሆናል፤ አውሬዎችም ከአካባቢው ይወጣሉ፤ ኤር. 12፥5፤ 49፥19።

**ትዕግሥት**፤ መቻል። ትዕግሥት ያለው ሰው ለረጅም ጊዜ በመከራ ይጸናል፤ ተስፋ ያደርጋል፤ ምሕረትንም ያሳያል። እግዚአብሔር ለሰዎች ብዙ ትዕግሥት አሳይቷል፤ ሮም 2፥4፤ 15፥5፤ 1ጴጥ. 3፥20። በእግዚአብሔርና በሰው ዘንድ ትዕግሥት የተመሰገነ ነው፤ ያዕ. 5፥11። ትዕግሥት የመንፈስ ፍሬ ነው፤ ገላ. 5፥22። ታጋሹም በፈተና ይጸናል፤ ሮም 5፥3-4፤ ያዕ. 1፥2-4።

**ትያጥሮን**፤ እስያ በተባለች በሮም ክፍል አገር የምትገኝ ከተማ። በዚች ከተማ ይሠራ የነበረው ቀይ ሐርና ጥሩ ቀለም ያለው ልብስ በሌሎች አገሮች ዘንድ የታወቀ ሆነ፤ ሐ.ሥ. 16፥14። ጳውሎስ በኤፌሶን ሳለ ቤ.ክ. በዚች ከተማ የተመሠረተች ይመስላል፤ ሐ.ሥ. 19፥10፤ ራእ. 1፥11፤ 2፥18-29። ዛሬ አኪሳር የሚባል ትልቅ ከተማ በቦታው ላይ ይገኛል። ከ. 7ሰ። «ኤልዛቤል» ይመ.

**ትጋት**፤ ንቃት፥ የሌሊት ዘብ፥ ያለ እንቅልፍ መጠበቅ። ሌሊቱን አይሁድ በሦስት፥ ሮማውያን ደግሞ በአራት ክፍለው ጠባቂዎችን ያቆሙ ነበር፤ እነዚህም ክፍሎች በመ.ቅ. ትጋቶች ተብለው ይጠራሉ፤ መሳ. 7፥19፤ ማር. 6፥48። ምእመናን እንዳይወድቁ በትጋት እንዲጸልዩ ታዝዘዋል፤ ማር. 13፥33፤ ሉቃ. 21፥36፤ ኤፌ. 6፥18፤ ቆላ. 4፥2።

**ትግል**፤ በመ.ቅ. በጨዋታና በውድድር ባይጠቀስም፥ በሰዎች መካከልና በመንፈሳዊ ዓለም ላሉ ግጭቶች ምሳሌ ሆኗል፤ ዘፍ. 30፥8፤ 32፥24፤ ኤፌ. 6፥12፤ 2ጢሞ. 2፥5።

**ቶማስ**፤ ከዐሥራ ሁለቱ ሐዋርያት አንዱ፤ ማቴ. 10፥3። ቶማስ በአራማይክ፥ ዲዲሞስ በግሪክ ሲሆን፥ ትርጉሙ መንታ ማለት ነው፤ የግል ስሙ አልተገለጠም፤ ዮሐ. 20፥24። ክርስቶስን ሲከተል ተስፋ መቁረጥን የሚያስከትል ድፍረት (ዮሐ. 11፥8-16)፥ አለማስተዋል (ዮሐ. 14፥5)፥ መጠራጠርም (ዮሐ. 20፥24-25) ይታይበት ነበር። ከትንሣኤ በኋላ ግን የክርስቶስን ጎን በመዳሰስ በእርሱ ላይ የተፈጸመበትን ከተረዳ በኋላ «ጌታዩ አምላኪ» ብሎ ወደ ሙሉ እምነት ደርሷል፤ ዮሐ. 20፥26-29። በቤ.ክ. ታሪክ በፋርስና በሕንድ ወንጌልን እንዳስተማረ ይነገራል። «ሐዋርያ» ይመ.

**ቶጳዝዮን**፤ የሚያብለጨልጭ ቢጫ ዓይነት የከበረ ድንጋይ፤ ዘጸ. 28፥17፤ ሕዝ. 28፥13።

**ቶፌት**፤ ልጆች ለሞሎክ የተቃጠሉበት፥ በሄኖም ሸለቆ የሚገኝ የመስገጃ ቦታ። ኢዮስያስ መስገጃውን ካፈረሰው በኋላ ቦታው የመቃብር ስፍራ ሆነ፤ 2ነገ. 23፥10፤ ኤር. 7፥31-34።

**ችል ማለት**፤ ተገቢውን አለማድረግ፥ በተለይ በመንፈሳዊ ስጦታ አለመጠቀም፤ 1ጢሞ. 4፥14፤ ዕብ. 2፥3።

**ቸርነት**፤ በደግነት፥ በለጋስነት የመስጠት ሁኔታ። እግዚአብሔር አስቀድሞ ለሰው ቸርነትን አሳይቷል፤ መዝ. 33፥5፤ ሮም 2፥4። ቸርነት መንፈስ ቅዱስ በአማኝ ሕይወት የሚያፈራው ፍሬ ነው፤ ገላ. 5፥22፤ ቆላ. 3፥12።

**ችንፌር**፤ እንደ መቅሠፍት ያለ ክፉ ነገር። ብዙ ጊዜ ተላላፊ በሽታን ያመለክታል፤ ዘጸ. 5፥3፤ 2ሳሙ. 24፥13-15፤ ኤር. 14፥12፤ ሕዝ. 6፥11:12፤ ማቴ. 24፥7። «በሽታ» ይመ.

**ችቦ**፤ የጥራሮ መብራት፤ መሳ. 15፥4:5፤ ራእ. 8፥10።

**ችፌ**፤ እንደ መ.ቅ. አሳብ ቃሉ የሚያሳክክና ፈሳሽ የሚያወጣ የቆዳ በሽታን ይገልጣል፤ ዘዳ. 28፥27። «በሽታ» ይመ.

**ኃሣር**፤ ከስድብና ከነቀፋ የተነሣ የሚመጣውን ውርደት ያመለክታል፤ መዝ. 69፥20።

**ኃይል**፤ ጥንካሬ፥ ጉልበት፥ ብርታት። መ.ቅ. ስለ ልዩ ልዩ ዓይነት ኃይል ይናገራል። ይኸውም የሰው ኃይል (ዘፍ. 31፥29፤ ሉቃ. 1፥17፤ ሐ.ሥ. 3፥12፤ 1ቆሮ. 4፥19:20)፥ የጦር ሠራዊት ኃይል (1ዜ.መ. 20፥1)፥ የመንግሥታት ኃይል (አስ. 1፥3)፥ የሰይጣን ኃይል (ኢዮብ 1፥12)፥ የእግዚአብሔር ኃይል (1ዜ.መ. 29፥11፤ ኢሳ. 40፥29፤ ሉቃ. 1፥35፤ 5፥17፤ ሮም 1፥16:20:21)፥ የክርስቶስ ኃይል (1ቆሮ. 5፥3:4)፥ የመንፈስ ቅዱስ ኃይል፤ ሉቃ. 4፥14፤ 24፥49፤ ሐ.ሥ. 1፥8፤ ሮም 15፥13:18:19። ምእመናን ለእግዚአብሔር ሊኖሩ የሚችሉት ክርስቶስ በሚሰጣቸው ኃይል ነው፤ 2ቆሮ. 12፥9፤ ፊል. 4፥13።

**ኃጢአት**፤ ስሕተት፥ ክፋት፥ ሕግን መተላለፍ፥ ዓመፃ፥ በጎ ማድረግን ዐውቆ አለመሥራት፥ በእምነት መሠረት አለመኖር፥ ወደ እግዚአብሔር ክብር አለመብቃት፤ ሮም 3፥11:12:23፤ 14፥23፤ 1ዮሐ. 3፥4፤ ያዕ. 2፥10፤ 4፥17። የተለያየ ኃጢአት ቢኖርም፥ ዋናው ኃጢአት በእግዚአብሔርና በክርስቶስ አለማመን ነው፤ መዝ. 51፥4፤ ሉቃ. 15፥18፤ ዮሐ. 16፥9፤ ሮም 8፥7።

1. የኃጢአት መኖር፤ ሰይጣን አስቀድሞ ወደቀ (2ጴጥ. 2፥4፤ ይሁዳ 6)፤ ሰውንም አታለለ። አዳም የተከለከለውን ፍሬ ዐውቆ በመብላቱ የእግዚአብሔርን ሥልጣን ተቃወመ፤ ቸርነቱን ረሳ፤ ጸጋውን ናቀ፤ ጥበቡን ነቀፈ፤ ጽድቁን ካደ፤ ቃሉንም አቃለለ፤ ዘፍ. 3፥1-6። እንደዚሁም የማንም ሰው ኃጢአት ውሸት፥ ስርቆት ... ወዘተ ብቻ ሳይሆን፥ ከእግዚአብሔር መንገድ መውጣትና እግዚአብሔርን መቃወም ነው።

2. የኃጢአት ውጤት ፦

ሀ) አዳም ሲወድቅ እግዚአብሔርን ፈራ፤ በእግዚአብሔር ፊት ለመታየት አፈረ፤ ዘፍ. 3፥7-10፤ ዮሐ. 3፥20።

ለ) የእግዚአብሔር ቍጣ በሰዎች ላይ ሆነ፤ ዘፍ. 3፥16-19:23፤ ዮሐ. 3፥36።

ሐ) ፍጥረት ተረገመ፤ ዘፍ. 3፥17፤ ሮም 8፥20።

መ) ሰው በሰው ላይ መነሣት ጀመረ፤ ዘፍ. 4፥8:19:23:24፤ 6፥2-5።

ሠ) የአዳም ኃጢአት በዘሩ ሁሉ ተቈጠረ፤ መዝ. 14፥2-3፤ መክ. 7፥20፤ ሮም 5፥12:18፤ 1ቆሮ. 15፥22።

ረ) ሞት ገባ፤ ዘፍ. 2፥17፤ ሮም 6፥23።

ሰ) ሰው ኃጢአተኛ ሆነ፤ ረከሰ፤ ልቡም ክፉ ሆነ፤ ዘፍ. 8፥21፤ መዝ. 51፥5፤ ኤር. 17፥9፤ ማር. 7፥20-23፤ ሮም 3፥10-18። ሰው ኃጢአትን ከመሥራት በእግዚአብሔርና በባለ ሥልጣን ፍርሃት፥ በሥራ ድካም በሌላም ይገታል። በከፊልም የእግዚአብሔርን ሕግ ሊፈጽም ይችላል (ሮም 2፥14:15)፤ ነገር ግን ከእምነትና ከፍቅር የማይመነጭ መልካም ሥራ ለእግዚአብሔር ክብር

ስለማይደረግ እግዚአብሔርን አያስደስትም። እንደዚህ የሚያደርጉም ግብዞች ይባላሉ፤ ማቴ. 6፥2:5:16፤ ማር. 7፥6:7፤ 1ቆሮ. 10፥31፤ 13፥3፤ ቲቶ 1፥15፤ 3፥5፤ ዕብ. 11፥6።

ሸ) ሰው ኃጢአተኛ በመሆኑ ፍጹም ደግነትን ማሳየት አይችልም፤ በራሱም ወደ እውነት ሊመለስ አይችልም፤ አያስተውልም (1ቆሮ. 2፥14)፥ አይታዘዝም (ሮም 8፥7)፥ አያምንም፤ ዮሐ. 6፥44:45:65። ስለዚህ የእግዚአብሔር መንፈስ ካልሠራ የሰው ልብ አይለወጥም፤ ዮሐ. 3፥3-8።

**ኅብረት**፤ አንድ መሆን፥ መተባበር፥ መስማማት። የክርስቲያን ኅብረት ከክርስቶስ ጋር አንድ መሆን ነው፤ 1ቆሮ. 12፥27፤ ገላ. 3፥27:28፤ 1ዮሐ. 1፥3። አማኝ ከእግዚአብሔርና ከሌሎች ምእመናን ጋር ኅብረት ይኖረዋል (ሐ.ሥ. 2፥42፤ ፊል. 2፥1፤ 1ዮሐ. 1፥3:4)፥ ከጨለማ ነገር ጋር ኅብረትን ከማድረግ ይሸሻል፤ 2ቆሮ. 6፥14-18፤ 1ዮሐ. 1፥6:7። ኅብረት ከመንፈስ ቅዱስ የሚገኝ በረከት ነው፤ 2ቆሮ. 13፥14። «አንድነት» ይመ.

**ኅብር**፤ መልክ፥ ዐይነት፤ ዘፍ. 37፥3።

**ኅብስት**፤ በብ.ኪ. ጊዜ ለቍርባን ይቀርብ የነበረ ማለፊያ ዳቦ። ካህናት በየሰንበቱ ዐሥራ ሁለት ኅብስት አዘጋጅተው በገበታ ላይ ያኖሩ ነበር፤ ይህም ገጸ ኅብስት ይባላል። ያደረውንም ኅብስት ይበሉታል፤ ዘሌ. 24፥5-9፤ ዘኍ. 4፥7።

**ነህምያ**፤ የፋርስ ንጉሥ የአርጤክስስ ጠጅ አሳላፊ የነበረ አይሁዳዊ፤ ነህ. 1፥1:2:11። በአንዳንድ የግእዝ መጽሐፍ ሴንያ ተብሎ ይጠራል። በአርጤክስስ ዘመነ መንግሥት በ20ኛው ዓመት፥ በ445 ከክ.ል. ኢየሩሳሌምን ለማሠራት ፈቃድ ተቀበለ፤ ነህ. 2፥1:5:6:11። የኢየሩሳሌምን ፍርስራሽ ካየ በኋላ የከተማይቱን ሹማምንት ለሥራ አነሣሣቸው፤ የጠላትን ተቃውሞ ሳይፈራ በ52 ቀን ቅጥርዋን አሠራ፤ ነህ. 2፥12-6፥15። አገሩን ሲገዛና ሕዝቡን በምክር ሲመራ እስከ 433 ከክ.ል. በኢየሩሳሌም ቆየ፤ ነህ. 8፥9፤ 10፥1፤13፥6። «ሐቴርሳታ» ማለት አገረ ገዥው ማለት ነው። በዚያን ጊዜ ወደ አርጤክስስ ተመለሰ፤ እንደገናም ወደ ኢየሩሳሌም መጥቶ ተገቢ ያልሆኑ ሁኔታዎችን አይቶ በማሳጹና በኃይል አስወገዳቸው፤ ነህ. 13። ነህምያና ዕዝራ አብረው ይሠሩ ነበር። ነህምያ የእምነት ሰው ነበረ፤ በእግዚአብሔርም ቃል መሠረት በድፍረት ለመጸለይና ለመሥራት ቻለ፤ 1፥4-11፤ 2፥4:20፤ 4፥14:15፤ 6፥9-11።

**የነህምያ መጽሐፍ**፤ መጽሐፉ በጥንታዊ ዕብራይስጥ ጽሑፍና በግእዝ የመጽሐፈ ዕዝራ ክፍል ነው። ነህምያ ራሱ የጻፈው መሆኑ ግልጽ ነው፤ ም. 1፥1:2:4 ሌላም።



ነነዌ

አከፋፈል ፡-

1. ነህምያ ወደ ኢየሩሳሌም ሄዶ ቅጥርዋን ማሠራቱ፤ 1፥1-7፥4።

2. ከምርኮ የተመለሱት፥ በኢየሩሳሌም የኖሩት፥ የካህናቱና የሌዋውያኑም ዝርዝር፤ 7፥5-73፤ 11፥1-12፥26።

3. የሕጉ መጽሐፍ መነበቡ፥ የንስሓ ጸሎት፥ ቃል ኪዳኑ መጽናቱ፤ 8፥1-10፥39።

4. የቅጥሩ መቀደስ፥ የእግዚአብሔርን ቤት ማስተዳደሩ፤ 12፥27-47።

5. ነህምያ ሕግ ተላላፊዎችን መገሠጹ፤ 13፥1-31።

**ነሐስ፤** «ናስ» ይመ.

**ነቃ፤** ተነሣ፥ ከእንቅልፍ፥ ከሞትና ከሌላም ሁኔታ፤ ዘፍ. 9፥24፤ ዳን. 12፥2፤ ሉቃ. 9፥32፤ ሮም 13፥11።

**ነቍጣ፤** በበግና በፍየል ወይም በሌላ እንስሳ መደበኛ አካል ላይ አልፎ አልፎ የሚታይ ልዩ መልክ፤ ዘፍ. 30፥33:35።

**ነቢይት፤** ትንቢትን የምትናገር ሴት። የታወቁት ነቢያት የሙሴ እኅት ማርያም (ዘጸ. 15፥20)፥ የለፊዶት ሚስት ዲቦራ (መሳ. 4፥4-7)፥ በኢዮስያስ ዘመነ መንግሥት የነበረችው ሕልዳና (2ነገ. 22፥14-20)፥ ሐና (ሉቃ. 2፥36)፥ የፊልጶስ አራት ደናግል ሴቶች ልጆች ናቸው (ሐ.ሥ. 21፥9)። ሴቶች በቤ.ክ. ትንቢት መናገር ይፈቀድላቸዋል፤ ሐ.ሥ. 2፥17፤ 1ቆሮ. 11፥5።

**ነቢይ፥ ነቢያት፤** ቃልን ከእግዚአብሔር ተቀብሎ ለሕዝብ የሚናገር። ነቢይ፥ የእግዚአብሔር ሰው (1ሳሙ. 9፥6)፥ ባለራእይ (1ሳሙ. 9፥9)፥ የእግዚአብሔር ባሪያ (2ነገ. 24፥2) ይባላል። ነቢያት ቃሉ ከእግዚአብሔር እንደመጣ ቢረዱም፥ እንዴት እንደመጣላቸው ብዙ ጊዜ አይገልጡም ነበር። ብቻ «እግዚአብሔር እንዲህ ይላል» እያሉ ትንቢት ይናገሩ ነበር፤ አሞጽ 1፥3:6:9፤ ሚክ. 3፥8። ቃሉ አንዳንድ ጊዜ በራእይ፥ በሕልም፥ በመልአክም ይገለጥላቸው ነበር፤ ዘኁ. 12፥6፤ ዳን. 10፥11። ቃሉ. በብዙ ዓይነት መንገድ ቢሰጣቸውም (ዕብ. 1፥1)፥ እስኪናገሩ ድረስ በእነርሱ ላይ እንደ ሸክም ነበረ። በእግዚአብሔር መንፈስ ተመርተው ተናገሩ፤ ኢሳ. 15፥1፤ 2ጴጥ. 1፥21። ነቢያት ለዚህ ሥራ ተጠሩ፤ ኢሳ. 6፤ ኤር. 1፥4-10፤ ሉቃ. 3፥2።

ቃሉ ስለ ሁለት የተያያዙ ነገሮች የሚያስገነዝብ ነበር።

1ኛ. በእግዚአብሔር ውሳኔ ስለሚፈጸሙ ድርጊቶች፥ ስለ መንግሥታት፥ ስለ ሰዎች፥ ስለ ኃጢአት።

2ኛ. ወደፊት ስለሚሆኑት ድርጊቶች። ነቢያት ብዙ ጊዜ የእግዚአብሔርን ቃል በምሳሌ (ኢሳ. 5፥1-7)፥ ወይም በድርጊት ይገልጡ ነበር፤ ኤር. 19፤ ሕዝ. 4።

ለነቢያት ትምህርት ቤትና ደቀ መዛሙርት ነበሩአቸው (1ሳሙ. 19፥20፤ 2ነገ. 2፥3፤ ኢሳ. 8፥16)፥ እነርሱም የነቢያትን ትንቢት የጻፉ ይመስላል። ራሳቸውም ነቢያት የታሪክ መጻሕፍትን ጽፈዋል፤ 2ዜ.መ. 9፥29፤ 32፥32። ነቢያት የእግዚአብሔርን ቃል ያስተላልፉ ነበር፤ 1ነገ. 13፥11-25።

ሐሰተኞች ነቢያት ነበሩ። አንዳንዶች በውቀው ለገንዘብ ሲሉ ይናገሩ ነበር (አሞጽ 7፥12:13)፥ ሌሎች ተሳስተው ከራሳቸው የልብ አሳብ ተናገሩ (ሕዝ. 13፥2)፥ የተወሰኑት ደግሞ በክፉ መንፈስ ተመርተው ተናገሩ፤ 1ነገ. 22፥19-25። ነቢይ ሐሰተኛ መሆኑ የሚታወቀው ፡- ቃሉ ሳይፈጸም ሲቀር (ዘዳ. 18፥20-22)፥ ባዕድ አምልኮትን ሲከተል (ዘዳ. 13፥1-4)፥ አካሄዱ ክፉ ሲሆን (ኤር. 23፥9-14)፥ ኃጢአት በበዛ ጊዜ ስለ ፍርድ ሳይሆን፥ ስለ ሰላም ሲተነብይ (ኤር. 23፥16-32) ነው።

ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ራሱ በትስብእቱ ከፈጸመላቸው አገልግሎቶች አንዱ የትንቢት ሥራ በመሆኑ ነቢይ ነው። ለደኅንነታችን የተሰጠውን የእግዚአብሔርን ፈቃድ በመግለጥ የነቢይነትን ሥራ ፈጸመ፤ ማቴ. 5፥17-18፤ ማር. 6፥4፤ ሉቃ. 7፥16፤ ዮሐ. 1፥18፤ 9፥17፤ 14፥24:26።

በአ.ኪ. ዘመንም እግዚአብሔር ነቢያትን አስነሣ፤ ከሐዋርያት ጋር የቤ.ክ. መሥራቾች ነበሩ፤ ከመምህራንም ጋር አገለገሉ፤ ሐ.ሥ. 13፥1፤ ኤፌ. 2፥20። ሥራቸው የሚመጣውን መግለጥ (ሐ.ሥ. 11፥28፤ 21፥10:11፤ ራእ. 1፥19)፥ ቤተ ክርስቲያንንም መምከር፥ ማጽናትና ማነጽ ነው፤ ሐ.ሥ. 15፥32፤ 1ቆሮ. 14፥3። በቤ.ክ. የትንቢት ቃል ለነቢይ ሲገለጥ በሥርዓት ሊነገር ይገባል፥ ሌሎችም የእግዚአብሔር ቃል መሆኑን መለየት ያስፈልጋቸዋል፤ 1ቆሮ. 14፥6-33። ሐሰተኞች ነቢያት እንደሚነሡ ክርስቶስም ሐዋርያትም ተናግረዋል፤ ማቴ. 7፥15-20፤ 2ጴጥ. 2፥1፤ 1ዮሐ. 4፥1። «ራእይ»፥ «ትንቢት» ይመ.

**ነብር፤** «እንስሳት» ይመ.



**ነነዌ፤** ይህ ጥንታዊ ከተማ በጤግሮስ ወንዝ ዳር በናምሩድ ተመሠረተ፤ ዘፍ. 10፥11:12። ለአሦር መናገሻ ከተማ ሆነ፤ እጅግ ሰፊና ያማረ ነበር። የከተማው ቅጥር ርዝመት ዐሥራ ሁለት ኪ.ሜ. ነበረ፤ እነሰናክሬም ብዙ ሕንጻዎችን ሠሩበት፤ ዮናስ 4፥11። የነነዌ ሰዎች ንስሓ እንዲገቡ ዮናስ ወደ ነነዌ ተላከ፤ ንስሓም ገቡ፤ ሉቃ. 11፥30። የባቢሎን መንግሥት በ612 ከክ. በ. ከተማውን ድል አፈረሰው። ካ. 1 ለ።

**ነካ፤** ዳሰሰ፤ ያዘ፤ ዘፍ. 3፥3፤ ኢሳ. 52፥11፤ ዘካ. 2፥8፤ ዮሐ. 20፥17፤ ቆላ. 2፥22።

**ነውር፤** አሳፋሪ ድርጊት ወይም ሁኔታ። በተለይ ከተፈጥሮ ሁኔታ በመውጣት የሚያጋጥም (ዘጸ. 12፥5፤ ሮም 1፥27፤ 1ቆሮ. 11፥14-15፤ 14፥35፤ ኤፌ. 5፥12) ወይም ኃጢአት ወደ በመሥራት ይታያል፤ ፊል. 3፥19፤ ይሁዳ 13። ክርስቲያን ያለ ነውር መሆን አለበት፤ ኤፌ. 1፥4፤ 5፥27። በዕብ. 12፥1-2 «ነውር» የመስቀል ላይ ውርደትን ያመለክታል።

**ነዘር፤** ተናዳፊ እባብ፤ ኢሳ. 30፥6።

**ነዶ፤** ከታጨደ በኋላ በአንድነት ታስሮ የተቀመጠ እህል። የገብስ፣ የስንዴና የጤፍ ነዶ ሊባል ይችላል፤ መዝ. 126፥6። የዮሴፍ የነዶ ሕልም አየ፤ ዘፍ. 37፥6-7። በፍርድ ቀን የጻድቃንና የኃጥአን መለየት በነዶ ተመስሏል፤ ማቴ. 13፥30።

**ነገ፤** ከዛሬ በኋላ የሚሆነው ቀን ወይም ዘመን፤ ምሳ. 27፥1፤ ኢሳ. 22፥13፤ ማቴ. 6፥34፤ ሉቃ. 13፥32፤ 1ቆሮ. 15፥32፤ ያዕ. 4፥13-14።

**ነገሥት፤** ስለ እስራኤልና ስለ ይሁዳ ንጉሦች የሚተርኩ 1ኛና 2ኛ ነገሥት መጻሕፍት። ከዳዊት ልጅ ከሰሎሞን አንሥቶ እስከ ይሁዳ መንግሥት ማለቂያ ድረስ የሁለቱን፣ የእስራኤልንና የይሁዳን መንግሥታት፣ የነገሥታትን ታሪክ ይተርካሉ። የ400 ዓመት ታሪክ ነው። ዳዊትና ሰሎሞን 12ቱን ነገዶች በሙሉ ሲገዙ፣ በሰሎሞን ልጅ በሮብዓም ዘመን መንግሥቱ ተከፍሎ ዐሥሩ ነገዶች የሰሎሞን ጠላት የኢዮርብዓም ግዛት ሆኑ፤ እስራኤልም ተባሉ። 2 ነገዶችም ለሮብዓም ሆኑ፤ ይሁዳም ተባሉ፤ 1ነገ. 11፥28-33፤ 12፥16-20። በኢዮርብዓም መሪነት የሰሜኑ መንግሥት ሕዝብ በእግዚአብሔር ላይ በማመፅ ሌሎችን አማልክት ማምለክ ጀመሩ፤ በእስራኤልም ነገሥታት መካከል እግዚአብሔርን የሚፈራ ብዙ አልነበረም። እግዚአብሔር አሦራውያንን በእስራኤል ላይ ያስነሣባቸው በዚህ ምክንያት ነው። የእስራኤልም መናገሻ ከተማ የነበረችው ሰማርያ በ722 ክክ. በ. በአሦራውያን እጅ ፈረሰች፤ የእስራኤልም ሕዝብ ተማርከው ወደ አሦር ፈለሱ፤ 2ነገ. 17፥3-6።

በደቡብ መንግሥት በይሁዳ የኢየሩሳሌም ከተማ፣ የእግዚአብሔር ቤተ መቅደስና ካህናት ነበሩ። ሕዝቡ እግዚአብሔርን ይፈሩ ነበር። መልካሞችም ነገሥታት ነበሩ፤ በኋላ ግን ምናሴ በጣም ስለከፋ፣ እግዚአብሔር በሰማርያ ላይ አሦራውያንን እንዳስነሣ በኢየሩሳሌም ላይ ናቡከደነፆር የተባለውን የባቢሎንን ንጉሥ አስነሥቶ በ586 ክክ. በ. ኢየሩሳሌም በባቢሎን ሰዎች (በከለዳውያን) እጅ ፈረሰች፤ የይሁዳም ሕዝብ ተማርከው ወደ ባቢሎን ፈለሱ፤ 2ነገ. 24፥3:4:10-15።

አብዛኞቹ ነቢያት የተነሡት በነገሥታት ዘመን ነው። ነገሥታቱና ሕዝቡ ሲያምፁበት፣ «ተመለሱ፣ ካልተመለሳችሁ እግዚአብሔር ይፈርድባችኋል» ብለው እንዲያስጠነቅቁአቸው እግዚአብሔር ነቢያትን ላከላቸው፤ 2ዜ.መ. 36፥15:16፤ ኤር. 25፥1-11። ከኤልያስና ከኤልሳዕ ሌላ ኢሳይያስና ሚክያስ፣ ሆሴዕና አሞጽ፣ ሶፎንያስ፣ ኤርምያስ፣ ሌሎችም ነቢያት የተነሡት በነገሥታት ዘመን ነው።

የነገሥታት ታሪክ በሙሉ አስቀድሞ በ1 መጽሐፍ ብቻ ተጽፎ ነበር፤ 70 ሊቃናት ግን ወደ ግሪክ ቋንቋ በተረጐሙት ጊዜ መጽሐፉ በ2 ተከፈለ። መጽሐፉ የተጻፈው ንጉሡ ዮአኪን ከሞተ በኋላ ነውና ምናልባት በስደት ዘመን በባቢሎን አገር ሳይጻፍ አልቀረም፤ 2ነገ. 25፥29:30። ጸሐፊው ማን እንደሆነ ግን አልታወቀም። ነገር ግን እንደ ጥንት አይሁድ አሳብ በታወቀ ነቢይ (ነቢያት) እንደተጻፈ ይታሰባል። ጸሐፊው ታሪኩን ሲያዘጋጅ ቀደም ብሎ ስለ ጉዳዩ የተጻፉ መጻሕፍትን እንዳነበበ ይታመናል፤ 1ነገ. 11፥41፤ 14፥19:29፤ 1ዜ.መ. 29፥29።

አከፋፈል ፦

1. የሰሎሞን ዘመነ መንግሥት፤ 1ነገ. 1-11።

2. እስራኤል እስከተማረከ ድረስ የነበሩ የእስራኤልና የይሁዳ ነገሥታት ታሪክ፤ 1ነገ. 12 እስከ 2ነገ. 17።

3. ይሁዳ እስከተማረከ ድረስ የቆዩት የይሁዳ ነገሥታት ታሪክ፤ 2ነገ. 18-25።

**ነገረ፤** አሳብን ገለጠ። እግዚአብሔር በብዙ ዓይነት መንገድና በመጨረሻም በልጁ ተናግሯል፤ ዕብ. 1፥1-2። ክርስቶስ ለሰዎች ተናገረ፤ ደቀ መዛሙርቱም ስለ ልዩ ልዩ ነገር ተነጋገሩ፤ ሉቃ. 24፥13-14:32።

**ነገድ፤** ከአንድ አባት የተወለደ ሕዝብ። ያዕቆብ ዐሥራ ሁለት ወንዶች ልጆቹን ባረካቸው (ዘፍ. 49)፤ እነርሱም የቤተ እስራኤል አባቶችና ነገዶች ሆኑ። የዮሴፍ ነገድ በስሙ ሳይሆን ብዙ ጊዜ በልጆቹ በኤፍሬምና በምናሴ ተጠርቷል፤ በእስራኤል ሰልፍም ጊዜ ኤፍሬምና ምናሴ ሁለት ነገዶች ሆነው ተቈጠሩ፤ ዘኍ. 2፥18-24።

የእስራኤል ነገዶች ከነዓንን ሲወርሱ፣ እንደ ሁኔታቸውና እንደ ብዛታቸው፣ በምርጫም በዕጣም ርስት ተሰጣቸው። የሌዊ ነገድ ካህናት በመሆናቸው እንደ ሌሎቹ መሬት አልተሰጣቸውም፤ ዘኍ. 32፤ ኢያሱ 13-19። ካ. 3 ይመ.። በመሳፍንት ዘመን እያንዳንዱ ነገድ በራሱ ተዳደረ። በሳኦልና በዳዊት ጊዜ ግን አንድ እየሆኑ ሄዱ፤ ዳዊትም ለየነገዱ አለቃ ሾመ፤ 1ዜ.መ. 27፥16-22።

የይሁዳ ነገድ እየበረታ ሲሄድ ሌሎች አልተደሰቱም ነበርና፣ ከሰሎሞን ሞት በኋላ በሮብዓም ላይ ዐመፁ፤ ኢዮርብዓምንም አነገሡ፤ የእርሱም መንግሥት እስራኤል ተባለ፤ 1ነገ. 12፥1-16። ከባቢሎን ምርኮ በኋላ ሰዎች ነገዳቸውን ቢያውቁም ለአስተዳደሩ ለውጥ አላመጣም፤ ሉቃ. 2፥36፤ ያዕ. 1፥1።

ዐሥራ ሁለት ነገዶችና ዐሥራ ሁለት ሐዋርያት ይመሳሰላሉ፤ ስሞቻቸውም በመንግሥተ ሰማያት በሮችና መሠረቶች ላይ ተጽፈዋል፤ ማቴ. 19፥28፤

ገላ. 6፡16፤ ራእ. 21፡12-14።

**ነጋሪት**፤ እንደ ከበሮ ያለ ባለአንድ አፍ፥ በቆላቱ እንጨት የሚመታ የዜማ ዕቃ፤ 2ሳሙ. 6፥5።



ነጋሪትና መምቻው

**ነጐድጓድ**፤ መብረቅ ከወረደ በኋላ የሚሰማ ድምፅ፤ ኢዮብ 37፥2-5፤ መዝ. 29። ፍልስጥኤማውያን እንዲሸነፉ እግዚአብሔር የነጐድጓድ ድምፅን አሰማ፤ 1ሳሙ. 7፥10። ነጐድጓድ የእግዚአብሔር ድምፅ ይባላል፤ የእግዚአብሔርንም ኃይል ይገልጣል፤ ኢዮብ 40፥9፤ መዝ. 18፥13፤ ዮሐ. 12፥29።

**ነፃነት**፤ «አርነት» ይመ.

**ነፃ ወጪዎች**፤ እነዚህ ሰዎች እነማን እንደነበሩ ለመወሰን ያስቸግራል። በ63 ከክ. ል. በነበረው ጦርነት የተያዙ ምርኮኞች ልጆች እንደነበሩ የሚገምቱ አሉ፤ ሐ.ሥ. 6፥9። «ሮማዊ»፥ «ባሪያ» ይመ.

**ነፃ ፈቃድ**፤ ሰው ሁሉ ዕውቀት ያለው ሆኖ ስለተፈጠረ፥ ክፉንም ሆነ መልካሙን እንደየጠባዩና እንደየምኞቱ ለመምረጥ ይችላል። ለምርጫውም ራሱ ኀላፊ ነው፤ ዘፍ. 2፥17፤ ዘዳ. 30፥19:20፤ ኢያሱ 24፥15፤ ያዕ. 1፥14:15። ሰው በኃጢአት ከወደቀም በኋላ ሁልጊዜ በራሱ ምርጫ በመመራት የልቡን ፍላጎት ይፈጽማል፤ እግዚአብሔርንና የእግዚአብሔርን ነገር አይፈልግም፤ አይመርጥምም። ሰው ከአዳም የተወለደ ስለሆነ የኃጢአት ባሪያ ነው። ስለዚህ እግዚአብሔር በሰው ልብ ሲሠራ ሰው ወደ እግዚአብሔር ይደርሳል፤ ዮሐ. 6፥44፤ 8፥34፤ ሮም 3፥11፤ 8፥5-8፤ 1ቆሮ. 2፥14፤ ኤፌ. 2፥1-10። «የእግዚአብሔር መጋቢነት» ይመ.

**ነጥብ**፤ የትንሽ መለያ ማቆሚያ። ክርስቶስ ነጥብ ሲል በአማርኛ ፊደላት ቅጽሎች እንዳሉ፥ በዕብራይስጥ ፊደሎችም መለያዎች አሉና በሕግ በኩል ከእነዚህ ጥቃቅን ምልክቶች አንዲት እንኳ እንደማትሻር አመለከተ፤ ማቴ. 5፥18። «የውጣ» ይመ.

**ነፋስ**፤ የአየር እንቅስቃሴ። ነፋስ ከየት እንደሚመጣ፥ ወዴት እንደሚሄድ አይታወቅም፤ ዮሐ. 3፥8። እግዚአብሔር የዓለምን የአየር ሁኔታ በአራት ነፋሳት እንደወሰነ ተጽፏል፤ ኤር. 49፥36፤ ዳን. 7፥2፤ ራእ. 7፥1። ነፋስ እንደ አቅጣጫው በረከት ወይም እንቅፋት ሊሆን ይችላል። በከነዓን የምሥራቅ ነፋስ መሬቱን ያደርቃል፤ ኃይለኛም ነው (ዘፍ. 41፥6፤ መዝ. 48፥7)፤ የምዕራብ ነፋስ የዝናም ነፋስ ነው (1ነገ. 18፥41)፤ የሰሜን ነፋስ ብርድ ያመጣል (ኢዮብ 37፥9፤ ምሳ. 25፥23)፤ የደቡብም ነፋስ ሙቀት ይሰጣል፤ ኤር. 4፥11፤ ሉቃ. 12፥55። ነፋስ በእግዚአብሔር ትእዛዝ ይነሣል (መዝ. 107፥25)፤ የእግዚአብሔርም እስትንፋስ ይባላል፤ ኢሳ. 40፥7። ነፋስ በምሳሌነት ለብዙ ነገር ተጠቅሷል፤ ኢሳ. 41፥29፤ ዮሐ. 3፥8፤ ኤፌ. 4፥14፤ ይሁዳ 12። «አውራቂስ»፥ «ዓውሎ ነፋስ» ይመ.

**ነፍስ ገዳይ**፤ ሰው በእግዚአብሔር መልክ ስለተፈጠረ ሰውን መግደል ተከልክሏል። በነፍስ ገዳይም የሞት ፍርድ ተወሰነ፤ ዘፍ. 9፥4-6፤ ዘጸ. 20፥13፤ 21፥14፤ ዘሌ. 24፥17። የሟቹ ቅርብ ዘመድ ነፍስ ገዳዩን መግደል ነበረበት። ገዳዩ ያለ ቂም በድንገት ገድሎ ወደ መማፀኛ ከተማ ቢሸሽ ይድናል፤ አለበለዚያ ግን ለደም ተበቃዩ ተላልፎ ይሰጣል፤ ዘኁ. 35፥9-34፤ ዘዳ. 19፥1-10።

ክርስቶስ ስድብና ንቀፈታ ነፍስ እንደ መግደል የሚቈጠሩ መሆናቸውን አስተማረ፤ ማቴ. 5፥21:22። ትእዛዙ «አትግደል» ሲል በግል ኀላፊነት እንጂ በእግዚአብሔር ሥልጣን ሰው እንዳይገድል አይከለክልም። በሕግ መሠረት የሞት ፍርድ የሚወስኑ በእግዚአብሔር ሥልጣን ይሠራሉ፤ ሮም 13፥3:4። እንደዚሁም የእስራኤል ሕዝብ በጦርነት ጊዜ በእግዚአብሔር ትእዛዝ ሰዎችን ሲገድሉ፥ የእግዚአብሔርን ውሳኔ ኃጢአት በሞላባቸው ሕዝብ ላይ ይፈጽማሉ፤ ዘዳ. 20፥13፤ ዘፍ. 15፥16፤ 1ነገ. 20፥26፤ 1ሳሙ. 15፥2:3። «ጦርነት» ይመ.

**ነፍስ**፤ የሰው ሕይወት፥ ከእግዚአብሔር እስትንፋስ የተገኘ ነው፤ ዘፍ. 2፥7። ነፍስ ሰውን ብቻ ሳይሆን እንስሳትንም ሊያመለክት ይችላል፤ ሆኖም የእንስሳት ሕይወታቸው ደማቸው ብቻ ነው፤ ዘፍ. 1፥20፤ ዘሌ. 17፥11። ሰው ሥጋና ነፍስ ነው። ሰው ሲሞት ነፍሱ ከሥጋው ይለያል፤ ወደ እግዚአብሔርም ይመለሳል፤ ምሳ. 11፥30፤ መክ. 12፥7፤ ሉቃ. 23፥46። ነፍሳት በእግዚአብሔር ፊት መቆምና መናገር ይችላሉ፤ ራእ. 6፥9:10። ነፍስ የሰውን ሕይወት (ሮም 11፥3)፥ ስሜትን (ሉቃ. 1፥46)፥ ፈቃድንም (ሮም 13፥1) ያጠቃልላል። እግዚአብሔር ለአዳም ነፍስን ሰጠው። ሰዎች ሳይወለዱ በአባታቸው ወገብ እንዳሉ ይቈጠራሉ፤ ዕብ. 7፥9:10። ደግሞም ነፍስ ከእግዚአብሔር እንደሚሰጥ መ.ቅ. ያስተምራል፤ መክ. 12፥7፤ ኢሳ. 42፥5። የሰው ነፍስ ሊጠፋ ይችላል። ይህም የእግዚአብሔርን መንግሥትና ክብር አለማግኘትን እንጂ ፈጽሞ መደምሰስን አያሳይም፤ ማቴ. 10፥28፤ 16፥26።

አንዳንዶች፥ ሰው ሥጋ፥ ነፍስና መንፈስ የሚገኙበት ፍጡር ነው ይላሉ። ነገር ግን መ.ቅ. ሰው ሁለት፥ ማለትም ሥጋና ነፍስ ወይም ሥጋና መንፈስ ብቻ መሆኑን ያስተምራል፤ ማቴ. 6፥25፤ 10፥28። መንፈስ ረቂቅ ስሆነው ለሰው ነፍስ በተለዋጭነት የተሰጠ ስም ነው፤ መክ. 12፥7፤ 1ቆሮ. 5፥3-5። በተጨማሪም ሮም 8፥10፤ 1ቆሮ. 7፥3-4፤ 2ቆሮ. 7፥13፤ ዘፍ. 35፥18፤ ሐ.ሥ. 15፥25፤ መዝ.

35፥3፤ ሉቃ. 23፥46 ይመ.። 1ተሰ. 5፥23 እና ዕብ. 4፥12 ነፍስንና መንፈስን ለየብቻ የጠቀሱት የተለያዩ ክፍሎች መሆናቸውን ለማመልከት ሳይሆን፥ ሰውን በሁለት አቅጣጫ ለማየት ነው። ማቴ. 22፥37ን ያስተያዩ። «መንፈስ»፥ «ቅጣት»፥ «ሰው» ይመ.

**ነፍስ ወከፍ**፤ እየራሱ፥ ለእየራሱ፥ እያንዳንዱ፥ ለእያንዳንዱ፥ አንድም ሳይቀር ማለት ነው፤ 1ዜ.መ. 23፥3።

**ኑኃሚን**፤ ትርጉሙ «ደስታዬ» ማለት ነው፤ ሩት 1፥20:21። የቤተ ልሔሙ የአቤሜሌክ ሚስት። በሞዓብ ሳለች ባሏና ልጆቿ ሞቱባት፤ ግን ሞዓባዊት የሆነች ምራቷ ሩት በአምላኳ ስላመነች፥ ከእርሷ ጋር ወደ ቤተ ልሔም ተመለሰች፤ ሩት ም. 1። ኑኃሚን ሕግን ከማክበሯ የተነሣ፥ የባሏ ዘመድ ቦዔዝ ሩትን እንዲያገባ አደረገች፤ ኢዮቤድ ለተባለ ልጃቸው ሞግዚት ሆነች። እርሱም የዳዊት አያት ነበረ፤ ሩት ም. 2-4፤ ዘዳ. 25፥5:6፤ ዘሌ. 25፥25።

**ኑዛዜ**፤ ሰው ሳይሞት ያለውን ንብረት ለማከፋፈል በሽማግሌዎች ፊት የሚያደርገው ውሳኔ። ሰው እስኪሞት ድረስ ግን ኑዛዜው አይጸናም። ክርስቶስ በመሞቱ ኑዛዜውንና ቃል ኪዳኑን አጸና፤ ዕብ. 9፥15-17። «ቃል ኪዳን» ይመ.

**ኑፋቄ**፤ ጥርጥርና መለያየት (ሐ.ሥ. 24፥14) ወይም ከትክክለኛ እምነት ጋር የማይስማማ ትምህርት፤ 2ጴጥ. 2፥1።

**ኒሳን**፤ «ወር» ይመ.

**ኒቆዲሞስ**፤ ፈሪሳዊና የአይሁድ አለቃ። ኢየሱስን ሊጠይቅ በሌሊት ወደ እርሱ ሄደ (ዮሐ. 3)፤ የኢየሩሳሌም ሸንጎ ኢየሱስን ሊከሰው ሲፈልግ ኒቆዲሞስ ስለ ክርስቶስ መሰከረ፤ ዮሐ. 7፥45-52። ኢየሱስ ከተሰቀለ በኋላ ለመግነዝ የሚሆን ልዩ ቅመም ይዞ መጣ፤ ዮሐ. 19፥39።

**ኒቆጵልዮን**፤ የእልዋሪቆን ወደብ። ጳውሎስ በዚህ አገር ከቲቶ ጋር ለመገናኘት አቀደ፤ ቲቶ 3፥12። ካ. 7ሪ።

**ኒካዑ**፤ ከ610 እስከ 595 ያህል ከክ.ል. በግብጽ ላይ የነገሠ ፈርዖን። በ609 ከክ.ል. ከአሦር ጋር ለመዋጋት ወደ ሰሜን ሲዘምት ኢዮስያስ ተነሣበት። ኒካዑም እንዲመለስ አስጠነቀቀው፤ ኢዮስያስ ግን በመጊዶ ተዋግቶ ሞተ፤ 2ነገ. 23፥29-30፤ 2ዜ.መ. 35፥20-24። ኒካዑ ከሄደበት ሲመለስ የኢዮስያስን ልጅ ንጉሥ ኢዮአክስን ወደ ግብጽ እንዲሰደድ አደረገው፤ ወንድሙንም በእርሱ ምትክ አነገሠው፤ ግብርም እንዲከፍል አደረገ፤ 2ነገ. 23፥33-35፤ 2ዜ.መ. 36፥1-4። ፈርዖን ኒካዑ በ605 ከክ.ል. በከርከሚሽ ጦርነት በባቢሎን ኃይል ተሸነፈ፤ ኤር. 46፥2።

**ናሆም**፤ ትርጉሙ «መጽናናት» ማለት ነው። ስለ ነነዌ ውድቀት ራእይ ያየ፤ ለይሁዳ የምሥራችን የተናገረ ነቢይ፤ ናሆም 1፥1:15። ይኖርበት የነበረው ከተማ ስም ኤልቆሽ ይባል ነበር። ከይሁዳ ከተሞች አንዱ ይመስላል እንጂ በታው አልተረጋገጠም።

**የናሆም ትንቢት**፤ ናሆም ራእዩን ባየበት ጊዜ የግብጽ ከተማ ኖእ አሞን ወድቃ ነበር፤ ናሆም 3፥8-10። ትንቢቱን የተናገረው ከክ. ል. 663ና ነነዌ በወደቀችበት በ612 መካከል ነበር። የይሁዳ ንጉሥ ኢዮስያስ ሕዝቡን ቃል ኪዳን ባስገባበት ዘመን የነበረ ይመስላል፤ ናሆም 1፥15፤ 2ዜ.መ. 34፥31:32፤ 35፥1:18። ይህም ኤርምያስ ትንቢቱን ከጀመረ በኋላ ማለት ነው። በዮናስ ዘመን ነነዌ ከክፋቷ ተመልሳ ዳነች። ውሎ አድሮ ግን፥ ከጭካኔዋና ከስስቷ ብዛት የተነሣ ፍርድ የማይቀርላት ሆነ፤ ናሆም 3፥1-7።

አከፋፈል ፦

1. እግዚአብሔር የፍርድና የበቀል አምላክ ነው፤ ም. 1።
2. የነነዌ ጥፋት፤ ም. 2።
3. የነነዌ ጥፋት ምክንያት፤ ም. 3።

**ናርዶስ**፤ የናርዶስ ቅጠል፥ ደስ የሚያሰኝ ሽቱ፤ መ.መ. 1፥12፤ 4፥13። አይሁድ ናርዶስ ከሕንድ አገር ያስመጡ ነበርና ውድ ነበረ፤ ዮሐ. 12፥3-5።



የናርዶስ ቅጠልና ብልቃጦች

**ናሲብ**፤ «ጊባ» ይመ.

**ናስ**፤ (ነሐስ)፤ ከሰማያዊና ከአረንጓዴ ዐፈር ተነጥሮ የሚወጣ። ንጹሕ የሆነ ናስ መልኩ ቀይ ነው። ሠራተኞች በመዶሻ እየመቱት ዕቃ ይሠሩበት ነበር፤ ዘኁ. 21፥9፤ 1ነገ. 7፥14፤ 2ጢሞ. 4፥14። ከቆርቆሮ ጋር በእሳት ተቀላቅሎ ሲነጠር ግን ይጠነክርና መልኩ እንደ ወርቅ ይሆናል፤ 2ዜ.መ. 12፥10። መዳብ እንደዚሁም ከልስ ናስ ነው፤ ሕዝ.

22፥18። የመቅደስ ዕቃዎች ይሠሩበት ነበር፤ 1ነገ. 7፥45። ለመስተዋትና ለቤት ዕቃ ደግሞ ሰዎች ይጠቀሙበት ነበር፤ ሕዝ. 27፥13።



በሙሴ ዘመን ግብጻውያን በዚህ ዓይነት የናስ መስተዋት ይጠቀሙ ነበር

**የናስ መሠዊያ፤** ከግራር እንጨት የተሠራ፥ በናስ የተለበጠ፥ በእግዚአብሔር ማደሪያ መግቢያ የቆመ መሠዊያ። ባለ አራት ማዕዘን ሆኖ እንደ ባዶ ሣጥን ይመስል ነበር፤ ከላይም በናስ መረብ ተሸፍኗል። በየማዕዘኑ ቀንዶች ነበሩበት፤ ዘጸ. 27፥1-8። በዚህ መሠዊያ ካህናት ልዩ ልዩ የሚቃጠሉ መሥዋዕቶችን ያቀርቡ ነበር፤ ዘጸ. 30፥28፤ 1ነገ. 8፥64።



የናስ መሠዊያ

**ናቡቴ፤** አክዓብ የተመኘው በኢይዝራኤል የነበረው የወይን ቦታ ባለቤት። እንደ እግዚአብሔር ሕግ፥ ርስቱን አልሸጥም በማለቱ (ዘሌ. 25፥23)፥ በኤልዛቤል ትእዛዝ በሐሰት ተመስክሮበት ተወገረ፤ 1ነገ. 20፥1-16። እግዚአብሔርም በኤልያስ አፍ በአክዓብና በቤተ ሰዎቹ ላይ ፍርድ እንደሚያመጣ ተናገረ፤ 1ነገ. 20፥17-26፤ 22፥34-38፤ 2ነገ. 9፥24-26:30-37፤ 10፥10።



የናቡከደነፆር ምስል

**ናቡከደነፆር፤** ከ605 እስከ 562 ከክ.ል. በባቢሎን በከለዳውያን ላይ የነገሠ ንጉሥ። ትርጉሙ «ናባው አልጋ ወራሽነቱን ጠበቀ» ማለት ይሆናል። ናባው ከባቢሎን ጣዖታት አንዱ ነበረ፤ ኢሳ. 46፥1። ናቡከደነፆር ከባቢሎን ነገሥታት ታላቁ ነበረ። ብዙ መቅደስ ሠራ፤ ብዙም መሥዋዕትን ሠዋ። በባቢሎን ትልቅ የከተማን በርና መንገድ፥ ቅጥርና መስናም ሠራ። በ605 ከክ.ል. በከርከሚሽ የግብጽን ንጉሥ ፈርዖን ኒካዑን አሸነፈ፤ ግብጽም የያዘቻቸውን መንግሥታት ሁሉ ያዘ። ከእነርሱ አንዱ ይሁዳ ነበረና በኢዮአቄም ዘመን መንግሥት ይሁዳን ያዘ (ኤር. 46፥2፤ 2ነገ. 24፥1:7)፤ በዚያን ጊዜ ወደ ባቢሎን ከተማረኩት ወጣቶች አንዱ ዳንኤል ነበረ፤ ዳን. 1፥1-7። ኢዮአቄም ከዐመፀበት በኋላ ናቡከደነፆር ወደ ባቢሎን ሊማርከው አሰበ፤ 2ዜ.መ. 36፥6:7። ኢዮአቄም ግን ሳይማረክ ሞተና ልጁ ዮአኪን ከብዙ ሰዎች ጋር ወደ ባቢሎን ተማረከ፤ 2ነገ. 24፥10-16፤ 2ዜ.መ. 36፥10። ከእርሱም በኋላ ሴዴቅያስ ነገሠ፤ ቢነግሠውም በባቢሎን ንጉሥ ላይ ስላመፀ የባቢሎን ሠራዊት ኢየሩሳሌምን ከብበው ያዙአት፤ አቃጠሉአትም፤ ከጥቂቶችም በቀር ሕዝቡን ማረኩ፤ 2ነገ. 25፥1-22፤ 2ዜ.መ. 36፥17-21፤ ኤር. 39፥1-12፤ 52፥4-30። በኋላም ግብጽን ጭምር አሸነፉ። ናቡከደነፆር እነዚህን አገሮች የያዘው፥ ያሸነፈውም በእግዚአብሔር ፈቃድ ነበር፤ ኤር. 27፥6፤ 46፥13፤ ሕዝ. 29፥19:20። ጣዖታትን ያመልክ (ዳን. 1፥2)፥ ያምዋርትም ነበር (ሕዝ. 21፥21)፤ እግዚአብሔር ግን የፍርዱ መፈጸሚያ መሣሪያ አድርጎት «ባሪያዬ» አለው፤ ኤር. 25፥7-11፤ 32፥28። በትንቢተ ዳንኤል ስለ ናቡከደነፆር ሕልም (ዳን. 2)፤ ስላሠራውም ምስል (ዳን. 3)፤ ከእግዚአብሔር ኃይልም የተነሣ ስለ መገረሙ (ዳን. 2፥47፤ 3፥28:29)፤ ስለ ታላቅነቱና ስለደረሰበትም ውርደት እግዚአብሔርን ወደ ማክበር እንደደረሰ (ዳን. 4፥1-37)፥ ተጽፎ ይገኛል። ዳንኤልን አከበረ፤ ለኤርምያስም አስተያየት አደረገለት፤ ዳን. 2፥48፤ ኤር. 39፥11:12። ናቡከደነፆር በኵራቱ ምክንያት ተዋርዶ ሰባት ዓመት እንደ በሬ ሆነ። ይህም የእግዚአብሔር መቅሠፍት ነበረ። በኋላም አእምሮው ተመልሶለት እግዚአብሔርን አከበረ። ይህ ዓይነት በሽታ አልፎ አልፎ በሰዎች ላይ ይገኛል። ሰው በዚህ በሽታ ሲያዝ አውሬን ለመምሰል ይሞክራል፤ ዳን. 4፥28-34።



የናዝሬት የውሃ ጉድጓድ

**ናቡዘረዳን**፤ የናቡከደነፆር የዘበኞቹ አለቃ። ኢየሩሳሌምም በተሸነፈች ጊዜ በሕዝቡ ላይ ባለሥልጣን ነበረ። ድሆችንም በይሁዳ አስቀርቶ ሌሎቹን ወደ ባቢሎን አፈለሰ፤ 2ነገ. 25፥11:12:20፤ ኤር. 39፥9፤ 52፥12:15:16:29:30። እንደ ንጉሡም ትእዛዝ ለኤርምያስ ቸርነትን አሳየ፤ ኤር. 39፥11-14፤ 40፥1-6።

**ናባው፥ ነቦ**፤ 1. የባቢሎን የዕውቀት አምላክ፤ ኢሳ. 46፥1። 2. ከዮርዳኖስ ወንዝ በስተምሥራቅ ያለው ተራራ። ሙሴ ከዚህ ተራራ ላይ ሆኖ ከነዓንን አየ፤ ዘዳ. 34፥1።

**ናታኒም**፤ ለቤተ መቅደስ አነስተኛ ሥራ እንዲሠሩ የተመደቡ አገልጋዮች፤ 1ዜ.መ. 9፥2፤ ዕዝ. 2፥43፤ ነህ. 7፥46-56። ከከነዓን፥ ከገባዖንና ከምድያም የመጡ ይመስላል፤ ዘኍ. 31፥11-12:25-29፤ ኢያሱ 9፥23።

**ናታን**፤ ትርጉሙ «እግዚአብሔር ሰጥቷል» ማለት ነው። 1. በዳዊት ዘመን የነበረ ነቢይ። ዳዊት ቤተ መቅደስ ለመሥራት ባሰበ ጊዜ፥ ናታን፥ እግዚአብሔር ለአንተ ቤት ይሠራልሃል፤ ለእርሱ ቤት የሚሠራው ግን ሰሎሞን ይሆናል አለው፤ 2ሳሙ. 7፤ 1ዜ.መ. 17። ስለ ቤተ መቅደሱ የሙስጋና ዝግጅት ዳዊትን አዘዘ፤ 2ዜ.መ. 29፥25። ዳዊት የኦርዮን ሚስት ከወሰደ በኋላ ናታን ገሠጸው፤ 2ሳሙ. 12፥1-14። አዶንያስ ሳይሆን ሰሎሞን ከአባቱ በኋላ እንዲነግሥ ካደረጉት አንዱ ነበረ፤ 1ነገ. 1፥8-46። ስለ ዳዊትና ስለ ሰሎሞን ዘመነ መንግሥት ታሪክ ጻፈ፤ 1ዜ.መ. 29፥29፤ 2ዜ.መ. 9፥29። 2. ከዳዊት ልጆች አንዱ፤ 2ሳሙ. 5፥14፤ ዘካ. 12፥12፤ ሉቃ. 3፥31። በ1ነገ. 4፥5 የተጠቀሰው የዳዊት ልጅ ወይም ነቢዩ እንደሆነ አናውቅም።

**ናትናኤል**፤ «የእግዚአብሔር ስጦታ» ማለት ነው። የክርስቶስ ደቀ መዝሙር። ናትናኤል ተብሎ የተጠራው በርተሎሜዎስ እንደሆነ ብዙዎች ያምናሉ። ፊልጶስ ወደ ኢየሱስ ጠራው፤ ዮሐ. 1፥44-52፤ 21፥2።

**ናዖስ**፤ 1. የአሞን ንጉሥ። በኢያቢስ ገለዓድ ላይ በዘመተ ጊዜ ሳያል አሸነፈው (1ሳሙ. 11፥1-11)፥ በኋላም የዳዊት ወዳጅ ሆነ፤ 2ሳሙ. 10፥2። 2. የጽሩያና የአቢግያ አባት፤ 2ሳሙ. 17፥25።

**ናዝራዊ**፤ ትርጉሙ የተቀደሰ፥ የተለየ ማለት ነው። አንድ እስራኤላዊ ልዩ አገልግሎት ለመስጠት ሲፈልግ የናዝራዊ ስእለትን ይሳል ነበር። ናዝራዊ ሲሆን ከሚያሰክር መጠጥ፥ ጠጕሩን ከመቁረጥ፥ ሬሳ ከመንካት ራሱን ይከለክል ነበር። የስእለቱ ዘመን ሲፈጸም ጠጕሩን ቈርጦ ልዩ ልዩ መሥዋዕትና ሥርዓት ይፈጽማል። የስእለቱ ዘመን ቢያንስ ለሠላሳ ቀናት፥ ቢረዝምም ሙሉው የሕይወት ዘመን ሊሆን ይችል ነበር፤ ለምሳሌ ሶምሶን ናዝራዊ ነበረ፤ ዘኍ. 6፥1-21፤ መሳ. 13፥5-7፤ አሞጽ 2፥11:12። ጌታችን ኢየሱስ ናዝራዊ ተብሎ ቢጠራም፥ ይህ በናዝሬት ማደጉንና መኖሩን እንጂ በኦሪት ሕግ መሠረት ናዝራዊ መሆኑን አያመለክትም፤ ማቴ. 2፥23፤ ዮሐ. 1፥47፤ ኢሳ. 53፥3።

**ናዝሬት**፤ ከገሊላ ባሕር በስተምዕራብ 25 ኪ.ሜ. ርቆ በዛብሎን ነገድ ድርሻ ውስጥ በተራራማ አገር ላይ የተመሠረተ ከተማ። ናዝሬት በብ.ኪ. አልተጠቀሰም፤ በአ.ኪ. ዘመንም ቦታው ወደ አገሩ ጠረፍ ስለሆነ ዝቅተኛ ግምት ይሰጠው ነበር፤ ዮሐ.

1፥47። ናዝሬት የዮሴፍና የማርያም መኖሪያ ከተማ ነበረ። ኢየሱስ በዚህ ተፀነሰ፤ በኋላም አደገበት፤ ሉቃ. 1፥26:27፤ 2፥39:40:51። ኢየሱስ የማስተማር ሥራውን ከጀመረ በኋላ አንድ ጊዜ ወደ ናዝሬት መጣ፤ ሕዝቡ ግን አልተቀበሉትም፤ ሉቃ. 4፥16-30። ዛሬ 30 ሺህ ያህል ሰዎች በናዝሬት ይኖራሉ። ካ. 5ለ።

**ናይን፤** ከደብረ ታቦር በስተደቡብ ሦስት ኪ.ሜ. ርቆ የሚገኝ ከተማ። ኢየሱስ በናይን የአንዲትን መበለት ልጅ ከሞት አስነሣ፤ ሉቃ. 7፥11-16። ካ. 5ለ።

**ናዳብ፤** 1. የአሮንታላቅ ልጅ፤ ዘጸ. 6፥23። ወደ እግዚአብሔር ወደ ሲና ተራራ ከወጡት አንዱ ነበረ፤ ዘጸ. 24፥1:9-11። ከአባቱና ከወንድሞቹም ጋር ለክህነት ተለየ፤ ዘጸ. 28፥1፤ ዘሌ. 8 እና 9። እርሱና ወንድሙ አብዩድ ዕጣን ባጠኑ ጊዜ ከሥርዓት ውጭ ያልታዘዘ እሳት አቅርበው ስላጠኑ፥ ወዲያውኑ ተቀሥፈው ሞቱ፤ ዘኍ. 3፥2-4፤ ዘሌ. 10። «አብዩድ» ይመ.

2. ከ910-909 ከክ.ል. የነገሠ ሁለተኛው የእስራኤል ንጉሥ፤ 1ነገ. 14፥20። ባእስም ገደለው፤ 1ነገ. 15፥25-32።

**ናፍቆት፤** ጽኑ ምኞት፥ የሚወዱትን በፍቅር ማሰብ። ብዙ ጊዜ ለመልካም ነገር ነው፤ 2ቆሮ. 7፥7:11፤ 1ተሰ. 2፥17፤ 3፥6።

**ኔሮን (ኔሮ)፤** ከ54-68 ዓ.ም. የነገሠ የሮም ቄሣር። ጨካኝ ገዥ ነበረ። በሮም በ64 ዓ.ም. የተነሣውን ትልቅ የእሳት አደጋ ምክንያት አድርጎ ብዙ ክርስቲያኖችን ገደለ። በሐ.ሥ. 25፥11 እና በፊል. 4፥22 «ቄሣር» የሚለው ቃል ኔሮንን ያመለክታል።



ኔሮ (ኔሮን) ቄሣር በድንጋይ ላይ የተቀረጸ

**ኔፊሊም፤** ረጃጅም ኃያላን ሰዎች፤ ዘፍ. 6፥4፤ ዘኍ. 13፥32:33። እነዚህ ኃያላን ፍጥረቶች የወደቁ መላእክት ናቸው ብለው የሚተረጉሙ ሊቃውንት አሉ።

**ንስሐ፤** የቃሉ ዋና ትርጒም በሙሉ ልብ መለወጥና መመለስ ማለት ነው። አሳብ ከተለወጠ አድራጎትም ይለወጣል። በዚህ ቃል ነቢያት ሕዝቡን ያስጠነቅቁ ነበር፤ ኢሳ. 46፥8፤ ሕዝ. 18፥30።

የዮሐንስና የጌታችን ኢየሱስ የትምህርት መጀመሪያ «ንስሐ ግቡ» የሚል ነው፤ ማቴ. 3፥1:2፤ 4፥17። ንስሐ የሚገባ ስለፈጸመው ኃጢአት አሳብ ያለው ሁሉ ይለወጣል። መጀመሪያ መንፈስ ቅዱስ ስለ ኃጢአቱ ይወቅሰዋል፤ ዮሐ. 16፥8። ከኃጢአቱ ይመለሳል፤ ይቅርታም ይጠይቃል፤ ምሳ. 28፥13፤ ሉቃ. 15፥11-24።

እውነተኛ ንስሐ ከዓለማዊ ጸጸት የተለየ ነው (2ቆሮ. 7፥10)፤ በሥራም ለውጥ ይታያል፤ ማቴ. 3፥8፤ ሐ.ሥ. 26፥20። ዓለማዊ ጸጸት ተስፋ መቍረጥን ሲያስከትል፥ እውነተኛ ንስሐ ግን በእምነትና በተስፋ ከእግዚአብሔር ምሕረት መለመንን ያሳያል፤ ማቴ. 27፥4-5፤ 2ቆሮ. 7፥10። ሰው ንስሐ ሲገባ ኃጢአቱ ይሰረያል፤ ይደመሰሳልም፤ ሐ.ሥ. 2፥38፤ 3፥19። ንስሐ መግባት የመዳን መጀመሪያ እርምጃ ነው፤ ከእምነትም ጋር የተያያዘ ነው፤ ማር. 1፥14፤ ሐ.ሥ. 2፥38፤ 20፥20። ሰዎች ሁሉ ንስሐ እንዲገቡ ታዝዟል፤ ለንስሓም ጊዜ ተሰጥቶአቸዋል፤ ሐ.ሥ. 11፥18፤ 17፥30፤ 2ጴጥ. 3፥9። አማኝ ኃጢአትን ሲሠራ ቶሎ ንስሐ እንዲገባ ታዝዟል፤ ራእ. 2፥5:16:21፤ 3፥19። ሰው የእግዚአብሔርን ቃል ቸል ካለ በኋላ እንዲሁ ሲመቸው ንስሐ ሊገባ አይችልም። ንስሐ የእግዚአብሔር ስጦታ ነውና፤ 2ጢሞ. 2፥25፤ ዕብ. 6፥4-6፤ 12፥17። «መናዘዝ»፥ «መመለስ» ይመ.

**ንስር፤** ትልቅ ነጣቂ አሞራ። የኃይልና የፍጥነት፥ እንዲሁም ያንዳንድ መንግሥታት ምሳሌ፤ ዘጸ. 19፥4፤ 2ሳሙ. 1፥23፤ ኢሳ. 40፥31፤ ሕዝ. 17፥3-7። «ወፎች» ይመ.



ንስር (አሞራ)

**ንቀት፤** በምክንያት ወይም አለ ምክንያት ሰውን ዝቅ አድርጎ መመልከት፥ ማዋረድ። የእግዚአብሔርን ቃል መናቅ ቅጣትን ያስከትላል፤ 1ሳሙ. 15፥23፤ መዝ. 123፥3:4፤ ሚል. 2፥9፤ ሉቃ. 23፥11፤ ሮም 14፥10፤ 2ቆሮ. 10፥10።

**ንቅሳት፤** ነቀሰ፤ በልዩ ልዩ ምልክት የቆዳን መልክ መለወጥ። ንቅሳት በሙሴ ሕግ የተከለከለ ነበር፤ ዘሌ. 19፥28።

**ንዋየ ቅድሳት፤** ለቤተ መቅደስ አገልግሎት የተቀደሰ (የተለየ) ዕቃ። ለማንኛውም የቤተ መቅደስ ዕቃ ሁሉ አጠቃላይ ስም ነው፤ 1ዜ.መ. 26፥26፤ 28፥12።

**ንዕማን፤** ለምጻም የሆነ የሶርያ ሠራዊት አለቃ። በአንዲት የተማረከች እስራኤላዊት ብላቴና ቃል ተመክሮ ከለምጹ ለመፈወስ ወደ ሰማርያ ሄደ። ኤልሳዕም እንዳዘዘው በዮርዳኖስ ወንዝ ታጠበና ነጻ፤ እግዚአብሔር የምድር ሁሉ አምላክ መሆኑን አመነ፤ 2ነገ. 5፤ ሉቃ. 4፥27።

**ንዳድ፤** በልዩ ልዩ ትንሾች አማካይነት የሚተላለፍ እንደ ወባ ያለ የሚያልብና የሚያንቀጠቅጥ በሽታ፤ ዘዳ. 28፥22፤ ማቴ. 8፥15፤ ዮሐ. 4፥52፤ ሐ.ሥ. 28፥8። «በሽታ» ይመ.

**ንጉሠ ነገሥት፤** ምድራዊ ንጉሥ በበታቹ ነገሥታት ኖረው እርሱ የበላይ ሲሆን፥ ንጉሠ ነገሥት ይባላል። እግዚአብሔር የነገሥታት ጌታ፥ የነገሥታት ንጉሥ ተብሎ ይከበራል፤ ዳን. 2፥47፤ 1ጢሞ. 6፥15። ክርስቶስ የዓለም ጌታ ስለሆነ የነገሥታት ንጉሥ ተብሎ ይጠራል፤ ራእ. 17፥14፤ 19፥16።

**ንጉሥ፤** በአንድ ሕዝብ ላይ ሙሉ ሥልጣን ያለው። በአብርሃም ዘመን አብዛኛውን ጊዜ ንጉሥ አንድን ከተማና አቅራቢያውን ይገዛ ነበር፤ ዘፍ. 14፥1:2። በብ.ኪ. የብዙ ነገሥታት ታሪክ ይተረካል። በአ.ኪ. ሄሮድስ ንጉሥ ይባላል፤ ነገር ግን መንግሥቱን የተቀበለው ከቄሣር ነበር፤ ማቴ. 2፥3። ቄሣርም ንጉሥ ተብሎ ተከበረ፤ ዮሐ. 19፥12፤ ሐ.ሥ. 17፥7።

በእስራኤል ላይ እግዚአብሔር ነገሠ። ነገር ግን ሕዝቡ እንደ አሕዛብ ሁሉ ንጉሥ ፈለጉ፤ ሳኦልም ተቀባና ነገሠባቸው፤ 1ሳሙ. 8፥5-7። ሳኦል ስለወደቀ ዳዊት ተተካ። እርሱም እግዚአብሔርን ንጉሤ ብሎ አከበረው፤ መዝ. 5፥2፤ 10፥16። የዳዊት መንግሥት ትልቅ ሆነ፤ ከእርሱ በኋላ እስከ ሴዴቅያስ ድረስ ብዙ ነገሥታት ነበሩ። ከእነርሱ ግን አንዳንዶች ብቻ እግዚአብሔርን ተከተሉ። ስለዚህም እግዚአብሔር በጽድቅ የሚያነግሠውን እንደሚያስነሣ ነቢያት ተነበዩ፤ ኢሳ. 32፥1፤ 33፥17፤ ኤር. 23፥5። ሕዝቡም «የዳዊት ልጅ» የተባለውን ሲጠባበቁ ቆዩ፤ ማቴ. 21፥8:9፤ ዮሐ. 6፥15። ኢየሱስ የትንቢቱን ቃል ፈጸመ። ነገር ግን መንግሥቱ ጊዜያዊና ምድራዊ ሳይሆን፥ ወደፊት የሚገለጥና ለዘለዓለም ጸንቶ የሚኖር ነው፤ ዮሐ. 18፥36፤ 1ቆሮ. 15፥24-28፤ 2ጴጥ. 1፥11።

**የንጉሥ ጐዳና፤** ከዔጽዮንጋብር በኤዶም፥ በሞዓብና በአሞን በኩል ወደ ሶርያ የሚወስደው የታወቀው መንገድ፤ ዘኍ. 20፥17፤ 21፥22። ዛሬ አውራ ጐዳናው ከጥንታዊው መንገድ ጋር አልፎ አልፎ ይገናኛል።

**የንጋት ኃይል፤** ቃሉ ምናልባት የዳዊት መዝሙር የተዘመረበትን የዜማ ስልት ያመለክት ይሆናል፤ የመዝ. 22 ርእስ።

**የንጋት ኮከብ፤** ሌሊት ከንጋት በፊት ከሌሎች ከዋክብት ሁሉ ይልቅ የሚያበራ ኮከብ፥ የንጋት መልእክተኛ። ኢየሱስ ክርስቶስ የዘለዓለም ብርሃን አብሳሪ በመሆኑ፥ የዚህን ኮከብ ስያሜ ለራሱ መጠሪያ አድርጎ ተጠቅሞበታል፤ ራእ. 2፥28፤ 22፥16፤ 2ጴጥ. 1፥19።

**ንግሥት፤** 1. ከነገሥታት ወገን ንጉሥ የሚሆን ሲታጣ አገርን የምታስተዳድር ሴት ንግሥት ትባላለች። ከንገሥታት ሁሉ የታወቁት ንግሥተ ሳባ (1ነገ. 10፥1)፥ ጎቶልያ (2ነገ. 11፥3)፥ ሕንደኬ (ሐ.ሥ. 8፥27) ናቸው። 2. የንጉሥ ሚስት። በእስራኤል ንግሥት ወደ መንግሥት ጉዳይ ብዙ ጊዜ አትገባም ነበር። ሆኖም ቤርሳቤህና ኤልዛቤል ነገሥታትን ሲቀሰቅሱ እናያለን፤ 1ነገ. 1፥15-31፤ ም. 20። በእስራኤል ቤተ መንግሥት ብዙውን ጊዜ የንጉሥ እናት ከሴቶች ሁሉ በላይ እንደ ታላቅ ሆና ትቈጠር ነበር፤ 1ነገ. 2፥19፤ 15፥2:10:13፤ ኤር. 13፥18። ምናልባት የሰማይ ንግሥት የተባለችው የከነዓን ጣዖት አስታሮት ትሆን ይሆናል፤ ኤር. 7፥18፤ 44፥17-25። «እቴጌ» ይመ.

**ንግድ፤** በብ.ኪ. አብርሃም ይኖርባት የነበረችው የከለዳውያን ዑር የተባለችው ከተማ በንግድ ገናና ነበረች። ግብጽም ከጥንት ጀምሮ ታላቅ የንግድ አገር ነበረች፤ ዘፍ. 37፥25። ጢሮስ ትልቅ የንግድ ከተማ ነበረችና በንጉሥ ሰሎሞን ዘመነ መንግሥት እስራኤል ከጢሮስና ከሲዶና ጋር ትነግድ ነበር፤ 1ነገ. 5፥6፤ 9፥27:28፤ 10፥11:22፤ ሕዝ. 27፥12-25። እስራኤል ግን በተለይ የእርሻ አገር ነበረች።



ሻጭና ገዥ

በአ.ኪ. ዘመን በእስራኤል አገር ይካሄድ ከነበረው የንግድ ሥራ አብዛኛው በሮምና በኢጣልያ እጅ ውስጥ ነበረ። ስለዚህ የሮም ሰዎች ብዙ መንገዶችን ሠሩ። ከእነዚህም አንዳንዶቹ እስከ ዛሬ ድረስ አገልግሎት በመስጠት ላይ ይገኛሉ።

በዱሮ ዘመን ከአገር ወደ አገር መጓዝ በጣም አስቸጋሪና አስጊ ነበረ፤ 2ቆሮ. 11፥25-27፤ ሐ.ሥ. 27 ና 28። «ጎንዘብ» ይመ.

**ንጥር**፤ የሮም መንግሥት የክብደት መለኪያ፤ ዮሐ. 12፥3፤ 19፥39። «ክብደት» ይመ.

**ንጹሕ**፤ መንጻት፤ ቤተ እስራኤል ቅዱስ እንዲሆን ተጠራ፤ ዘሌ. 11፥44:45። ሰው ርኩሰትን በሚያስከትሉበት ምክንያቶች መጠን ብዙ ዓይነት የመንጻት ሥርዓት ነበረ። መንጻት ሰውነትንና ልብስን በማጠብ (ዘሌ. 15፥8-11)፥ የረከሰውን ነገር በማቃጠል (ዘሌ. 13፥52-57)፥ መሥዋዕትን በማቅረብ (ዘሌ. 12፥6-8) ይፈጸማል። በዚህም ሥርዓት መሠረት ሰው ከኃጢአቱ በእግዚአብሔር እንደሚነጻ ተነግሯል፤ መዝ. 51፥7፤ ሕዝ. 36፥25። አ.ኪ. ግን ኢየሱስ በመስቀል ላይ በመሞቱ የደኅንነት መሥዋዕታችን ስለሆነ፥ ከኃጢአት መንጻት የሚገኘው በክርስቶስ ደም እንደሆነ ያስተምራል፤ 1ዮሐ. 1፥7-9። «ርኩስ» ይመ.

**ንፍታሌም**፤ የስሙ ትርጉም «የሚታገል» ማለት ነው። የራሔል ገረድ ባላ የወለደችው የያዕቆብ ስድስተኛ ልጅ፤ ዘፍ. 30፥7:8። ከእስራኤል ነገዶች የአንዱ አባት ሆነ፤ በስሙም ነገደ ንፍታሌም ተብሎ ተጠራ። ያዕቆብ በሚዳቋ መሰለው (ዘፍ. 49፥21)፤ ሙሴም በሞገስ ጠግቧል አለው፤ ዘዳ. 33፥23። በከነዓን የደረሰውም የርስት ድርሻ በገሊላ ባሕር በስተምዕራብ ነበረ፤ ኢያሱ 19፥32-39፤ ኢሳ. 9፥1:2፤ ማቴ. 4፥13-17። በዚህ አገር ኢየሱስ ብዙ ዘመንኖረ፤ አስተማረም፤ ኢሳ. 9፥1፤ ማቴ. 4፥13-17። ባርቅ ከንፍታሌም ነገድ ተወለደ፤ መሳ. 4፥6፤ 5፥18። ካ. 3ሀ። «ነገድ» ይመ.

**ኖራ**፤ የነጭ ድንጋይ ዱቄት። በግብጽ፥ በእስራኤል፥ በባቢሎን፥ በሌሎችም አገሮች ቤቶችና ሐውልቶች በኖራ ይለሰኑ ነበር፤ ዘዳ. 27፥2:4፤ ዳን. 5፥5፤ ማቴ. 23፥27፤ ሐ.ሥ. 23፥3።

**ኖብ**፤ በኢየሩሳሌም አጠገብ የነበረ ከተማ። ዛሬ ቦታው በኢየሩሳሌም በአዲሱ ከተማ ውስጥ ይገኛል። ታቦቱ ከሴሎ ከተማረከ በኋላ ካህናት በኖብ ተቀመጡ። የኖብ ካህናት ዳዊትን ስለረዱ ሳኦል አስፈጃቸው፤ 1ሳሙ. 4፥11፤ 21፥1-9፤ 22፥11-23።

**ኖኅ**፤ ከአዳም ልጅ ከሴት ትውልድ ተወለደ፤ ዘፍ. 5፥28:29። በእምነት ከነቤተሰቦቹ ከጥፋት ውሃ ዳነ፤ ዘፍ. 7፥1:23፤ ዕብ. 11፥7። ክፉ በነበረው ዘመን ኖኅ ብቻ ጻድቅ ነበረ፤ እንደ አያቱም እንደ ሄኖክ ከእግዚአብሔር ጋር አካሄዱን አደረገ፤ ዘፍ. 6፥9፤ 5፥24። 500 ዓመት ከሆነው በኋላ ሴምን፥ ካምን፥ ያፌትንም ወለደ፤ ዘፍ. 5፥32። እግዚአብሔር የጥፋትን ውሃ በምድር ላይ እንደሚያመጣ አስጠነቀቀው፤ ኖኅም ቤተ ሰቡና ሕያው ነፍስ ካላቸው ተባትና እንስት ፍጥረታት በየዓይነቱ የሚድኑበትን መርከብ እንዲያዘጋጅ ታዘዘ፤ ዘፍ. 6፥13-22። መርከቡም እስኪዘጋጅ እግዚአብሔር ታገሠ፤ ኖኅም ጽድቅን ያስተምር ነበር፤ ዘፍ. 6፥3፤ 1ጴጥ. 3፥20፤ 2ጴጥ. 2፥5።

ኖኅ 600 ዓመት በሆነው ጊዜ የጥፋት ውሃ መጣ፤ ከእርሱና ከእርሱም ጋር ወደ መርከብ ከገቡት በቀር የዳነ አልነበረም፤ ዘፍ. 7። እግዚአብሔር ኖኅን አስቦ የጥፋትን ውሃ ከምድር ላይ አደረቀ፤ ኖኅ ወጥቶ መሥዋዕትን ሠዋ፤ ዘፍ. 8። እግዚአብሔር ምድርን ዳግመኛ በውሃ እንዳያጠፋ ተስፋ ሰጥቶ ከኖኅና ከሕያው ፍጥረታት ሁሉ ጋር ቃል ኪዳን ገባ፤ ዘፍ. 8፥21:22፤ 9፥8-17። ኖኅንና ልጆቹን፥ ብዙ ተባዙ ብሎ ባረካቸው፤ በእነርሱ ምድር ሁሉ ተሞላች፤ ዘፍ. 9፥1-7:19፤ 10። ኖኅ ወይን ተከለ፤ ሰክሮም ሳለ ካም የአባቱን ነውር አወራ፤ ሴምና ያፌት ግን አለበሱት። ኖኅ ሴምንና ያፌትን ባረካቸው፤ ከካም ልጆች አንዱን ከነዓንን ግን ረገመው፤ ዘፍ. 9፥20-27። ኖኅ 950 ዓመት ሲሆነው ሞተ፤ ዘፍ. 9፥29። «የጥፋት ውሃ» ይመ.

**የኖኅ መርከብ**፤ ይህች መርከብ በውሃ ላይ እንድትንሳፈፍ እንጂ ከአንድ ቦታ ወደ ሌላ እንድትሄድ ሆና አልተሠራችም። ርዝመትዋ 150፥ ወርድዋ 25፥ ከፍታዋ 15 ሜትር ነበረ። ኖኅ ከመርከቢቱ ከወጣ በኋላ ምን እንደሆነች አይታወቅም፤ ዘፍ. 6-8።

**ኖእ**፤ የደቡብ ግብጽ ዋና ከተማ። አሞን የተባለው ጣዖት መቅደስ በኖእ ነበረ፤ ኤር. 46፥25፤ ሕዝ. 30፥14-16፤ ናሆም 3፥8-10።

**አህያ**፤ በእስራኤል የሚገኘው አህያ ረጅም ስለሆነ ለጭነት ብቻ ሳይሆን ለኮርቻ ከብትነትም ያገለግል ነበር፤ ዘፍ. 42፥26፤ 1ነገ. 13፥13፤ ማቴ. 21፥4-7። የበለዓምም አህያ በሰው ቋንቋ ተናግራ ወቀሰችው፤ ዘኍ. 22፥28።

**አሆማ**፤ የዛፍ ስም፤ የዋንዛ ዓይነት እንጨት፤ ሆሴዕ 4፥13።

**አለላ**፤ በጣም ቀይ የሆነና የማይለቅ ቀለም፤ ኢሳ. 1፥18።

**አለንጋ**፤ ብዙ ጊዜ ከቆዳ ሊሠራ የሚችል ለእንስሳ መቀስቀሻ ወይም መንጃ (ምሳ. 26፥3፤ ናሆም 3፥2)፥ ለሰው ምርመራና መቅጫ የሚያገለግል፥ የጽኑ አገዛዝ ምሳሌ፤ 1ነገ. 12፥11። «ግርፋት» ይመ.

**አለኸለኸ**፤ ከሙቀት፥ ከውሃ ጥምና ከረሀብ የተነሣ ምላስን አውጥቶ መተንፈስ። ለውሻና ለሌላም አውሬ ይነገራል፤ ኢዩ. 1፥20።

**አላባሽ አግሬ ጋሻ**፤ ሰፋት ያለው ከእግር እስከ ራስ የሚለበስ (የሚመከት) የጦር መሣሪያ፥ መከላከያ፤ 1ነገ. 10፥16፤ 2ዜ.መ. 14፥8፤ ሕዝ. 39፥9። «የጦር መሣሪያ» ፥ ገጽ 144 ይመ.

**አሌፋት**፤ የዕብራይስጥ ፊደላት ከአሌፍ እስከ ታው ድረስ በጠቅላላ አሌፋት ይባላሉ። አልፍ አልፍ


አላባሽ አግሬ ጋሻ

በዕብራይስጡ ብ.ኪ. ውስጥ ደራሲዎች አንደኛውን መሥመር በአሌፍ ፊደል፥ ሁለተኛው በቤት ፊደል፥ ሦስተኛውም በጋሜል ፊደል ... ወዘተ እንዲነሣ አድርገዋል፤ መዝ. 119፤ ሰ.ኤ. 1፤ 2፤ 3፤ 4፤ 5። «ዕብራይስጥ» ይመ.

**አሌፍ፤** የዕብራይስጥና የሌሎችም የሴም ቋንቋዎች የመጀመሪያ ፊደል ስም፤ መዝ. 119፥1፤ ሰ.ኤ. 1፥1፤ 2፥1። «ዕብራይስጥ»፥ «ግዋም» ይመ.

**አልማዝ፤** ከሁሉ ይልቅ ዋጋ ያለው የከበረ ድንጋይ። ፈርጡ ብዙ ገጽ ወይም ቅርጽ ያለው፥ እንደ መስተዋት ብርሃንን የሚያስተላልፍ ዕንቍ ከማዕድናት ሁሉ ጠንካራ፥ ጽኑና የማይሰበር ነው፤ ዘጸ. 28፥18፤ ሕዝ. 3፥9፤ ዘካ. 7፥12።

**አልቅት፤** (አለቅት)፤ በውሃ ውስጥ የሚኖር ትል። ከብቶች ውሃ ሲጠጡ በአፋቸው ገብቶ ደማቸውን የሚመጥ፤ ምሳ. 30፥15።

**አልባስጥሮስ፤** የክብር ዕቃ የሚሠራበት ነጭ ድንጋይ፤ ማቴ. 26፥7።

**አልቦ፤** ከወርቅ፥ ከሌላም ማዕድን የሚሠራ በእግር ላይ የሚታሰር ጌጥ፤ ዘኍ. 31፥50፤ ኢሳ. 3፥18።

**አልቦ፥ አልባ፤** ባዶ፥ ያለ ... ማለት ነው። ለምሳሌ «ልጅ አልባ ቀረሁ» (ዘፍ. 42፥36)፥ ያለ ልጅ ቀረሁ ማለት ነው። «ቤቶች ሰው አልቦ ሆኑ» (ኢሳ. 6፥11)፥ ያለ ሰው ሆኑ ማለት ነው።

**አልዓዛር፤** ትርጕሙ «እግዚአብሔር ረድቶአል» ማለት ነው። በዚህ ስም ሦስት የታወቁ ሰዎች ተጠርተዋል።

1. የአሮን ሦስተኛ ልጅ፤ ዘጸ. 6፥23። በሲና ተራራ ኦሪት ለእስራኤል ልጆች በተሰጠ ጊዜ አሮንና አራቱ ልጆቹ ካህናት እንዲሆኑ እግዚአብሔር መድቧቸው ነበር፤ ዘጸ. 28፥1-2። ልጆቹም ናዳብ፥ አብዩድ፥ አልዓዛርና ኢታምር የተባሉት ናቸው። ናዳብና አብዩድ በአገልግሎታቸው ያልታዘዘ እሳት በማቅረብ እግዚአብሔርን አሳዘኑና በሞት ተቀጡ፤ ዘሌ. 10፥1-2። ከዚህም የተነሣ በእስራኤል የክህነት አገልግሎታቸውን በመቀጠል ለተከታዮች የክህናት ትውልዶች አባቶች የሆኑት አልዓዛርና ኢታምር ናቸው። አሮን ከሞተ በኋላ ሊቀ ካህናት የሆነው አልዓዛር ነው። የሙሴ ረዳትም ሆነ፤ ዘኍ. 3፥32፤ 20፥28፤ 26፥1-2፤ 31፥13-54፤ 32፥28። ዐሥራ ሁለቱ የእስራኤል ነገዶች የከነዓንን አገር በተከፋፈሉ ጊዜ ኢያሱን በሥራው የረዳው አልዓዛር ነው፤ ኢያሱ 14፥1፤ 19፥51። በከነዓንም አገር በሞት ከዚህ ዓለም ተለይቶ ጊብዓ በተባለው ቀበሌ ተቀበረ፤ ኢያሱ 24፥33።

2. ኢየሱስ ከሙታን ያስነሣው የማርያምና የማርታ ወንድም፤ ዮሐ. 11፤ 12፥1-19።

3. ጌታችን በተናገረው ምሳሌ ውስጥ ከሀብታሙ ደጅ የሞተው፥ ከሞተም በኋላ በአብርሃም ዕቅፍ የተቀመጠው ድሀ፤ ሉቃ. 16፥19-31።

**አልጋ፤** በጥንት ጊዜ ድሆች ልብሳቸውን እንደለበሱ ከመሬት ላይ ሲተኙ፥ መጠነኛ ሀብት ያላቸው ደግሞ ከቆዳ፥ ከሣርና ከሰሌን በተሠራ ምንጣፍ ይተኙ ነበር። ሀብታሞች ግን ከእንጨትና ከብረት ከሌላም ታላላቅ አልጋዎችን ሠሩ፤ ዘዳ. 3፥11፤ አስ. 1፥6፤ አሞጽ 6፥4።

**አልጫ፤** ጣዕም የሌለው፥ የማይጠቅም ነገር፤ ማቴ. 5፥13፤ ሉቃ. 14፥34።

**አልፋ፤** የግሪክ ቋንቋ የመጀመሪያ ፊደል ስም፤ ራእ. 1፥8፤ 22፥13።

**አሕሻዊሮስ፤** የዳርዮስ አባት፤ ዳን. 9፥1። «አርጤክስስ» ይመ.

**አሕዛብ፤** አሕዛብ ማለት ሕዝቦች ማለት ነው፤ ዘፍ. 10፥5። በመ.ቅ. ቃሉ በተለይ ከእስራኤል ወገን ላልሆኑ ተነግሯል፤ ኢሳ. 11፥10፤ ማቴ. 10፥5፤ ሮም 9፥24። አሕዛብ ሕግን ስላልጠበቁ ለጣዖትም ስለሠው አይሁድ እንዳይረክሱ ከእነርሱ ጋር አይተባበሩም ነበር። በክርስቶስ መንጌል ሲያምኑ ግን አይሁድና አሕዛብ አንድ ይሆናሉ፤ ሐ.ሥ. 10፥9-16:28:34:35፤ 11፥2:3:17:18፤ ሮም 3፥29:30፤ ኤፌ. 2፥11-22።

**አመል (ዐመል)፤** ጠባይ፥ አካሄድ፥ ግብረ ገብነት፤ 1ቆሮ. 15፥33።

**አመልማሎ፤** የጥጥ ወይም የበግ ጠጕር (የሱፍ) ጥቅልል። መጀመሪያ ባዘቶ፥ ቀጥሎ ንድፍ፥ በመጨረሻ አመልማሎ ይሆንና ይፈተላል፤ ምሳ. 31፥19።

**አመዳይ፤** ለስላሳና በጣም ነጭ የሆነ በብርዳም አገርና በተራራ ላይ ለብዙ ቀን የሚተኛ ውርጭ፤ ዘኍ. 12፥10፤ 2ሳሙ. 23፥20፤ ኢሳ. 1፥18። የሚወርድበት ወራት አለው (1ዜ.መ. 11፥22፤ ኢዮብ 38፥29)፤ ደግሞ ውሃ ቀዝቅዞ ሲረጋ አመዳይ ሊባል ይችላል፤ ኢዮብ 6፥16።

**አመድ፤** በእሳት የተቃጠለ እንጨት ትራፊ። የጭንቀት (መዝ. 102፥9)፥ የንስሐ (ማቴ. 11፥21፤

ዮናስ 3፥6)፥ ራስን የማዋረድና የትሕትና ምሳሌ ነው፤ ዘፍ. 18፥27፤ ኢዮብ 30፥19። ሰው በአመድ ላይ ቢተኛ ወይም በራሱ ላይ አመድ ቢነሰንስ ራሱን እንደማይረባ ነገር አድርጎ ቈጠረ ማለት ነው፤ ዳን. 9፥3፤ 2ሳሙ. 13፥19።

**አሚናዳብ (አቢናዳብ)፤** የእግዚአብሔር ቃል ኪዳን ታቦት ከፍልስጥኤማውያን እጅ ወደ እስራኤል ሲመለስ ሀያ ዓመት የተቀመጠበት ቤት ባለቤት፤ 1ሳሙ. 7፥1፤ 2ሳሙ. 6፥3።

**አማለደ፤** «ምልጃ» ይመ.

**አማሌቃውያን፤** ከአማሌቅ የተገኙ ነገዶች ከእስራኤል አገር በስተደቡብ በኩል ይኖሩ ነበር። ከሙሴ እስከ ሕዝቅያስ ዘመን ድረስ እስራኤልን ይቃወሙ ነበር፤ ዘጸ. 17፥8-13፤ መሳ. 3፥13፤ 6፥3፤ 1ሳሙ. 15፥3፤ 1ዜ.መ. 4፥43።

**አማሌቅ፤** የዔሳው የልጅ ልጅ፤ ዘፍ. 36፥12:16።

**አማኑኤል፤** አማኑኤል ማለት እግዚአብሔር ከእኛ ጋር ማለት ነው። ስለ አማኑኤል ትንቢት የተናገረው ኢሳይያስ ነው። እንዲናገርም ምክንያት የሆነው ነገር በአጭሩ እንዲህ ነው፤ የይሁዳ ንጉሥ አካዝ በጦርነት ምክንያት ስለተቸገረ እንዲያበረታታውና እንዲያጽናናው እግዚአብሔር ነቢዩን ላከ። ነቢዩም በእግዚአብሔር እንዲያምን ሊያደፋፍረው ሲል ምልክት እንዲለምን ንጉሡን መከረው። የማያምነው ንጉሥ ግን ይህንን አላደርግም አለ። ኢሳይያስ እንዲህ አለው ፦ ስለዚህ ጌታ ራሱ ምልክት ይሰጣችኋል፤ እነሆ፥ ድንግል ትፀንሳለች፥ ወንድ ልጅም ትወልዳለች፤ ስሙንም አማኑኤል ብላ ትጠራዋለች፤ ኢሳ. 7፥13-14፤ 8፥8። በኢሳ. 7፥13-17 ለአካዝ የተነገረው ትንቢት በእርሱ ዘመን ስለመፈጸሙ ልዩ ልዩ አሳብ አለ፤ ሆኖም የትንቢቱ ዋና ፍጻሜ ከቅድስት ድንግል ማርያም የኢየሱስ ክርስቶስ መወለድ ነው፤ ማቴ፡ 1፥21-23።

ማርያም ሕፃኑን ከወለደች በኋላ እንደ መልአኩ ቃል ኢየሱስ ተብሎ ተሰየመ፤ ትርጕሙም አዳኝ፥ መድኃኒት ማለት ነው። ሕዝቡን ከኃጢአታቸው ያድናቸዋልና። ስለዚህ ከኃጢአቱ የሚያድን በመሆኑ በእርግጥ አማኑኤል የሚለው ስም ይገባዋል። በኢየሱስ መድኅኒትነት እግዚአብሔር ከሰው ጋር አንድነትን ሊያደርግ ችሏል። ነቢዩ ኢሳይያስ በም. 9፥6 በተጨማሪ እንደገለጠልን ይህ ሕፃን ከሴት የተወለደ ቢሆንም እስከ ዘለዓለም የሚኖር አምላክ ነው።

**አማካሪ፤** በቤተ መንግሥት የሚያገለግል ጠቢብ፤ 2ሳሙ. 17፥15። «ምክር» ይመ.

**አሜስያስ፤** 1. ከ796-787 ከክ.በ. የነበረ የይሁዳ ዘጠነኛ ንጉሥ፤ 2ነገ. 14፥1-22፤ 2ዜ.መ. 25። 2. ነቢዩ አሞጽን የተቃወመው የቤቴል ካህን፤ አሞጽ 7፥10-17።

**አሜቴስጢኖስ፤** ወይን ጠጅነት ቀለም ያለው የከበረ ድንጋይ፤ ዘጸ. 39፥12፤ ራእ. 21፥20።

**አሜን፤** «የተረጋገጠና የታመነ» ከሚል የዕብራይስጥ ቃል የወጣ ነው። እንደ አንቀጹ ትርጕሙ «ይሁን»፥ «በእውነት»፥ «መልካም» ማለት ነው፤ ዘዳ. 27፥15። ክርስቶስ እውነት ስለሆነ አሜን ተብሏል፤ ራእ. 3፥14።

**አሜከላ፤** የሚጠመጠም እሾህ፤ ዘፍ. 3፥18፤ ኢሳ. 34፥13።

**አምላክ፤** ቃሉ ገዥ፥ ፈጣሪ፥ ክብርና ኃይል ሥልጣንም ያለው ማለት ነው። ብዙ ጊዜ በመ. ቅ. እግዚአብሔርን ያመለክታል፤ «እግዚአብሔር» ይመ.። ደግሞም የአረማውያንን አማልክት (ዘጸ. 18፥11)፥ ጣዖትን (ዘዳ. 4፥28)፥ ሰዎችን (ዘጸ. 7፥1፤ መዝ. 82፥6)፥ የሰውንም ምኞት ሊያመለክት ይችላል፤ ፊል. 3፥19።

**አምልኮ፤** ለአምላክ ብቻ የሚሰጥ አገልግሎት። አምልኮ ፦ ስግደትን፥ ውዳሴን፥ አክብሮትን፥ መገዛትን፥ ጸሎትን፥ መሥዋዕትን፥ መልካም ሥራን፥ ፍርሃትንና ፍቅርን ያጠቃልላል። በመ.ቅ. አምልኮ በአራት መንገድ ይታያል።

1. ከሙሴ በፊት። የቤተሰብ ራስ የሆነው ሰው በየቦታው መሠዊያን ሠርቶ መሥዋዕት ያቀርብ ነበር፤ ዘፍ. 12፥7:8።

2. ከሙሴ እስከ ክርስቶስ። በሕግና ሥርዓት በመገናኛ ድንኳን ቀጥሎም በቤተ መቅደስ በካህናት በኩል የአምልኮ ሥርዓት ሲፈጸም ኖሯል።

3. የእስራኤል ሕዝብ ከባቢሎን ምርኮ በኋላ እስከ ክርስቶስ። በምኵራብ ውስጥ ጸሎት፥ መዝሙር፥ ንባብና ትምህርት ያደርጉ ነበር።

4. የክርስቲያን አምልኮ። በክርስቲያን አምልኮ ውስጥ ስብከት (ሐ.ሥ. 20፥7)፥ ቃሉን ማንበብ (1ጢሞ. 4፥13)፥ ጸሎት (1ጢሞ. 2፥8)፥ መዝሙር (ኤፌ. 5፥19)፥ ትንቢትና በልሳን መናገር (1ቆሮ. 14፥26-33)፥ ምጽዋት (1ቆሮ. 16፥1:2)፥ ጥምቀትና ቅዱስ ቍርባን ይገኛሉ (1ቆሮ. 11፥18-34)። እውነተኛ አምልኮ እግዚአብሔርን በሁለንተናችን ወድዶ ፈቃዱን ማድረግ (ማር. 12፥30፤ ማቴ. 7፥21)፥ ባልንጀራችንንም እንደ ራሳችን መውደድ ነው፤ ማር. 12፥31፤ ያዕ. 1፥27። እውነተኛ አምልኮ በልብ እንጂ በቦታ አይወሰንም፤ ዮሐ. 4፥20-24።

**አምሳል፤** የሌላ ነገር መገለጫ ምሳሌ። «አርአያ እግዚአብሔር» ይመ.

**አምቡላ፤** የወይን ጠጅ አተላ። የትዕቢት ምሳሌ ነው፤ ኤር. 48፥11።

**አሞራውያን፤ (አሞሬዎን)፤** ከከነዓን የተወለዱ ሕዝቦች፤ ዘፍ. 10፥16። በአብርሃም ዘመን በመስጴጦምያና በሶርያ ይኖሩ ነበር። ካራን መናገሻ ከተማቸው ነበረ። ደግሞ ከዮርዳኖስ ወንዝ በስተምዕራብና ምሥራቅ በተራራማው አገር ይኖሩ

ነበር፤ ኢያሱ 7፥7። ኢያሱ ድል ካደረጋቸው በኋላ ግን ለእስራኤል ገባሮች ሆኑ፤ ኢያሱ 11፥1-14፤ 1ነገ. 9፥20:21። አሞራውያን የሚለው ስም የከነዓንን ሕዝብ ሁሉ ሊያጠቃልል ይችላል፤ ኢያሱ 24፥15።

**አሞናውያን**፤ ከእስራኤልና ከሞዓብ አገር በስተምሥራቅ ይኖሩ የነበሩ ሕዝብ። ካ. 1ሠ። እስራኤልን ብዙ ጊዜ ይቃወሙ ነበር፤ መሳ. 3፥13፤ 10፥6፤ 11፤ 1ሳሙ. 11፤ 2ሳሙ. 10፤ 2ዜ.መ. 20፤ ነህ. 2፥10፤ 13፥23-31። አሞናውያን ለጣዖታቸው ለሞሎክ ልጆችን ያቃጥሉ ነበር፤ ዘሌ. 18፥21። አሞናውያን እስከ ዐሥር ትውልድ ድረስ ወደ እግዚአብሔር ጉባኤ እንዳይገቡ ተከልክለው ነበር፤ ዘዳ. 23፥3-6። «ሞዓብ» ይመ.

**አሞን**፤ ሎጥ ከትንሿ ሴት ልጁ የወለደው የአሞናውያን አባት፤ ዘፍ. 19፥38።

**አሞጽ**፤ 1. የነቢዩ የኢሳይያስ አባት። ነቢዩ አሞጽ አይደለም፤ 2ነገ. 19፥2:20።

2. በዳግማዊ ኢዮርብዓም ዘመነ መንግሥት (783-746 ከክ.በ.) በእስራኤል ዘንድ ያገለገለ ነቢይ። እርሱ እንደ ነቢያት ልጆች አላደገም። በእግዚአብሔር ከመጠራቱ በፊት ላም ጠባቂና የወርካ ፍሬ ለቃሚ ነበረ። አገሩ ቴቁሔ የምትባል ከቤተ ልሔም ዐሥር ኪ.ሜ. ያህል ርቃ የምትገኝ አገር ናት። የተነበየው ግን በይሁዳ ሳይሆን በእስራኤል መንግሥት ውስጥ ነው፤ አሞጽ 1፥1፤ 7፥14። በምቾትና በግድየለሽነት የሚኖሩትን የሰማርያን ሰዎች በጽኑ ገሠጻቸው፤ ግፍንና የጣዖት አምልኮን ትተው ወደ እግዚአብሔር እንዲመለሱ፥ ጽድቅንም እንዲሹ አስጠንቀቃቸው። ስለ እስራኤል መማረክ ተነበየ። የቤቴል ካህን አሜስያስ አሞጽን ተቃውሞ በንጉሥ ፊት ክስ ካቀረበበት በኋላ ወደ አገሩ እንዲመለስ አዘዘው፤ አሞጽ 7፥10-17። የአሞጽ ትንቢት በአብዛኛው የፍርድ ቃል ነው። ፍጻሜ ዘመን ላይ ግን ለእስራኤልም ሆነ ለአሕዛብ የደኅንነትና የሰላም ጊዜ እንደሚመጣ በመጽሐፉ መጨረሻ ተነግሯል። ያዕቆብም ፍጻሜውን አይቶ ጠቅሶታል፤ አሞጽ 9፥11-15፤ ሐ.ሥ. 15፥14-18።

3. ከ642-640 ከክ. በ. የነገሠ ዐሥራ አምስተኛ የይሁዳ ንጉሥ፤ 2ነገ. 21፥18-26፤ 2ዜ.መ. 33፥20-25።

**የአሞጽ ትንቢት**፤ አከፋፈል ፦

1. ፍርድ በእስራኤል ጎረቤት አገሮች፤ 1፥1-2፥5።
2. ፍርድ በእስራኤል፤ 2፥6-16።
3. ፍርድ በእስራኤል ኃጢአት ምክንያት፤ 3፥1-6፥14።
4. ፍርድ በአምስት ዓይነት መንገድ፤ 7፥1-9፥10። በዚህም መካከል የአሜስያስና የአሞጽ ታሪክ፤ 7፥10-17።
5. በፍጻሜ ዘመን ስላለው ተስፋ፤ 9፥11-15።

**አሣሄል**፤ የዳዊት እኅት የጽሩያ ልጅ፥ የኢዮአብና የአቢሳ ወንድም። እንደ ሚዳቋ ፈጣን ሯጭና ኀያል ነበር። አበኔር ገደለው። ኢዮአብም ደሙን ለመበቀል አበኔርን ገደለው፤ 2ሳሙ. 2፥18-32፤ 3፥27፤ 1ዜ.መ. 11፥26።

**አሥራት**፤ «ዐሥራት» ይመ.

**አሥር ከተማ**፤ «ዐሥር ከተማ» ይመ.

**አሦር**፤ የሴም ሁለተኛ ልጅ፤ ዘፍ. 10፥22። አሦር አሦራውያን ለተባሉት ሕዝቦች የመጀመሪያ አባት ሆነ። አገራቸው በላይኛው መስጴጦምያ ነው፤ ነነዌም ዋና ከተማቸው ነበረች። መንግሥትዋ ስትስፋፋ ብዙ ጊዜ ከእስራኤልና ከይሁዳ ጋር ተዋጋች። ሰማርያን ይዛ የእስራኤልን ሕዝብ አፈለሰች። ይሁዳን ብዙ ጊዜ በዘበዘች፤ ንጉሡን ምናሴንም ወደ ባቢሎን ወሰደች፤ ነገር ግን ኢየሩሳሌምንና ሕዝብዋን አላጠፋችም። በሕዝቅያስ ዘመነ መንግሥት አሦራውያን እግዚአብሔርን ተፈታተኑ፤ ስለዚህም የእግዚአብሔር መልአክ ሠራዊታቸውን አጠፋ፤ 2ነገ. 19፥10:35። ዮናስ ወደ ነነዌ ተላከ። አሦራውያን ከኃጢአታቸው ተመለሱ



የአሦርን ወታደሮች የሚያሳይ የድንጋይ ቅርጽ

(የዮናስ ትንቢት ይመ.)። ኢሳይያስ እግዚአብሔር ይሁዳን በአሦር እጅ እንደሚቀጣ አስቀድሞ እንደተነበየው፤ ኢሳ. 10፥5-11፤ 20፥1-6)፤ በመጨረሻም ናሆም እንደተናገረው የባቢሎን መንግሥት በ612 ከክ. ል. ነነዌን ያዘች፤ የአሦርም መንግሥት ወደቀች።

**አረመመ፤** ጸጥ አለ፤ ዝም አለ፤ ኢዮብ 29፥10።

**አረማሞ፤** ከርጥበት የተነሣ የምርቅና የአገዳ እህልን የሚያበላሽ ጥቁርና አረንጓዴ ዓይነት በሽታ፤ ዘዳ. 28፥22፤ 1ነገ. 8፥37።

**አረማዊ፤** ያልተማረና ያልሠለጠነ ሰው፤ ቆላ. 3፥11።

**አረር፤** «እርሳስ» ይመ.

**አረፍት፤** ከግድግዳ ጋር ወይም ከግንብ ጋር ተያይዞ የሚሠራ ማረፊያ፥ መደገፊያ፤ ሕዝ. 41፥6።

**አራማይክ፤** የአራማውያን (የአራም ሰዎች) ቋንቋ ማለት ነው። በመ.ቅ. የሶርያ ቋንቋ ተብሎ ይጠራል፤ 2ነገ. 18፥26። አይሁድ ከምርኮ ከተመለሱ በኋላ ከዕብራይስጥ ይልቅ በአራማይክ ይጠቀሙ ስለነበር፥ ዕዝራ የእግዚአብሔርን ሕግ በዕብራይስጥ ሲያነብብ ሳለ ወደ አራማይክ እንዲተረጉም ያደረገ ይመስላል፤ ነሀ. 8፥8። በክርስቶስም ዘመን አራማይክ በእስራኤል አገር ነዋሪዎች ዘንድ የተለመደ ቋንቋ ነበር።

በብ.ኪ. ዳን. 2፥4-7፥28፤ ዕዝ. 4፥8-6፥18፤ 7፥12-26፤ ኤር. 10፥11 በአራማይክ ተጽፏል። መጽሐፈ ሄኖክ በአራማይክ ተጽፎ ነበር የሚሉም አሉ።

በአ.ኪ. አንዳንዶች የአራማይክ ቃላት ከግሪክ ትርጓሜአቸው ጋር ተጽፈው ይገኛሉ፤ ማር. 5፥41፤ 7፥34፤ 15፥34 ይመ.። ማራናታ የአራማይክ ቃል ነው፤ ትርጉሙም ጌታ ሆይ ና ማለት ነው፤ 1ቆሮ. 16፥22 በግእዝና በጥንቱ የአማርኛ ትርጓሜ። የአራማይክ ፊደልና አጻጻፉ እንደ ዕብራይስጥ ነው።

**አራም፤** የሴም አምስተኛ ልጅ፤ ዘፍ. 10፥22:23። አራም ለተባሉት ሕዝቦች የመጀመሪያ አባት ሆነ፤ ዘኍ. 23፥7። በመ.ቅ. እነዚህ ሕዝቦች አራም በሚለው ስም ሳይሆን ሶርያውያን ተብለው ይጠራሉ። አገራቸው ሶርያ ይባላል፤ ዋና ከተማቸውም ደማስቆ ነው። ከሬንቁ አገር እየተነሡ ወደ ምሥራቅ በመጓዝ በጤግሮስና በኤፍራጥስ ወንዞች መካከል ወደሚገኘው አገር የፈለሱና በሌላም በብዙ አገር የተስፋፉ ሕዝቦች ነበሩ። ቋንቋቸውም በዚህ መጠን ተስፋፍቶ ብዙ ሰዎች የሚጠቀሙበት ሆነ።

ከእስራኤል ጋር ዝምድና ነበራቸው፤ ታሪካቸውም የተሳሰረ ነበር። በነገሥታት ዘመን በእስራኤልና በሶርያ መካከል ብዙ ጊዜ ጦርነቶች ተደርገዋል፤ 2ሳሙ. 8፥5፤ 1ነገ. 21፥20፤ 1ዜ.መ. 19፥10-12። በኋላም የአሦር ንጉሥ በ732 ከክ.ል. ደማስቆን ያዘ። «አራማይክ» ይመ.

**አራራት፤** ከእስራኤልና ከሶርያ በስተሰሜን ያለ ተራራማ አገር፤ 2ነገ. 19፥37፤ ኤር. 51፥27። የኖኅ መርከብ በአራራት ተራራዎች ዐረፈች፤ ዘፍ. 8፥4። ዛሬ አገሩ አርመን የሚባለው ሲሆን የሚገኘውም በቱርክ አገር ውስጥ ነው። ካ. 1ሐ።

**አራት እንስሳት፤** «ኪሩብ» ይመ.

**አራዊት፤** አራዊት ማለት አውሬዎች ማለት ነው። ቃሉ የሚከተሉትን ሊያመለክት ይችላል።

1. ከሰው፥ ከወፍ፥ ከዓሣ በስተቀር በምድር ላይ የሚኖሩ ሕያዋን ፍጡሮች፤ ዘፍ. 1፥24:25።

2. ለሰው የማይገዙ እንስሳት፤ ዘሌ. 26፥22፤ ኢሳ. 13፥21:22። በምሳሌነት ደግሞ ጨካኝ የሆኑ የዓለም መንግሥታትን ያመለክታል፤ ዳን. 7፤ ራእ. 13።

**አራጣ፤** ሰው ገንዘብን ሲያበድር በወር በወር የሚቀበለው ትርፍ፥ ወለድ፤ ዘጸ. 22፥25፤ መዝ. 15፥5። «ብድር» ይመ.

**አርሆ፤** የወንድ ወይም የሴት ዘፋኝ። እንደ አዝማሪ በግብዣ፥ በሰርግና በታላላቅ ሰዎች ቤት እየሄደ የሚዘፍን፤ መክ. 2፥8።

**አርማቴም፤** ከፍታ ማለት ነው። ሳሙኤል የተወለደበትና የኖረበት ከተማ፤ 1ሳሙ. 1፥1፤ 7፥17፤ 25፥1። ዛሬ አቀማመጡ አይታወቅም። ከኢየሩሳሌም በስተሰሜን ስምንት ኪ.ሜ. ርቆ እንደነበረ ይገመታል። አርማቴም፥ አርማትያስ፥ ራማ የአንድ ቦታ ስሞች ይሆኑ ይሆናል። «ራማ» ይመ.

**አርማትያስ፤** ጌታችንን የቀበረው የዮሴፍ አገር፤ ማቴ. 27፥57። ዛሬ ቦታው ተለይቶ አይታወቅም።

**አርማጌዶን፤** «መጊዶ» ይመ.

**አርሞንኤም፤** በሶርያ፥ በሊባኖስና በእስራኤል ድንበር ላይ ያለው ተራራ ከባሕር ጠለል እስከ 2777 ሜትር ከፍ ስለሚል በአቅራቢያው ካሉት ተራራዎች ከፍታ አለው። የአርሞንኤም በረዶ እየሟሟ ወደ ዮርዳኖስና ወደ ገሊላ ባሕር ይፈሳል፤ ዘዳ. 4፥48፤ መዝ. 133፥3። ክርስቶስ ክብሩን የገለጠው በዚህ ተራራ ሳይሆን አልቀረም፤ መዝ. 89፥12፤ ማቴ. 17፥1-8። አርሞንኤም ሢርዮን፥ ሳኔር፥ ኤርሞን ተብሎ ይጠራል፤ ዘዳ. 3፥8:9፤ መ.መ. 4፥8። ካ. 5ሐ።

**አርስጥሮኮስ፤** ከጳውሎስ ጋር የወንጌልን ሥራ የሠራ አይሁዳዊ። የተሰሎንቄ ሰው ነበረ፤ ሐ.ሥ. 19፥29፤ 20፥4፤ 27፥2፤ ቆላ. 4፥10፤ ፊልሞና 24።

**አርነት፥ ነፃነት፤** ከባርነት መውጣት፥ የባርነት ተቃራኒ፤ ዘጸ. 21፥2፤ ዘዳ. 15፥12-15፤ ኤር. 34፥8-16። ኢየሱስ ሰውን ከኃጢአትና ከፍርሃት ባርነት አርነት ሊያወጣ ወደ ዓለም ገባ፤ ኢሳ. 61፥1፤ ሉቃ. 4፥17-19፤ ዮሐ. 8፥32-36፤ ሮም 6፥16-18:22፤ 8፥2:15:21፤ ዕብ. 2፥14:15። ሰው በክርስቶስ ሲያምን ከሕግ ባርነት አርነት



በቁፋሮ ጥንታዊ የቦታ ሁኔታ አጠናን ዘዴ

ይወጣል፣ ገላ. 5፥1፣ 2ቆሮ. 3፥17፣ ሮም 8፥2። አማኙ በመንፈስ ቅዱስ ተሞልቶ በዚህ ነፃነት መራመድ ይገባዋል እንጂ፥ የሥጋን ምኞት እንዲፈጽም አይፈቀድለትም፣ ሮም 6፥19-22፣ ገላ. 5፥13፣ 1ጴጥ. 2፥16፣ 2ጴጥ. 2፥19።

**አርኖን፦** ከምሥራቅ ወደ ጨው ባሕር የሚፈስ ወንዝ። በሙሴ ዘመን የሞዓብና የአሞራውያን አዋሳኝ ነበረ፤ በኋላም የሮቤልና የሞዓብ ዳርቻ ሆነ፤ ዘኍ. 21፥13፣ ዘዳ. 2፥24፣ 3፥12:16። ካ. 2ለ።

**አርአያ እግዚአብሔር፦** ሰው በእግዚአብሔር አምሳልና መልክ ተፈጠረ፤ ዘፍ. 1፥26-28። እግዚአብሔር መንፈስ ነውና አምሳሉ በሰው ላይ የሚታየው በነፍሱ በኩል እንጂ በሥጋው አይደለም። እውነት ነው፤ መ.ቅ. ለእግዚአብሔር ዐይን ጆሮ እጅ ... ወዘተ አለው ይላል። ሆኖም እነዚህ ቃላት በሰው አገላለጥ የእግዚአብሔርን ሥራዎች እንጂ ባሕርዩን አይገልጡም።

የእግዚአብሔር አርአያ በሰው ላይ የሚታየው በተለይ በሚከተሉት ሦስት ነገሮች ነው፤

1. ሰው፥ እግዚአብሔር ለፍጥረቱ ሁሉ ገዥ ስላደረገው፥ የእግዚአብሔርን ንጉሥነት በአስተዳደሩ በመጠኑ ይገልጣል፤ ዘፍ. 1፥28፣ መዝ. 8፥4-9።

2. ሰው አስቦ የሚሠራና የሚኖር መንፈሳዊ ፍጡር ነው፤ ዘፍ. 2፥16:17።

3. ሰው በቅድስናና በጽድቅ የተፈጠረ ነው፤ ዘፍ. 1፥31። ሰው በኃጢአት ስለወደቀ ቅድስናውና ጽድቁ ጠፋ። ምንም ቢሆን የእግዚአብሔር መልክ በመንፈሳዊነት ረገድ በኃጢአተኛም ሳይቀር ይታያልና ማናቸውም ሰው ክብር ይኖረዋል፤ ዘፍ. 9፥6፣ 1ቆሮ. 11፥7፣ ያዕ. 3፥9። ምእመናን ቅድስናና ጽድቅ በሚሆን በእግዚአብሔር ምሳሌ ይታደሳሉ፤ ኤፌ. 4፥23:24፣ ቆላ. 3፥10። «ሰው» ይመ.

«ክርስቶስ የእግዚአብሔር ምሳሌ ነው» ሲል፥ አምላክነቱን ያመለክታል፤ 2ቆሮ. 4፥4፣ ቆላ. 1፥15-16፣ ዕብ. 1፥3።

**አርኤል፦** የእግዚአብሔር ምድጃ ማለት ነው። ለኢየሩሳሌም የተሰጠ ስም፤ ኢሳ. 29፥1-7።

**አርኬኦሎጂ፦** አርኪኦሎጂ ሥነ ጥንት በድሮ ዘመን ስለነበሩ ከተሞች፥ ቤቶች፥ ጽሑፎች፥ ሐውልቶች በጠቅላላው ስለ ድሮ ሰዎች አኗኗር መመራመሪያ ጥበብ ነው። ከሁለት መቶ ዓመታት በፊት ጀምሮ ብዙ ሰዎች በመ.ቅ. በተጠቀሱት አገሮች ይህን ጥናት ተከታትለዋል። የተገኙት የቤትና የሕንጻ መሠረቶች በድንጋይና በሸክላ የተጻፉ ታሪኮችና ሕጎች፥ በድንጋይ የተቀረጹ ሥዕሎች፥ መሣሪያዎችና ዕቃዎች በብዙ ሺህ የሚቈጠሩ ናቸው። እነዚህም ከሁለት ሺህ ዓመታት ከክርስቶስ በፊት ጀምሮ ስለ መ.ቅ. ሰዎች አኗኗር፥ ባህል፥ ቤት፥ ሕግና ታሪክ ብዙ ነገሮችን ይገልጣሉ። የመ.ቅ. ጸሓፊዎችም በጥንቃቄና በማስተዋል እንደጻፉ ያረጋግጣሉ። «ሕንጻ» ይመ.

**አርያም፦** ሰማይ፥ ከሁሉ በላይ ከፍ ያለ፤ ማቴ. 21፥9። የኢየሩሳሌም ሕዝብ «ሆሣዕና በአርያም» እያሉ ኢየሱስን በመቀበላቸው ሰማያዊ አዳኝ ጌታ መሆኑን ገለጡ፤ መዝ. 144፥7:8።

**አርዮስፋጎስ፦** «የአሬስ ኮረብታ» ማለት ነው። (አሬስ በግሪኮች ዘንድ የጦር አምላክ ነበረ)። 1. በአቴና ውስጥ የአንድ ኮረብታ ስም። 2. ከጥንት የመጣና የተከበረ፥ በኮረብታ ላይ የሚሰበሰብ ዋና የአቴና ጉባኤ ነበር። በተለይ በጳውሎስ ጊዜ የፍልስፍናና የግብረ ገብ ነገሮችን ይህ ጉባኤ ያጠና ነበር፤ ሐ.ሥ. 17፥16-34።

**አርጃኖ፦** እንደ አዞ፥ ከአዞ ግን ያነሰ፥ ሰውንም የማይበላ በባሕር ዳርና በባሕር ውስጥ የሚኖር አውሬ፤ ዘሌ. 11፥30።

**አርጤምስ፦** «ኤፌሶን» ይመ.

**አርጤክስስ፦** በአማርኛ መ.ቅ. አልተለዩም እንጂ በዚህ ስም የተጠቀሱ ሁለት ነገሥታት አሉ።

1. በመጽሐፈ አስቴርና በዕዝራ 4፥6 ላይ የተጠቀሰው ንጉሥ። ይኸውም ከ486-465 ከክ.በ. በፋርስ አገር ነግሦ የነበረው ነው። በታሪክ መጻሕፍት ላይ ዘርክሲስ የተባለው ገናና ንጉሥ ነው ተብሎ ይታወቃል። አስጢን የተባለችውን የቀድሞ ሚስቱን ፈትቶ በአርሷ ፈንታ አስቴር የተባለችውን ቆንጆ አይሁዳዊት አገባ፤ አስ. 1፥1-22፤ 2፥17። የዚህ ንጉሥ ስም በዕብራይስጥ ቋንቋ አሕሻዊሮስ ይባላል።

በመጽሐፈ አስቴር ከተጠቀሰው የተለየ በትንቢተ ዳንኤል 9፥1 ላይ የንጉሥ ዳርዮስ አባት በዚህ ስም ተጠቅሶ ይገኛል። አማርኛው ግን ትንሽ የፊደል ልዩነት ያሳያል።

2. በ1ኛው ተራ ቍጥር ላይ የተጠቀሰው የንጉሥ ዘርክሲስ ልጅና አልጋ ወራሽ። ዘመነ መንግሥቱም ከ465-423 ነበረ። የእርሱ ስም በዕብራይስጥ ቋንቋ አርታሕሻስታ ይባላል። በታሪክ መጻሕፍትም ላይ ቀዳማዊ አርታዘርክሲስ ሎንጊማኑስ ተብሎ ይጠራል። በእርሱ ዘመን ዕዝራና ነህምያ እግዚአብሔርን በኢየሩሳሌም ያገለግሉ ነበር፤ ዕዝ. 4፥7፤ 7፥1-11፤ 8፥1፤ ነህ. 2፥1፤ 5፥14።

**አሮን፤** የሙሴና የማርያም ወንድም፤ ዘኍ. 26፥59፤ ዘጸ. 6፥20። ስሙ ለመጀመሪያ ጊዜ የተጠቀሰው እግዚአብሔር ራሱን ለሙሴ በገለጠበት ጊዜ ነው፤ በዚያን ጊዜ ሙሴ የእስራኤል መሪ እንዲሆን ተመርጦ ነበር፤ ነገር ግን ሙሴ «አፈ ኰልታፋ ምላሴም ጸያፍ የሆነ ሰው ነኝ» በማለት ለመታዘዝ አለመውደዱን በገለጠ ጊዜ እግዚአብሔር «ወንድምህ አሮን አፍ ይሆንልሃል» ብሎ መለሰለት፤ ዘጸ. 4፥14-16። የይሁዳ ነገድ አለቃ እኅት የሆነችውን ኤልሳቤጥ የተባለችውን ሴት አግብቶ ከእርስዋ ናዳብ፥ አብዩድ፥ አልዓዛርና ኢታምር የተባሉ አራት ልጆችን ወለደ፤ ዘጸ. 6፥23። ሙሴ ወደ ፈርዖን በቀረበ ቍጥር፥ ከዚያም በኋላ የአርባው ዓመት የምድረ በዳ ጕዞ እስኪያልፍ ድረስ ሙሴ በሚሠራው ሥራ ሁሉ አሮን የቅርብ ረዳቱ ነበረ። የእስራኤል ልጆች ከአማሌቅ ጋር በተዋጉ ጊዜ አሮንና ሖር የሙሴን እጆች ይደግፉ ነበር፤ ዘጸ. 17፥9-12። ሆኖም የእስራኤል ልጆች ይሰግዱለት ዘንድ የወርቅ ጥጃን በመሥራቱ እግዚአብሔርን ሳያስቈጣው አልቀረም፤ ዘጸ. 32። አሮን ለተለየ አገልግሎት በእግዚአብሔር የተመረጠ ለመሆኑ በበትሩ ማቈጥቈጥ ታወቀለት፤ ዘኍ. 17። ቢሆንም መሪባ በተባለው ስፍራ ከሙሴ ጋር ሆኖ የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ባለማክበሩ ኃጢአት ሠራ፤ ዘኍ. 20፥12። ሊቀ ካህናት እንዲሆን በመመረጡ ከሌዊ ወገን ካህናት የመጀመሪያው ሆነ፤ ዘጸ. 28፥1። ልጆቹም ካህናት እንዲሆኑ ተቀደሱ፤ ዘሌ. 8፥12-13:30። በ123ኛ ዓመቱ ሲሞት ሊቀ ካህናትነቱ ለልጁ ለአልዓዛር ተሰጠ፤ ዘኍ. 20፥22-29፤ 33፥38፤ ዘዳ. 10፥6። በዕብ. 5፥4-5 አሮን የክርስቶስ ምሳሌ ሆኖ ተቈጥሯል።

**አሰረ፤** በገመድ፥ በግዞት፥ በሕግ፥ በነፍስ፥ በመንፈስ ወሰነ፤ ዘፍ. 22፥9፤ 44፥30፤ ኢሳ. 61፥1፤ ሐ.ሥ. 20፥22፤ ሮም 7፥2፤ ራእ. 20፥2። «ማሰርና መፍታት» ይመ.

**አሰር፤** ለእንስሳት የሚሰጥ መናኛ እህል። ነገር ግን በሉቃ. 15፥16 አሰር የተባለው ለከብት እንዲሁም ለድሆች የሚሰጥ የአንድ እንጨት ፍሬ ነው።

**አሳ፤** በይሁዳ ከ911-870 ከክ.ል. የነገሠ ሦስተኛ ንጉሥ፤ 1ነገ. 15፥9-24፤ 2ዜ.መ. 14-16። ዘመነ መንግሥቱን የጀመረው አምልኮ ባዕድን ለማስወገድና ሕዝቡን ወደ ፈሪሀ እግዚአብሔር ለመመለስ ብርቱ ጥረት በማድረግ ነው፤ 2ዜ.መ. 14፥3-5፤ 15፥1-17። ምንም እንኳ የቀድሞ ወገኖቹ ጣዖት አምላኪዎች ቢሆኑም እርሱ እግዚአብሔርን የሚፈራ ንጉሥ ነበረ። በነገሠ በመጀመሪያው ዐሥር ዓመት ውስጥ በመንግሥቱ ሰላም ነበረ። ከዚያ በኋላ ግን ዝራ ከተባለው ኢትዮጵያዊ ጋር፥ እንዲሁም ከእስራኤል መንግሥት ጋር ጦርነት ገጠመ፤ 2ዜ.መ. 14፥9-15፤ 1ነገ. 15። በሕይወቱ መጨረሻ ላይ እግዚአብሔርን በማመን ረገድ እየደከመ ሄደ። ጽኑ በሆነ የእግር በሽታ ታምሞ ሞተ፤ 2ዜ.መ. 16፥12-14።

**አሳፍ፤** በዳዊትና በሰሎሞን ጊዜ የነበረ የመዘምራን አለቃ፤ 1ዜ.መ. 16። በቤተ መቅደስ የመዘምራን መሪ ከመሆኑም በላይ የመዝሙር ደራሲ ነበረ። ከመዝሙራት ውስጥ የአሳፍ መዝሙር የሚል ርእስ ያላቸው መዝሙራት ዐሥራ ሁለት ናቸው። እነርሱም መዝሙር 50፥ እንዲሁም ከመዝሙር 73 እስከ 83 ያሉት ናቸው፤ 2ዜ.መ. 29፥30። ከአሳፍ ቤተሰብ የተገኙት ሰዎች ለረጅም ጊዜ በዘማሪነት የሚያገለግሉ ሆነዋል። ከባቢሎን ምርኮ በተመለሱት እስራኤላውያን መካከል የአሳፍ ልጆች እየተባሉ የሚጠሩ አንድ መቶ ሃያ ስምንት መዘምራን ነበሩ፤ ዕዝ. 2፥41።

**አሴር፤** ትርጉሙ «ደስተኛ» ማለት ነው። የልያ ገረድ ዘለፋ የወለደችው ለያዕቆብ ስምንተኛ ልጅ፤ ዘፍ. 30፥12:13። ከእስራኤል ነገዶች የአንዱ አባት ሆነ፤ በስሙም ነገደ አሴር ተብሎ ተጠራ፤ ያዕቆብ ሲባርከው ዘሩ በረከትን እንደሚያገኝ ተናገረ፤ ዘፍ. 46፥17፤ 49፥20፤ ዘኍ. 26፥44-47። ሙሴም ሲባርከው ተወዳጅና ኃይለኛ እንደሆነ ተናገረለት፤ ዘዳ. 33፥24:25። በከነዓን የተቀበለው የርስት ድርሻ በታላቁ ባሕር፥ በንፍታሌምና በዛብሎን መካከል ነበር። ኢ. 3. ሀ። የአሴር ሰዎች ባርቅን አልረዱም፤ ጌዴዎንን ግን ተከተሉ፤ መሳ. 5፥17፤ 6፥35፤ 7፥23። የሕዝቅያስን ጥሪ ተቀብለው በኢየሩሳሌም ፋሲካን አከበሩ፤ 2ዜ.መ. 30፥11። ነቢይት ሐና ከአሴር ወገን ነበረች፤ ሉቃ. 2፥36። «ነገድ» ይመ.

**አስማተኛ፤** ምሥጢራዊ ስምን እየጠራ መድኃኒት የሚያደርግ ሰው፤ ዘጸ. 7፥11፤ ዘዳ. 18፥10፤ 2ነገ. 17፥17፤ ሐ.ሥ. 19፥19፤ ራእ. 22፥15። «ጥንቆላ» ይመ.

**አስራዶን፤** የአሦር መንግሥት ንጉሥ። የሰናክሬም ልጅ ነው። ወንድሞቹ አባቱን ከገደሉት በኋላ የአባቱን አልጋ ወረሰ። ዘመነ መንግሥቱ ከ681-669 ከክ.ል. ነበረ፤ 2ነገ. 19፥37፤ ኢሳ. 37፥38። በውጭ አገሮች ላይ ልዩ ልዩ ዘመቻዎችን ያደረገ ንጉሥ ነው። በአንዱ ዘመቻ የግብጽን አገር አሸነፈ። ይሁዳንም ወርር ንጉሡ ምናሴን በሰንሰለት አስሮ ወደ ባቢሎን ወሰደው፤ 2ዜ.መ. 33፥11። ከእሕዛብ ወገን የሆኑትን ሰዎች አስመጥቶ በሰማርያ

እንዲቀመጡ አደረገ፤ ዕዝ. 4፥2።

**አስቀሎና፤** ከጋዛ ወደ ሰሜን 20 ኪ.ሜ. የሚርቅ የባሕሩ ዳር ከተማ። ከአምስቱ የፍልስጥኤማውያን ከተሞች አንዱ ነበረ፤ ኢያሱ 13፥3። ሶምሶን ከአስቀሎና 30 ሰው ገደለ፤ መሳ. 14፥19። ንጉሥ ሄሮድስ በዚህ ቦታ ተወለደ። ነቢዩ ሶፎንያስ ከተማው ይፈርሳል፤ በኋላ ግን በአይሁድ እንደገና ይሠራል አለ፤ ሶፎ. 2፥4:7። ዛሬ እንዲሁ ተሠርቷል። በ1ሳሙ. 5፥6-12 በአማርኛ አስቀሎና ይላል፣ ሆኖም በዕብራይስጥ አቃሮን ይላል። ከ. 3ቀ።

**አስቀድሞ መወሰን፤** ዓለም ሳይፈጠር እግዚአብሔር በክርስቶስ የመረጣቸውን ወዳዘጋጀላቸው ደኅንነትና በረከት ሁሉ ያደረሰበት ዕቅድ፤ ሮም 8፥29-30፤ ኤፌ. 1፥5:11። «እግዚአብሔር5» ይመ.

**አስተማረ፤** ልጆችን ማስተማር የወላጆች ኀላፊነት መሆኑን የሙሴ ሕግ ይገልጣል፤ ዘጸ. 12፥25-27። በብ.ኪ. ዘመን ካህናት ሕዝቡን ያስተምሩ ነበር፤ ዘዳ. 20፥2-9። ነቢያትም የእግዚአብሔርን ቃል ሲገልጡ የነቢያት ልጆች የተባሉትን አስከተሉ፤ 2ነገ. 2፥3። በአ.ኪ. ዘመን ጸሐፊዎች የሕግ መምህራን ሆነው ያስተምሩ ነበር፤ ሉቃ. 2፥46። በየምኵራቡም የምኵራቡ አገልጋይ ልጆችን ያስተምር ነበር።

በቤ.ክ፡ በመጀመሪያ ሐዋርያት አስተማሩ (ሐ.ሥ. 6፥2-4)፤ ቀጥሎም ማንም ሰው የማስተማር ችሎታ ካለው ወንጌልን ማስተማር እንደሚገባው ተጽፏል፤ ሮም 12፥7። የማስተማር ስጦታ ያላቸው ሰዎች በቤ.ክ. ይሾማሉ፤ «ሽማግሌዎች»ና «ኤጲስ ቆጶሳት» ተብለውም ይጠራሉ፤ 1ቆሮ. 12፥28፤ ኤፌ. 4፥11፤ 1ጢሞ. 3፥2፤ 5፥17፤ ቲቶ 1፥5-9። ለአስተማሪዎች ሁሉ ኢየሱስ ታላቅ ምሳሌ ሰጠ፤ ዮሐ. 3፥2፤ ማቴ. 7፥29፤ 13፥34:35። «የቤተ ክርስቲያን አስተዳደር» ይመ.

**አስታ፤** በደጋ የሚበቅል፣ ቅጠሉ የጥድን የሚመስል፣ ችፍግ ያለ ቍጥቋጦ፤ ኢሳ. 41፥19:20፤ 60፥13። «ኤርሞን» ይመ.

**አስታሮት፤** በከነዓናውያን መካከል የተከበረች የባሕር አምላክ ጣዖት። አምልኮትዋ ከበኣል አምልኮት ጋር የተያያዘ ነበር። በበኣል መሠዊያዎች አጠገብ «የማምለኪያ ዐፀዶች» የሚባሉ ምስሎች ለአስታሮት ይተከሉ ነበር። በአምልኮትዋ የዝሙት ሥራ ይፈጸም ነበር፤ መሳ. 3፥7፤ 1ነገ. 16፥29-34። በስምዋም የተሰየመ ከተማ ነበረ፤ ኢያሱ 12፥4። «ዐጸድ» ይመ.

**አስቴር፤** በፋርስ ቋንቋ «አስቴር» ማለት «ኮከብ» ማለት እንደሆነ ይነገራል። አንዳንዶች ግን «አስቴር»፣ «ኢሽታር» ከሚባል ከአንዲት የባቢሎን ጣዖት ስም የተገኘ ነው ይላሉ። የዕብራይስጥ ስምዋ ሀደሳ ነው። የፋርስ ንጉሥ አርጤክስስ ባገባት ጊዜ ንግሥት የሆነች አንዲት አይሁዳዊት ምርኮኛ ነበረች። ንጉሡ ሚስቱን፣ ንግሥት አስጢንን ከሰደዳት በኋላ፣ አስቴርን ያሳደጋት የአጎትዋ ልጅ መርዶክዮስ ንግሥት



«የሰማይ ንግሥት» የተባለች የፍቅርና የጦርነት እንስት አምላክ አስታሮት በአንበሳ ላይ ቆማ አማኞዋን ስትቀበል በ650 ዓመት ገደማ ከክ.ል. ከተቀረጸ የአሦር ማኅተም የተሣለ

እንድትሆን አሰበ፤ አስ. 2፥5-11። ንጉሡም መርጦ አገባትና አነገሣት፤ አስ. 2፥17። የአይሁድ ጠላት የነበረው ሐማ አይሁድን ሁሉ ለማጥፋት ባሰበ ጊዜ አስቴር ንጉሡን በመለመን አዳነቻቸው፤ አስ. 3-8። በተለይ 4፥10-5፥2። መርዶክዮስና አስቴርም የሐማን ክፉ አሳብ በማስለወጥ አይሁድ በጠላቶቻቸው ላይ እንዲነሡ አደረጉ። ፉሪም የተባለው የመታሰቢያ በዓል በየዓመቱ እንዲከበር አዘዙ፤ አስ. 8-10።

**መጽሐፈ አስቴር፤** መጽሐፉ በፋርስ መንግሥት ጊዜ በምርኮኝነት ይኖሩ በነበሩ እስራኤላውያን ላይ የደረሰውን ስደትና ከሞት አደጋ መዳናቸውንም ይተርካል። መጽሐፉ አርጤክስስ ከሞተበት ከ465 ከክ.ል. እንደተጻፈ ይገመታል። መጽሐፉን የጻፈው ማን እንደሆነ አይታወቅም፤ ሆኖም ጸሐፊው የፋርስን ቤተ መንግሥት ሥርዓትና ደምብ ያወቀ አይሁዳዊ ይመስላል። በየዓመቱ በፉሪም ዓመት በዓል አይሁድ ስለሚያነቡት መጽሐፉ የታወቀ ሆነ።

መጽሐፉ የተጻፈው በዕብራይስጥ ነው። በመጽሐፉ ውስጥ የእግዚአብሔር ስም አልተጠቀሰም። ይህ የሆነው ምናልባት በምርኮ ዘመን በስደት ጊዜ ስለተጻፈ ይሆናል። ሆኖም ስሙ ባይጠቀስም እንኳ እግዚአብሔር ከሁሉ በላይ ያለ ኃያል ንጉሥ በመሆኑ በአስቴር አማካይነት ለሕዝቡ ያለውን በጎ ፈቃድ እንደፈጸመ በግልጽ ያሳያል፤ አስ. 4፥14።

አከፋፈል ፦

1. 1፥1-2፥20፤ አስቴር የፋርስ ንግሥት ሆነች።
2. 2፥21-3፥15፤ ሐማ አይሁድን ለማጥፋት አሰበ።
3. 4፥1-7፥10፤ የአስቴር ልመናና የሐማ ውድቀት።
4. 8፥1-10፥3፤ የፉሪም ቀናት።

**አሶር፤** (ሐጾር)፣ ከገሊላ ባሕር በሰሜን በኩል 15 ኪ.ሜ. ርቆ የተቆረቆረ የከነዓናውያን ከተማ። ይህ ከተማ ከ«አሦር መንግሥት» ጋር ግንኙነት የለውም። አርባ ሺህ ሰዎች የሚኖሩበት ከተማ ነበር። ኢያሱ አቃጠለው፤ ኢያሱ 11፥1-13። ዲቦራ የአሶርን ጦር ሠራዊት አሸነፈች፤ መሳ. 4። ሰሎሞን አሶርን አሳደሰ፤ ቅጥሩን እስከ 20 ሜትር በሚደርስ ቁመት ሠራ፤ 1ነገ. 9፥15። የአሦር ንጉሥ ቴልጌልቴልፌልሶር በ732 ከክ.በ. ከተማውን አፈረሰ፤ 2ነገ. 15፥29። ዛሬ አሶር የነበረበት ስፍራ ባድማ ሆኗል። አሶር (ሐጾር) ማለት የታጠረ ማለት ነው። ሌሎችም ቦታዎች አሶር (ሐጾር) በሚል ስም ተጠርተዋል። ካ. 3ለ።

**አሽበሸበ፤** 1. አረገደ፤ ተወዛወዘ። በማጎሌት፥ በዘፈንና በልቅሶ ጊዜ የሚታይ ውዝዋዜ ነው፤ ሕዝ. 6፥11። 2. ተጨማደደ፤ ተኮማተረ፤ ዳን. 10፥8።

**አሸነፈ፤** ድል ነሣ፤ ሉቃ. 11፥22። ክርስቶስ ዓለምን አሸነፈ፤ ዮሐ. 16፥33። ተከታዮቹም ክፉውን ነገር በመልካም ቢያሸንፉም፥ በሥጋቸው ሊገደሉ ይችላሉ፤ ሮም 12፥21፤ ራእ. 11፥7፤ 13፥7። አማኞች በክርስቶስ ሆነው ሰይጣንን፥ ሌሎች ተቃዋሚዎቻቸውንና ዓለምን ያሸንፉሉ፤ 1ዮሐ. 2፥13:14፤ 4፥4፤ 5፥4-5። «ድል ነሣ» ይመ.

**አሸንክታብ፤** አንዳንድ አይሁድ፥ በተለይም ፈሪሳውያን ከሙሴ ሕግ ልዩ ልዩ ጥቅሶችን ከጻፉ በኋላ እንደ ክታብ አድርገው፥ ወደ ምኩራብ ሲሄዱ



በግንባር ላይ የሚታሰር አሸንክታብ

በእጃቸውና በግምባራቸው ያስሩ ነበር፤ ማቴ. 23፥5። ይህንም በማድረጋቸው በዘጸ. 13፥9:16 እና በዘዳ. 6፥4-8 የተጻፈውን የሚፈጽሙ መስሎ ታያቸው። ሴቶች በእግራቸውና በአንገታቸው የሚያደርጉት ጌጥ አሸንክታብ ይባላል፤ ኢሳ. 3፥20።

**አሸዋ፤** በባሕር ዳርና በምድረ በዳ የሚገኝ ዐፈር። በምሳሌነት ብዛትን (ዘፍ. 22፥17)፥ ክብደትን (ኢዮብ 6፥3)፥ የመሠረትን ድክመት ያሳያል፤ ማቴ. 7፥26።

**አሹራውያን፤** ኢያቡስቴን የተከተሉ ሰዎች፤ 2ሳሙ. 2፥9። እነማን እንደነበሩ አልታወቀም።

**አሽክላ፤** ከብረት ወይም ከገመድ በመረብ ዓይነት የሚሠራ ወፍ ወይም አውሬ የሚይዝ ወጥመድ፤ ኢዮብ 18፥9፤ ኢሳ. 8፥14፤ አብ. 7፤ ሮም 11፥9።

**አቂላና ጵርስቅላ፤** በክርስቶስ ያመኑ አይሁዳውያን ባልና ሚስት ድንኳን ሰፊዎች። ከጳውሎስ ጋር በቆሮንቶስ ከተማ ይኖሩ ነበር። በኋላም ጳውሎስ በኤፌሶን ተዋቸው፤ በዚያም አጵሎስ የሚባለውን አዋቂ ሰው መከረው፥ ከበፊቱ ይልቅ የእግዚአብሔርን መንገድ ገለጡለት። ክርስቲያኖች በቤታቸው ይሰበሰቡ ነበር፤ ጳውሎስን ከሞት አዳኑት፤ ሐ.ሥ. 18፥2:3:18:19:24-28፤ ሮም. 16፥3-5፤ 1ቆሮ. 16፥19፤ 2ጢሞ. 4፥19።

**አቃሮን፤** ከፍልስጥኤማውያን ከተሞች ሁሉ ለሰሜንና ለይሁዳ ቅርብ የሆነ ከተማ። ንጉሥ አካዝያስ የአቃሮንን አምላክ ለመጠየቅ መልእክተኛ ላከ፤ 2ነገ. 1፥2:3። ካ. 5ሰ። «አስቀሎና» ይመ.

**አቆስጣ፤** መልኩ እንደ ቀበሮ፥ እግሩ አጭር የሆነ፥ በውኃ የሚዋኝ፥ እንደ ድመት ያለ አውሬ። ምግቡ ዓሣ ነው፤ ዘጸ. 25፥5፤ ሕዝ. 16፥10።

**አበራየ፤** እህሉን በአውድማ ላይ በከብት አሄደ፤ አስረገጠ፤ ዘዳ. 25፥4። አበራየ ማለት ወንጌልን የማስተማር ሥራ ይገልጣል፤ 1ቆሮ. 9፥9:10፤ 1ጢሞ. 5፥18።

**አበሳ፤** ከፍ ያለ አሳዛኝ በደል፤ ኢዮብ 31፥11።

**አበኔር፤** የሳኦል የአጐቱ ልጅና የሳኦል የሠራዊት አለቃ፤ 1ሳሙ. 14፥50። ሳኦል ከሞተ በኋላ በሁለቱ ነገድ በይሁዳ ሳይሆን በዐሥሩ ነገድ በእስራኤል ላይ የሳኦልን ልጅ ኢያቡስቴን አነገሠ፤ 2ሳሙ. 2፥8:9። በጦርነት ላይ የኢዮአብን ወንድም አሣሄልን «ፈቀቅ በል» በማለት ሲለምነው፥ እንቢ በማለቱ ተገድዶ ገደለው፤ 2ሳሙ. 2፥18-23። ኢያቡስቴ በነገሩ ባልተደሰተበት ጊዜ መንግሥቱን ወደ ዳዊት ለማዞር ሲሞክር ሳለ ኢዮአብ በተንኰል ገደለው፤ 2ሳሙ. 3፥6-30።

**አበዛ፤** እንጀራ ጋጋሪ ወይም የእንጀራ ጋጋሪዎች አለቃ አበዛ ይባላል፤ ዘፍ. 40፥1-5:16:22፤ ሆሴዕ 7፥6።

**አቡነ ዘበሰማያት፤** ጌታችን ተከታዮቹ እንዲጸልዩ ያስተማረው ጸሎት። ጌታችን ስለ ጸሎት ሲያስተምር አቡነ ዘበሰማያትን ሁለት ጊዜ አስተማረ፤ ማቴ. 6፥5-15፤ ሉቃ. 11፥1-4። ይህ ጸሎት ተከታዮቹ የሚጠቀሙበት ጸሎት ነው። ደግሞም ለጸሎታቸው ሁሉ መሪና ምሳሌ ነው። ምንም እንኳ አጭር ቢሆን፥ የጸሎትን አሳብ ሁሉ ያጠቃልላል። በውስጡ ስድስት ነገሮችን ይዟል፤ ከእነዚህም ሦስቱ ስለ እግዚአብሔር ክብር፥ ሦስቱ ስለ ሰዎች ጥቅም ይናገራሉ። 1. ስለ እግዚአብሔር ክብር ፦ ስሙን መቀደስ፥ መንግሥቱን መሻት፥ ፈቃዱን መጠየቅ። 2. ስለ ሰዎች ጥቅም ፦ የዕለት እንጀራን፥ ይቅርታን ማግኘት፥ ከክፉ ሁሉ መዳን ናቸው። ጸሎቱም በውዳሴ ይደመደማል።

**አቢሳ፤** የዳዊት እኅት የጽሩያ ልጅ የኢዮአብና የአሣሄል ወንድም፤ 2ሳሙ. 2፥18። በፈቃደኝነት የዳዊት ጦር አለቃ ሆነ፤ 1ሳሙ. 26፥6-9፤ 2ሳሙ. 3፥30፤ 16፥9፤ 18፥2፤ 23፥18።

**አቢብ፤** «ወር» ይመ.

**አቢግያ፤** 1. ባልዋ ናባል ዳዊትን ከመፍራት የተነሣ ከሞተ በኋላ አቢግያ የዳዊት ሦስተኛ ሚስት በመሆን ሁለተኛውን ልጅ ወለደችለት፤ 1ሳሙ. 25፥2-43፤ 27፥3፤ 2ሳሙ. 2፥2፤ 3፥3። 2. የዳዊትና የጽሩያ እኅት፥ የአሜሳይ እናት፤ 2ሳሙ. 17፥25።

**አባሪም፤** ሙሴ ወደ ወንኑ የተከማቸበት ተራራ፤ ዘኊ. 27፥12-13። ይህ ተራራ ናባው (ነቦ) ተብሎ ተጠርቷል። «ናባው» ይመ.

**አባት፤** የወለደ፥ በሥርዓት ኮትኩቶ ያሳደገ፥ በሥጋና በመንፈስ የአባትነትን ሥራ የፈጸመ ሁሉ አባት ይባላል። ቃሉ የሚከተሉትን አሳቦች ሊያመለክት ይችላል። 1. በሥጋ ወላጅ፥ 2. በትውልድ ሐረግ የሚገኝ የቅርብ ወይም የሩቅ ወላጅ (ዘፍ. 17፥4፤ ዮሐ. 4፥12)፥ 3. በሃይማኖት የመጀመሪያ ተጠሪ (ዮሐ. 8፥44፤ ሮም 4፥11)፥ 4. ሰውን ወደ እምነት ያደረሰ (1ቆሮ. 4፥15)፥ 5. የአንድ ዐይነት ኑሮ መሥራች (ዘፍ. 4፥20)፥ 6. አማካሪ (መሳ. 17፥10)፥ 7. የአንድ ነገር ምንጭና ምክንያት (ኢዮብ 38፥28፤ ኢሳ. 9፥6፤ ዮሐ. 8፥44)። እግዚአብሔር ፈጣሪ በመሆኑ የልዩ ልዩ ፍጥረታት አባት ይባላል፤ ያዕ. 1፥17፤ ሚል. 2፥10። ምእመናን ከእርሱ በመንፈስ ስለተወለዱ «አባ አባት» ብለው ይጠሩታል፤ ማቴ. 6፥9፤ ዮሐ. 1፥12:13፤ ገላ. 4፥6። «ወላጆች» ይመ.

**የአባቶች አለቆች፤** በመ.ቅ. ውስጥ የእስራኤልን ሕዝብ ታሪክ ጀማሪዎች ናቸው። አብርሃም (ዕብ. 7፥4)፥ የያዕቆብ ልጆች (ሐ.ሥ. 7፥8:9)፥ ዳዊትም (ሐ.ሥ. 2፥29) የአባቶች አለቆች ተብለዋል።

**አቤል፤** የአዳምና የሔዋን ሁለተኛ ልጅ። አቤልና ወንድሙ ቃየል ለእግዚአብሔር መሥዋዕትን ባቀረቡ ጊዜ እግዚአብሔር የአቤልን መሥዋዕት ወደደ። የአቤልን መሥዋዕት በእግዚአብሔር ፊት ተወዳጅ ያደረገው እምነቱ ነው። አቤል በወንድሙ በቃየል እጅ ተገደለ። ጻድቅም እንደሆነ ተመሰከረለት፤ ዘፍ. 4፥2-8፤ ማቴ. 23፥35፤ ዕብ. 11፥4፤ 12፥24። አቤል የሞተው በእምነቱ ምክንያት ነው፤ ስለዚህ ከሰማዕታት ሁሉ የመጀመሪያው ነው ለማለት ይቻላል።

**አቤል ምጽራይም፤** የግብጻውያን ልቅሶ፤ ዘፍ. 50፥10-11።

**አቤል ቤትመዓካ፤** ከእስራኤል በስተሰሜን በሊባኖስ ድንበር ያለ ከተማ። ኢዮአብ የዳዊትን ጠላት ሳቤዔን ለመግደል ይህን ከተማ ከብቦ ነበር፤ 2ሳሙ. 20፥14-22። በኋላም የአሦር ንጉሥ ሕዝቡን አፈለሰ፤ 2ነገ. 15፥29።

**አቤሜሌክ፤ ወይም ኤቤድሜሌክ፤**

ኤቤድሜሌክ ማለት የንጉሥ አገልጋይ ማለት ነው። ነቢዩን ኤርምያስን ከሞት ያዳነ ኢትዮጵያዊ ጃንደረባ። የነቢዩ ጠላቶች የእግዚአብሔርን ቃል ለመስማት ባለመፈለጋቸው ምክንያት በንጉሥ ሴዴቅያስ ፈቃድ ኤርምያስን ወደ ጕድጓድ ጣሉት፤ ኤር. 38፥6። የንጉሡ ጃንደረባ አቤሜሌክ ግን ለነቢዩ አዝኖ ከንጉሥ አስፈቅዶ በገመድ ከጕድጓድ አወጣው፤ ኤር. 38፥7-13። ጃንደረባው ለእግዚአብሔር አገልጋይ የቸርነትን ሥራ በመሥራቱ፥ በእግዚአብሔርም በመታመኑ፥ በአገሪቱ ላይ ከሚደርስባት መቅሠፍት እንደሚድን እግዚአብሔር ራሱ በነቢዩ አፍ ተስፋ ሰጠው፤ ኤር. 39፥15-18። በመ.ቅ. ውስጥ ሌሎች ሰዎች በዚህ ስም ተጠቅሰው ይገኛሉ።

1. በአብርሃም ዘመን የነበረ የጌራራ ንጉሥ፤ ዘፍ. 21፥22-34። 2. በይስሐቅ ዘመን የነበረ ሌላ የጌራራ ንጉሥ፤ ዘፍ. 26። 3. ለ ወንድሞቹን በድንጋይ ላይ የገደለው የጌዴዎን ልጅ፤ መሳ. 8፥31፤ 9። 4. ካህን፤ 1ዜ.መ. 18፥16።

**አቤሮን፤** ዘኊ. 16፥1። «ዳታን» ይመ.

**አቤሴሎም፤** ትርጕሙ «አባቴ ሰላም ነው» ማለት ነው። የንጉሥ ዳዊት ሦስተኛ ልጅ። ወንድሙ አምኖን ትዕማር የተባለችውን እኅቱን ስለደፈራት አቤሴሎም ቂናድዶ ገደለው። ከዚያም ወደ ውጭ አገር ሸሸ፤ 2ሳሙ. 13፥22-39። አባቱ ንጉሥ ዳዊት እንዲመለስ ፈቀደለት። ግን እስከ ሁለት ዓመት ድረስ ፊት እየነሣው ቆየ። አቤሴሎም ራሱን ለማንገሥ ቢል በይሁዳ ጭፍራ ደጋፊዎችን ፈልጎ በአባቱ ላይ ዐመፀ። የዳዊት ደጋፊዎች ግን አቤሴሎምን ድርነት ገጠሙትና ኢዮአብ በተባለው የዳዊት ጦር አዛዥ እጅ ተወግቶ ሞተ፤ 2ሳሙ. 18፥6-17። በአቤሴሎም መሞት ንጉሥ ዳዊት ምርር ብሎ አለቀሰ፤ 2ሳሙ. 18፥33።

**አብ፤** አባት ማለት ነው። ይህ ስም ከዘለዓለም ከወልድና ከመንፈስ ቅዱስ ጋር ለነበረው ለእግዚአብሔር አብ የሀላዌ (የአንዋንዋር) ስሙ ነው፤ ማቴ. 28፥19፤ 1ጴጥ. 1፥1:2። ኢየሱስ ስለ ሰማያዊ

አባት ሲናገር ብዙ ጊዜ አብ ብሎ ጠራው። ኢየሱስ እኔና አብ አንድ ነን አለ፤ ዮሐ. 10፥30። ኢየሱስ በትምህርቱ ውስጥ ብዙ ጊዜ በአብና በእርሱ መካከል ይለያል። ስለዚህ ይህ አንድነት የመለኮት እንጂ የአካል አይደለም፤ ዮሐ. 5፥19፤ 14፥28። ኢየሱስ የአብን ፈቃድ አደረገ፤ ሰዎችም በእርሱ ብቻ ወደ አብ እንደሚደርሱ ተናገረ፤ ዮሐ. 6፥46፤ 14፥6-11። ወልድ ሰው ሆኖ በምድር ሳለ በፈቃዱ ለአብ በመታዘዙ «ከእኔ አብ ይበልጣል» ብሎ ተናገረ። ሥራውንም ጨርሶ ወደ አብ ተመለሰ፤ ዮሐ. 14፥28:31። የአብና የወልድ ክብር አንድ ነውና «አብ» ስንል ከወልድ ይቀድማል ማለት ሳይሆን የህላዌ ስም መሆኑን እናያለን፤ ዮሐ. 5፥17-23። «እግዚአብሔር»፥ «ኢየሱስ»፥ «መንፈስ ቅዱስ» ይመ.

**አብርሃም**፤ የመጀመሪያ ስሙ አብራም ነበረ፤ አብራም ማለት ታላቅ አባት ማለት ነው። በኋላ ግን እግዚአብሔር ለብዙ አሕዛብ አባት ትሆናለህ በማለት አብርሃም ብሎ ስሙን ለወጠ፤ ዘፍ. 17፥1-5። የታራ ታላቅ ልጅ ነው። እግዚአብሔር ብዙ ጊዜ አነጋገረው።

1. ለእስራኤል ሕዝብ አባቱ የመጀመሪያው ይሆን ዘንድ ከትውልድ አገሩ ከከለዳውያን ዑር እንዲወጣ በጠራው ጊዜ አነጋገረው፤ ዘፍ. 12፥1-6፤ ሐ.ሥ. 7፥2-3።

2. ከአባቱ ከታራና ከአጐቱ ልጅ ከሎጥ ጋር ሆኖ ከዑር ተነሥቶ ወደ ካራን ሄደ። ከካራን ወጥቶ ወደ ከነዓን ምድር ሲገባ፥ ያችን ምድር ለዘሩ እንደሚሰጥ በግልጥ አነጋገረው፤ ዘፍ. 12፥7።

3. ለጥቂት ጊዜ በሴኬም፥ በቤቴልና በአዜብ ወይም በደቡብ አገር ቆይቶ በራብ ምክንያት ወደ ግብጽ ተጓዘ። ከዚያም ተመልሶ በኬብሮን ከቆየ በኋላ ከሎጥ በተለያየ ጊዜ አነጋገረው፤ ዘፍ. 13።

4. ወራሽ ልጅ እንደሌለው አይቶ ባዘነ ጊዜ በራእይ አነጋገረው፤ ዘፍ. 15፥1-21።

5. ስሙን አብርሃም ብሎ በለወጠ ጊዜ በግልጥ አነጋገረው፤ ዘፍ. 17።

6. በመምሬ የኦድባር ዛፍ ሥር ተገልጦ ካነጋገረው በኋላ ወደ ቤቱ ገብቶ ሚስቱ ሣራ ልጅ እንደምትወልድለት ተስፋውን ነገረው። በኋላም ስለ ሰዶምና ገሞራ ብዙ ጊዜ ከእግዚአብሔር ጋር ተወያየ፤ ዘፍ. 18።

7. ልጁን ይስሐቅን እንዲሠዋ በፈተነው ጊዜ አነጋግሮታል፤ ዘፍ. 22፥1-18።

አብርሃም እግዚአብሔር የሰጠውን ተስፋ ሳይጠብቅ አጋር ከተባለች ግብጻዊት ገረዱ እስማኤልን ወለደ፤ ዘፍ. 16። እግዚአብሔር ቃል ኪዳኑንና ምልክት የሆነውን ግዝረት ከሰጠው በኋላ ግን የተስፋ ልጁ ይስሐቅ ከሚስቱ ከሣራ ተወለደለት፤ ዘፍ. 17፤ 21፥1-3። ሚስቱ ሣራ ከሞተች በኋላ ኬጡራ



የአብርሃም አኗኗር

የተባለችውን ሴት አግብቶ 6 ልጆችን ወለደ፤ ዘፍ. 25፥1-2።

አብርሃም በከነዓን አገር በድንኳን ውስጥ ይኖር ነበር። ባረፈበትም ሁሉ መሠዊያን ይሠራ ነበር። ዘሩ አገሩን እንደሚወርስ ተተነበየለት። ተስፋውም በምድራዊ ርስት ብቻ ሳይሆን በሰማያዊ አገርም እንደሚፈጸም ተረዳ፤ ዕብ. 11፥8-16። በ175 ዓመቱ ሞተና በኬብሮን ተቀበረ፤ ዘፍ. 25፥9:10።

አብርሃም የተጠራበት ምክንያት ከዘሩ ክርስቶስ በሥጋ እንዲወለድ ነው። «የምድር ነገዶች በአንተ ይባረካሉ» የሚለው ተስፋ የተፈጸመው በክርስቶስ ነው። ስለዚህ በአ.ኪ. መጻሕፍት ብዙ ጊዜ ስሙ ተጠቅሷል።

ለምሳሌ :- 1. ለእግዚአብሔር ስለመታዘዙ፤ ዮሐ. 8፥39-40፤ ዕብ. 11፥17-19፤ ያዕ. 2፥21-24። 2. እምነቱ ጽድቅ ሆኖ ስለመቈጠሩ፤ የምእመናን ሁሉ አባት ስለመባሉና በእርሱ ምሳሌ በክርስቶስ የሚያምኑ ሁሉ በእምነት ስለመጽደቃቸው፤ ሮም 4፤ ገላ. 3፥6-7። 3. የዓለም ወገኖች ሁሉ በእምነት የአብርሃም እውነተኞች ልጆች የተስፋውም ወራሾች ተብለው ስለመጠራታቸው፤ ሮም 4፥11:12፤ 9፥7-8፤ ገላ. 3፥7-9:29።

<u>የአብርሃም እቅፍ፤</u>

ሉቃ. 16፥22-23። በአይሁድ አስተሳሰብ በአብርሃም እቅፍ መቀመጥ ማለት በእግዚአብሔር መንግሥት ከአብርሃም ጋር በደስታ መቀመጥ (መኖር) ማለት ነው፤ ማቴ. 8፥11።

**አብዩድ (አቢሁ)፤** የአሮን ሁለተኛ ልጅ፤ ዘጸ. 6፥23። እንደ ወንድሙ ተቀሠፈ፤ ዘሌ. 10። «ናዳብ» ይመ.

**አብያ፤** 1. ከ913-911 ከክ. ል. በይሁዳ የነገሠ የሮብዓም ልጅ፤ 2ዜ.መ. 13። 2. የኢዮርብዓም ልጅ፤ 1ነገ. 14፥1-18።

**አብያታር፤** በዳዊት ዘመነ መንግሥት የነበረ ካህን። በኖብ የነበሩ ካህናት ዳዊትን ስለረዱ ሳኦል ሲያጠፋቸው አብያታር ኤፉዱን ይዞ ወደ ዳዊት አመለጠ፤ 1ሳሙ. 22፥11-23፥9። በዳዊት ዘመን ሁሉ በክህነትና በአማካሪነት ያገለግል ነበር፤ 1ዜ.መ. 15፥11፤ 27፥34። አቤሴሎም ባመፀ ጊዜ ዳዊትን ለመርዳት በኢየሩሳሌም ቀረ፤ 2ሳሙ. 15፥35-37፤ 17፥15። በኋላ ግን አዶንያስን ስለደገፈ በሰሎሞን ተሻረ፤ 1ነገ. 1፥7-2፥35።

**አብድዩ፤** ትርጉሙ «የእግዚአብሔር አገልጋይ» ማለት ነው። 1. እግዚአብሔርን የሚፈራ የአክዓብ የግቢ አዛዥ። ኤልዛቤልም የእግዚአብሔርን ነቢያት ባስገደለች ጊዜ መቶውን ነቢያት ወስዶ በዋሻዎች ሸሸጋቸው። ለእንስሶችም ሣር ለመፈለግ በተላከ ጊዜ ኤልያስ አገኘው፤ አብድዩም ወደ ንጉሡ ተመልሶ የኤልያስን መምጣት ነገረው፤ 1ነገ. 18፥3-16። 2. ነቢዩ አብድዩ፤ አብ. 1።

**የአብድዩ ትንቢት፤** አብድዩ በኤዶምያስ ላይ ስለሚመጣው ፍርድ ተነበየ። ኤዶማውያን የተባሉት የዔሳው ዘሮች ከጥንት ጀምሮ በያዕቆብ ዘሮች በእስራኤል ላይ በጠላትነት ይነሣሡ ነበር፤ ዘፍ. 25፥23፤ አሞጽ 1፥11። አብድዩም፥ መከራ በደረሰባቸው ቀን በይሁዳ ሰዎች ላይ ስለፈጸሙባቸው ግፍ ይወቅሳቸዋል (አብ. 10-14)፤ ከአገራቸውም ፈጽመው እንደሚጠፉ ይናገርባቸዋል፤ አብ. 18። ይህም የይሁዳ የመከራ ቀን የናቡከደነፆር ሠራዊት ኢየሩሳሌምን ያቃጠለበት ቀን ይመስላል። በዚህ ምክንያት አብድዩ ትንቢቱን የተናገረው ከዚያ ጊዜ በኋላ እንደነበረ ይገመታል። አንዳንዶች ግን በይሁዳ ንጉሥ በአካዝ ዘመን እንደተናገረ ይተርካሉ፤ 2ዜ.መ. 28፥16:17።

አከፋፈል ፦

1. ቍ. 1-9 ፍርድ በኤዶምያስ ላይ።

2. ቍ. 10-14 የኤዶምያስ ቂምና ጭካኔ።

3. ቍ. 15-21 ፍርድ በኤዶምያስና በአሕዛብ ላይ፥ የጽዮን መዳን።

ዋና መልእክቱም፥ ቅን ፍርድ የሚፈረድበት «የእግዚአብሔር ቀን» ይመጣል (ቍ. 15-18)፤ «መንግሥቱም ለእግዚአብሔር ይሆናል» የሚል (ቍ. 21) ነው።

**አብጥሊስ፤** 81 ወይም 83 ቀኖና (አንቀጽ) ያለበት የሲኖዶስ መጽሐፍ ክፍል። «ሲኖዶስ» ይመ.

**አቦሊ፤** የክብደት መለኪያ፤ ግማሽ ግራም ያህል፤ ሕዝ. 45፥12። «ክብደት» ይመ.

**አተላ፤** የወይን፥ የጠጅ፥ የሌላም የማንኛውም መጠጥ ዝቃጭ ሁሉ አተላ ይባላል። የመቅሠፍት ምሳሌ ሆኖ ተጠቅሷል፤ መዝ. 75፥8። በብረት፥ በብርና በሌላም ማዕድን ላይ የሚታይ ዝገት። በዚህ ምሳሌ የእስራኤል ርኩሰት ተገልጿል፤ ሕዝ. 22፥18-22።

**አታሞ፤** እንደ ከበሮና እንደ ነጋሪት ያለ፥ ባለአንድ አፍ በእጅ ተይዞ የሚመታ አነስተኛ የዜማ ዕቃ፤ 1ሳሙ. 18፥6።



**አቴና፤** በግሪክ አገር አክሮፖሊስ በሚባል ኮረብታ ዙሪያ የተቋቋመች ከተማ። በሥነ ጥበብ በሥነ ሥርዓት ገናና ከተማ ሆነች። ጳውሎስ በሁለተኛው ጉዞው አቴናን ጐበኘ፤ ሐ.ሥ. 17፥15-34። «አርዮስፋጎስ»፥ «ኤፊቆሮስ»፥ «ኢስጦኢክ» ይመ.። ካ. 6ሸ።



በአቴና የነበሩ አብያተ ጣዖታት

**የአትክልት ስፍራ፤** አበባዎች፥ ዛፎችና ልዩ ልዩ ዓይነት ተክሎች የተተከሉበት ቦታ፤ ዘዳ. 11፥10፤ መክ. 2፥5:6፤ አሞጽ 4፥9። ብዙ ጊዜ በድንጋይ ወይም በእሾህ ይታጠር ነበር፤ ምሳ. 24፥31፤ ኢሳ. 5፥5። አንዳንድ ጊዜ መቃብር በአትክልት ቦታ ውስጥ ይደረግ ነበር፤ 2ነገ. 21፥18፤ ዮሐ. 19፥41። ደግሞም ባዕድ አምልኮ ይፈጸምበት ነበር፤ ኢሳ. 1፥29፤ 65፥3። «ገነት»፥ «ጌቴሴማኒ»፥ «የወይን አትክልት» ይመ.

**አነባ፤** አለቀሰ፤ እንባውን አፈሰሰ፤ 2ነገ. 8፥11:12።

**አነጸ፤** በድንጋይና በእንጨት በሌላም ቤት መሥራትን ያመለክታል፤ 1ቆሮ. 3፥12-15። በምሳሌያዊ አነጋገር ግን በእውነተኛው መሠረት በኢየሱስ ክርስቶስ ላይ ምእመናንን ማጽናትና ማበርታት ማለት ነው። በዚህም መሠረት የወንጌል ሰባኪ እንደ አናጺ ተመስሏል፤ 1ቆሮ. 3፥10-11። ታነጸ ማለትም በእውነተኛው የወንጌል ትምህርት ምእመናን መጽናታቸውንና የቤ.ክ.ን መደራጀት ያመለክታል፤ ሐ.ሥ. 9፥31፤ ኤፌ. 2፥20።

**አናሲሞስ፤** «ወደ ፊልሞና የተላከ መልእክት» ይመ.

**አናት፤** መሐል ራስ። «ዓመፃው በአናቱ ላይ ይወርዳል» ሲል ሙሉ ሰውነትን ያመለክታል፤ መዝ. 7፥16።

**አናጢ፤** በመ.ቅ. አገላለፁ በጠቅላላው የቤትን ሥራ የሚያቅድና የሚሠራ፤ 2ዜ.መ. 34፥11። ትልቅ ቤት ሲሠራ፥ ሥራው በአናጢ አለቃ ይቀየስ ነበር፤ 1ቆሮ. 3፥10። አናጢ ሕንፃ የሚሠራበትን መሬት በገመድ ወይም በዘንግ ይለካል፤ ሕዝ. 40፥3፤ ራእ. 21፥15። የሕንጻውም አቀማመጥ በቱንቢ ይመረመራል፤ 2ነገ. 21፥13፤ ኢሳ. 28፥17። «ተግባረ እድ» ይመ.

**አንቋረረ፤** በሥቃይ ምክንያት ጮኸ ማለት ነው፤ ሕዝ. 26፥15።

**አንበሪ፤** በትልቅ ባሕር ውስጥ የሚኖር ዓሣ መሳይ ፍጡር። የአንበሪ እንስት እንደ ከብት ልጅዋን ጡት ታጠባለች፤ ዘፍ. 1፥21።

**አንበሳ፤** ጥንት አንበሳ በእስራኤል አገር ይገኝ ነበር። ዛሬ ግን ጠፍቷል፤ መሳ. 14፥5:6፤ 1ሳሙ. 17፥34:35። ትልቅና ብርቱ አውሬ ስለሆነ የነገሥታት ምሳሌ ነው (ምሳ. 30፥29-31)፤



አንበሳ

በተለይም ዳዊትና ንጉሣዊ ወገንነት ያላቸው ሁሉ ከይሁዳ ነገድ የሚወለዱ ስለሆነ ይሁዳ የአንበሳ ደቦል (ልጅ) ተብሎ በትንቢት ተሰየመ፤ ዘፍ. 49፥9። ኢየሱስ ክርስቶስም የትንቢቱ የመጨረሻ ፈጻሚ ስለሆነ ከዚህ ነገድ በመወለዱ የይሁዳ አንበሳ ተባለ፤ ማቴ. 2፥5:6፤ ራእ. 5፥5። በሌላ ጥቅስ ሰይጣን በጉጂነቱ ምክንያት በአንበሳ ተመስሏል፤ 1ጴጥ. 5፥8። እንዲሁም አንበሳ የፍርድ ምሳሌ ነው፤ 2ነገ. 17፥24-26፤ ሆሴዕ 5፥14።

**አንበጣ፤** ብዙ ዓይነት አንበጣ አለ። አራቱ ዓይነት በእስራኤላውያን ዘንድ ለምግብ ተፈቅዷል፤ ዘሌ. 11፥22። አንበጣ በበረሃ አሸዋ ተፈልፍሎ የሚራባ ሲሆን፥ በየጊዜው ሰውነቱን እየለወጠ፥ መጀመሪያ ክንፍ የሌለው ተንቀሳቃሽ፥ ቀጥሎም ኩብ ኩብ እያለ የሚሄድ ኩብኩባ፥ በኋላም ያልጠነከረ ክንፍ አውጥቶ የሚፈናጠር፥ በመጨረሻም ብዙ ሆኖ በክንፍ እየበረረ ከአገር ወደ አገር የሚዛመት ነው። ሣር፥ እህል፥ ቅጠል ሁሉ ይበላል። በልዩ ልዩ ጥቅስ የአንበጣ መቅሠፍት የእምላክን ቍጣ ያመለክታል፤ ዘጸ. 10፥4-6፤ መዝ. 105፥34:35፤ ኢዩ. 1፥4።



አንበጣ ቅጠል ሲበላ

**አንባላይ፤** (አምባላይ)፤ ነጭ መልክ። አብዛኛውን ጊዜ ለፈረስ የሚነገር ቃል ነው፤ ዘካ. 1፥8፤ 6፥3፤ ራእ. 6፥2፤ 19፥11:14።

**አንባር፤** (አምባር)፤ ከወርቅ ከሌላም ማዕድን የሚሠራ። በክንድ ላይ የሚደረግ፥ ቀለበት መሰል ጌጥ። በጋብቻ ጊዜ ሙሽራ ለሙሽሪት አንባር ይሰጣል፤ ዘፍ. 24፥22፤ 38፥18።



የግብጽ አንባሮች

**አንቲጳጥሪስ፤** በባሕር ዳር ካለው ከኢዮጴ 15 ኪ.ሜ. ርቆ በሰማርያ አቅጣጫ የሚገኝ ከተማ። ንጉሥ ሄሮድስ ጥንት አፌቅ በነበረበት ቦታ ላይ

የአባቱን ስም ለማስጠራት ይህን ከተማ ሠራ። ጳውሎስ ታስሮ ወደ ቂሣርያ ሲወሰድ አንድ ሌሊት በአንቲጳጥሪስ አደረ፤ ሐ.ሥ. 23፥31።

**አንካሳ**፡ በትክክል ለመራመድ የማይችል፤ ዘሌ. 21፥18። ክርስቶስና ሐዋርያት አንካሳዎችን ፈወሱ፤ ማቴ. 11፥5፤ ሐ.ሥ. 3፥2-8፤ 4፥22፤ 8፥7፤ 14፥8-10። የመንፈሳዊ ድካም ምሳሌ ነው፤ 1ነገ. 18፥21፤ ዕብ. 12፥13። «በሽታ» ይመ.

**አንኰራፋ**፡ አንገረበደ፤ ፈረስ በአፍንጫው ፉር ፉር የሚል ድምፅ እያሰማ ሲጐደፍር አንኰራፋ ይባላል፤ ኢዮብ 39፥20።

**አንዠረገገ**፡ ፍሬ በብዛት አፈራ፤ መ.መ. 7፥13።

**አንደበት**፡ ምላስ፥ የቃል መፍለቂያ፥ በአንጎል ውስጥ የንግግር ችሎታ ያለበት ክፍል። የሰው ጠባይና ስሜት በአንደበቱ ይገለጣል፤ መዝ. 51፥14፤ 64፥3፤ ምሳ. 6፥17፤ 10፥20፤ ኤር. 9፥3:8፤ ያዕ. 3፥6-8። አንደበቱን የማይገታ ወደ ስሕተት ያመራል፥ የሚገታው ግን ፍጹም ሰው ይባላል፤ ያዕ. 1፥26፤ 3፥2። ምላስ የንግግርና የጣዕም መለያ አካል ነው። ትንሽ ብልት ሲሆን ብዙ ነገርን ይሠራል፤ ምሳ. 18፥21፤ ያዕ. 3፥3-5።

**አንድነት**፡ (ኅብረት)። ክርስቶስ ምእመናን ሁሉ አንድ እንዲሆኑ ጸለየ፤ ዮሐ. 17፥20:21። በመስቀሉም በአይሁድና በአሕዛብ መካከል የነበረውን ጥል በማስወገድ አንድ አደረጋቸው፤ ኤፌ. 2፥14-16። የምእመናን ተስፋ፥ አካል፥ መንፈስ፥ ሃይማኖት፥ ጥምቀት፥ ጌታና አምላክ አንድ ናቸው፤. ኤፌ. 4፥4-6። ነገር ግን ብዙ የተለያዩ አብ.ክ. አሉና መለያየታቸው የክርስቶስ ፈቃድ አይመስልም። ከመጀመሪያ ጀምሮ ስለ አንዳንድ ጥቃቅን ጉዳዮች ልዩ ልዩ አሳብ፥ ሥርዐት ወይም ድርጊት ነበረ። ለምሳሌ ሐ.ሥ. 15፥19-21፤ ሮም 14፥5:6፤ ቆላ. 2፥16:17 ይመ. እንደዚሁም አሳቾች እንደሚነሡ ሐዋርያት ተናገሩ፤ ሐ.ሥ. 20፥29:30፤ 1ቆሮ. 11፥19፤ 2ጴጥ. 2፥2። ቢሆንም ምእመናን በፍቅር እንጂ በመለያየት መኖር አይገባቸውም፤ ዮሐ. 13፥34:35፤ 1ዮሐ. 3፥23፤ ያዕ. 4፥1-3። ዛሬ ስለ አብ.ክ. አንድነት የሚደክሙ ብዙዎች አሉ። አንድነት የሚገኘው በተለይ በድርጅት ሳይሆን፥ በእውነትና በፍቅር በአገልግሎትም ነው፤ ኤፌ. 4፥11-16።

**አንድያ**፡ ተቀዳሚና ተከታይ የሌለው አንድ ብቻ ማለት ነው። ቃሉ ለክርስቶስ ሲነገር በልደቱ በኩል ተቀዳሚና ተከታይ የሌለው መሆኑን ይገልጣል፤ ዮሐ. 3፥16። በልዩ ልዩ ክፍል ስለ ክርስቶስ ሲነገር «አንድ ልጅ» የሚለው ይህን አሳብ ይገልጣል፤ ዮሐ. 1፥14:18፤ 1ዮሐ. 4፥9።

**አንጀት**፡ ከሆድ ክፍሎች አንዱ። ጥልቅ ስሜትና ርኅራኄ ይገለጠበታል፤ ኤር. 4፥19፤ ሰ.ኤ. 1፥20።

**አንገት**፡ ብዙ ጊዜ እልከኛነትን (ዘጸ. 32፥9፤ ኢሳ. 48፥4፤ ሐ.ሥ. 7፥51)፥ በተሸካሚነቱም የባርነትን ትርጕም ይገልጣል፤ ዘፍ. 27፥40፤ ኤር. 30፥8።

**አንጐራጐረ**፡ «አጕረመረመ» ይመ.

**አንጥረኛ**፡ ወርቅና ብር፥ ብረታ ብረትም በእሳት አቅልጦ የሚያነጥር፤ ኢዮብ 28፥1፤ ኢሳ. 40፥19። የፈታኝ ምሳሌ ነው፤ ምሳ. 17፥3፤ ዘካ. 13፥9፤ ሚል. 3፥2:3፤ 1ጴጥ. 1፥6:7።

**አንጾኪያ**፡ 1. የሶርያ አንጾኪያ 301 ከክ. በ. በአሮንቴስ ወንዝ የተቋቋመች ከተማ። 65 ከክ. በ. የሮም መንግሥት የሶሪያ መናገሻ ከተማ አደረጋት። ትልቅም ከተማ ሆነች። የመጀመሪያዋ የአሕዛብ ቤ.ክ. እዚያ ተመሠረተች፤ ሐ.ሥ. 11፥19-26። ጳውሎስና በርናባስ እዚያ ወንጌልን አስተማሩ፤ ሐ.ሥ. 15፥35። ጳውሎስና ጓደኞቹ ለሦስቱ የስብከተ ወንጌል ጕዞ ከአንጾኪያ ቤ.ክ. ተላኩ፤ ሐ.ሥ. 13፥1-4፤ 15፥35-41፤ 18፥22:23። ስለ አሕዛብ መገረዝ በተነሣው ክርክር ምክንያት እነጳውሎስ ከአንጾኪያ ወደ ኢየሩሳሌም ተላኩ፤ ሐ.ሥ. 15። ካ. 6 አ።




አውግስጦስ ቄሣርን የሚያሳይ የሶሪያ አንጾኪያ ገንዘብ

2. በጲስድያ ተራራማ አገር አጠገብ ያለች አንጾኪያ በትንሹ እስያ ክፍል አገር የምትገኝ ከተማ። በመጀመሪያ ጕዞው ጳውሎስ ከበርናባስ ጋር በአንጾኪያ ወንጌልን አስተማረ፤ ሐ.ሥ. 13፥14-14፥19። በሁለተኛና በሦስተኛ ጕዞውም አንጾኪያን ሳይጐበኛት አልቀረም፤ ሐ.ሥ. 16፥6፤ 18፥22-23። ዛሬ አንጾኪያ ባድማ ሆናለች። ካ. 6በ።

**እእላፋት**፡ የብዛት ቍጥር። ዐሥር መቶ ሺህ ወይም አንድ ሚሊዮን ነው። ነገር ግን በመ.ቅ. ውስጥ ከፍ ባለና ሊቈጠር ለማይችል ቍጥር የተጠቀሰ ይመስላል፤ ዳን. 7፥10፤ ሚክ. 5፥2፤ ይሁዳ 14:15፤ ራእ. 5፥11።

**አእምሮ**፡ የዕውቀትና የአሳብ መኖሪያ፥ መገኛና መውጫ። በመ.ቅ. አእምሮ እንደ ሰው ልብ ክፉ ወይም መልካም ሊሆን ይችላል፤ ሮም 7፥25፤ ቆላ. 2፥18።

**አኪያ**፡ «እግዚአብሔር ወንድሜ ነው» ማለት ነው። በዚህ ስም ብዙ ሰዎች ተጠርተዋል። ከእነርሱ የታወቀው ለኢዮርብዓም ስለ መንግሥቱ መከፈል፥ ቀጥሎም ስለ ቤተሰቡ ውድቀት የተነበየው ነቢይ ነው፤ 1ነገ. 11፥29-39፤ 14፥6-16።

**አኪጦፌል፤** የንጉሥ ዳዊት አማካሪ፤ 2ሳሙ. 15፥12። አቤሴሎም በአባቱ በዳዊት ላይ ባደመ ጊዜ፥ አኪጦፌል በአድማው ተባበረው። ነገር ግን ዳዊትን በፍጥነት እናሳድደው የሚል ምክሩን አቤሴሎም ሳይቀበለው በመቅረቱ፥ አኪጦፌል ወደ ቤቱ ተመልሶ በገዛ እጁ ታንቆ ሞተ፤ 2ሳሙ. 17፥1-23።

**አካል፤** የሕዋሳት ሁሉ ሙሉ አቅዋም (1ቆሮ. 15፥40-44)፥ በምሳሌነት በሁለት መንገድ ይነገራል። 1. ምእመናን ሁሉ በክርስቶስ አንድ አካል ናቸው፥ እንደ ብልቶች ሆነው እያንዳንዱ አገልግሎት ይኖረዋል፤ ሮም 12፥4:5፤ 1ቆሮ. 12፥12-27። 2. ምእመናን ሁሉ ከክርስቶስ ጋር አንድ ስለሆኑ ቤተ ክርስቲያን የክርስቶስ አካል ናት፤ ክርስቶስም ራስዋ ነው፤ ኤፌ. 2፥16፤ 4፥12-16።

**አካን፤** ለእግዚአብሔር የተቀደሰውን የኢያሪኮን ምርኮ ለራሱ የወሰደ እስራኤላዊ። በዚህ ስርቆት ምክንያት እስራኤላውያን ጋይ በተባለችው ከተማ በተደረገው በመጀመሪያ ውጊያ ተሸነፉ። ኃጢአቱ በተገለጠ ጊዜ ከነቤተሰቡ ተወገረ፤ በእሳትም ተቃጠለ፤ ኢያሱ 7፥1-26።

**አካዝ፤** የእስራኤል መንግሥት በሁለት ከተከፈለ በኋላ በይሁዳ የነገሠ 12ኛ ንጉሥ። ከ732-716 ከክ.በ. ነገሠ። አባቱ ኢዮአታም ነበረ። የጣዖትን አምልኮ በይሁዳ አስፋፋ። በእግዚአብሔር ፊት እጅግ ክፉ ሥራ የሠራ ንጉሥ ነበር። ሶርያና የእስራኤል መንግሥት ይሁዳን በጦርነት ሰላስቸገሩት አካዝና ሕዝቡ ተሸበሩ። ነቢዩ ኢሳይያስ «ብታምኑ ትድናላችሁ» ብሎ ምክር ሰጠ። አካዝ ግን ምክሩን ችላ በማለት የአሦር ንጉሥ እንዲረዳው ለመነ፤ 2ነገ. 16፤ 2ዜ.መ. 28። አልተቀበለውም እንጂ «እነሆ ድንግል ትፀንሳለች፥ ወንድ ልጅም ትወልዳለች፥ ስሙንም አማኑኤል ብላ ትጠራዋለች» የሚለው የክርስቶስን መወለድ የሚያመለክተው ትንቢታዊ ቃል የተነገረው ለንጉሥ አካዝ ነው፤ ኢሳ. 7፥10-14።

**አካዝያስ፤** 1. ከ853-852 ከክ.በ. የነገሠ የእስራኤል ዘጠነኛ ንጉሥ፤ 1ነገ. 22፥51-53፤ 2ነገ. 1፥1-18። 2. በ841 ከክ.በ. የነገሠ የይሁዳ ስድስተኛ ንጉሥ፤ 2ዜ.መ. 22፥1-9። 3. ነቢዩ አሞጽን የተቃወመው የቤቴል ካህን፤ አሞጽ 7፥10-17።

**አካይያ፤** በአሁኑ የግሪክ አገር ውስጥ ከቆሮንቶስ በስተደቡብ የሚገኝ አውራጃ፤ ሐ.ሥ. 19፥21፤ 1ቆሮ. 16፥15። ጥንት የአካይያ ዋና ከተማ ቆሮንቶስ ነበረ፤ 2ቆሮ. 1፥1። ካ. 6ን።

**አኬልዳማ፤** የደም መሬት ማለት ነው። አስቆሮታዊው ይሁዳ ጌታችንን የሸጠበትን ገንዘብ ሲመልስ፥ የካህናት አለቆች በብሩ የሸክላ ሠሪ መሬት ለእንግዶች መቃብር ገዙ። የደም መሬት የተባለበት ምክንያት በደም ዋጋ ስለተገዛ፥ ወይም ይሁዳ ስለሞተበት ይሆናል፤ ማቴ. 27፥3-10፤ ሐ.ሥ. 1፥18:19።

**አክሊል፤** የክብር ምልክትና መደምደሚያ፥ ትልቅ ማዕረግና ክብር ያላቸው ሰዎች የሚቀዳጁት፤ ሲኤ. 5፥16። የብ.ኪ. ሊቃነ ካህናት አክሊልን ይቀዳጁ (ይጭኑ) ነበር፤ ዘጸ. 29፥6። ሙሴ በጽላቱ ማስቀመጫ በታቦቱ ላይ አክሊልን እንዲቀርጽ ታዘዘ፤ ዘጸ. 25፥11። ወታደሮች ክርስቶስን እንደ ንጉሥ አድርገው ሲያላግጡበት በራሱ ላይ የእሾህ አክሊል ጫኑበት፤ ማቴ. 27፥29። ግሪኮች በእስፖርት አሸናፊ ለሆነ የአበባ አክሊል ይሸልሙ ነበርና ይህ ለክርስቲያን ድል አድራጎት ምሳሌ ሆነ፤ 2ጢሞ. 4፥8፤ ራእ. 2፥10።



በስፖርት ውድድር ለአሸናፊ ይሰጥ የነበረ ከቅጠል የተሠራ አክሊል

**አክብሮት፤** ለእግዚአብሔር፥ ለባለሥልጣን፥ ለሰው ሁሉ የሚሰጥ ክብር፤ ሮም 12፥10፤ 13፥7፤ 1ጴጥ. 2፥17። ሆኖም ለእግዚአብሔር የምንሰጠው አክብሮት አምልኮትን ሲጨምር፥ ለፍጡራን በምንሰጠው አክብሮት ግን አምልኮት የለበትም፤ ሐ.ሥ. 10፥26፤ ራእ. 19፥10፤ 22፥8-9። «ስግደት»፥ «አምልኮ» ይመ.

**አክዓብ፤** የአባት ወንድም ማለት ነው። የዘንበሪ ወይም የአምሪ ልጅ በእስራኤል መንግሥት የነገሠ ሰባተኛ ንጉሥ። ዘመነ መንግሥቱም 874-853 ከክ.በ. ነው። ጠቅላላ ታሪኩ ከ1ነገ. 16፥28-22፥40ና በ2ዜ.መ. ም. 18 ተጽፏል። በመንግሥት አስተዳደር በኩል ጠንካራ ንጉሥ ነበረ። ነገር ግን እግዚአብሔርን የማይፈራ ሆኖ ተገኘ። ከእርሱ በፊት ከነበሩት ሁሉ ይልቅ በእግዚአብሔር ፊት ክፉ አደረገ የሚል ከባድ ቃል ተጽፎበታል፤ 1ነገ. 16፥30። ኤልዛቤል የተባለች ሚስቱ ፈሪሀ እግዚአብሔርን ለማጥፋትና አምልኮ ባዕድን በአገሪቱ ለማስፋፋት ተጣጣረች። አክዓብ ከሶርያው ንጉሥ ከወልደ አዴር ጋር ሦስት ጊዜ ተዋጋ። በሦስተኛው ዘመቻ በጽኑ ቈሰለ፤ 1ነገ. 22፥34-36። ነቢዩ ኤልያስ በእስራኤል መካከል እግዚአብሔርን ያገለገለው በአክዓብ ዘመነ መንግሥት ነው፤ 1ነገ. 16፥28-22፥40።

**አኻያ (አሀያ)፤** በወንዝ ዳር የሚበቅል ዛፍ፤ ዘሌ. 23፥40፤ ኢዮብ 40፥22።

**አውራቂስ፤** ለመርከብ አደገኛ የሆነ ምሥራቃዊ ነፋስ፤ ሐ.ሥ. 27፥14።

**አውሬ፤** «አራዊት» ይመ.

**አውታር፤** የበገና ገመድ። በብሉ. መዘምራን ዐሥር አውታር ባለው በገና ይዘምሩ ነበር፤ መዝ. 33፥2፤ 92፥3። የቀስት ደጋን በአውታር ይለጠጣል፤ መዝ. 11፥2። የድንኳን መወጠሪያም አውታር ይባላል፤ ኢሳ. 33፥20፤ 54፥2።

**አውግስጦስ፤** «ቄሣር» ይመ.

**አዕማድ፤** «ዐምድ» ይመ.

**አዕዋፍ፤** የወፍ ብዛት፤ መዝ. 50፥11። «ወፎች» ይመ.

**አዘበዘበ፤** ገድግዳው፥ ጣራው፥ ግንቡ፥ አጥሩ፥ ቅጥሩ ሊወድቅ አዘነበለ፤ ወደ ፊት አሰገደደ፤ አጎነበሰ፤ አረገረገ፤ ኢሳ. 30፥13።

**አዛሄል፤** ትርጉሙ «እግዚአብሔር ያያል» ማለት ነው። የሶርያን ንጉሥ ወልደ አዴርን ገድሎ በፈንታው ነገሠ፤ 2ነገ. 8፥7-15። ለኤልያስና ለኤልሳዕ እንደተገለጠላቸው እግዚአብሔር እስራኤላውያንን ከክፋታቸው የተነሣ በአዛሄል እጅ አሳልፎ ሰጣቸው፤ 1ነገ. 19፥15-17፤ 2ነገ. 8፥12፤ 10፥32:33፤ 13፥1-3። አዛሄል ግን ከሚገባ በላይ እጅግ ጨከነባቸው፤ 2ነገ. 13፥7:22-25፤ አሞጽ 1፥3-5። በኢየሩሳሌም ላይ ዘመተ፤ ብዙ ገንዘብም ማርኮ ተመለሰ፤ 2ነገ. 12፥18:19።

**አዛዥ፤** በላይ ያለ፥ ትእዛዝ የሚሰጥ፤ ምሳ. 6፥7።

**አዛጦን፤** ምሽግ ማለት ነው። ከአስቀሎና ወደ ሰሜን 15 ኪ.ሜ. የሚርቅ በታላቁ ባሕር አቅራቢያ ያለ ከተማ። ከፍልስጥኤማውያን አምስት ከተሞች አንዱ ነበረ፤ ኢያሱ 13፥3። ታቦቱ በተማረከ ጊዜ በጣዖታቸው በዳጎን ቤት እንዲኖር ወደ አዛጦን ተወሰደ፥ ነገር ግን በኋላ ለእስራኤላውያን ተመልሷል፤ 1ሳሙ. 5፥1-8። ግብጻውያን ከተማውን ካፈረሱት በኋላ ሮማውያን እንደገና ሠሩት። ካ. 3ሪ።

**አዜብ፤** በምዕራብና በደቡብ መካከል ያለ አቅጣጫ፤ ዘፍ. 12፥9፤ 13፥1። ንግሥተ ሳባ ለእስራኤል አዜብ ከሚሆን አገር መጣች፤ ማቴ. 12፥42።

**አዝሙድ፤** የወጥ ቅመም፥ ጥቁር ወይም ነጭ ቀለም ያለው፤ ኢሳ. 28፥25፤ ማቴ. 23፥23።



**አዞ፤** በደረቱ የሚሳብ፥ በሞቃት አገር በወንዝ ውስጥና በወንዝ ዳር የሚኖር፥ ሰውንና እንስሳን የሚበላ አውሬ፤ ዘሌ. 11፥30፤ ኢዮብ 40፥25፤ ሕዝ. 29፥3-5።



**የአየር ጠባይ፤** በሕዋ ዙሪያ የሚታይ የአየር ንብረት። ይህም ማለት ሙቀት፥ ቅዝቃዜ፥ ርጥበት፥ ድርቅ፥ ዝናም፥ ብራ ... ወዘተ በሕዋ መታየት። በከነዓን አገር ከኅዳር እስከ ጥር፥ በመጋቢትም ዝናብ ይዘንባል፤ ኤር. 5፥24፤ ኢዩ. 2፥23። በክረምት ጊዜ ብርድ ይበዛል፤ ዕዝ. 10፥9:13፤ ኤር. 36፥22። በአርሞንዔም ተራራ ጫፍ በረዶ ዘወትር ይታያል፤ በጨው ባሕር አካባቢ ግን ዝቅተኛ ቆላ ስለሆነ ኃይለኛ ሙቀት አለ። በታላቁ ባሕር አጠገብ ሙቀት ቢበዛም እንኳን ነፋስ አለና ለመኖሪያ ይመቻል። ሰማይን በመመልከት የሚቀጥለው ቀን የአየር ጠባይ ሊታወቅ ይቻላል፤ ኢዮብ 37፥9፤ ማቴ. 16፥2:3።

**አይሁድ፤** የይሁዳ ነገዶች፥ የሚጠሩበት የብዙ ቍጥር ስም። በመጀመሪያ ቃሉ በይሁዳ የሚኖሩትን ሰዎች ያመለክታል፤ 2ነገ. 16፥6፤ 18፥26። በኋላም ከምርኮ ከተመለሱት የሚበልጡቱ ከይሁዳ ነገድ ስለሆኑ፥ እንደዚሁም ወደ ይሁዳ አገር ስለተመለሱ ቃሉ፥ በይሁዳም ሆነ በሌላ አገር ለሚገኙ ለያዕቆብ ዘሮች ሁሉ መጠሪያ ሆነ፤ ኤር. 34፥9፤ ሐ.ሥ. 2፥5፤ 16፥1። ነገር ግን ክርስቶስን ስላልተቀበሉ፥ አይሁድነታቸው እውነተኛ እንዳልሆነ ተነግሯል፤ ሮም 2፥28፤ ራእ. 2፥9፤ 3፥9።

**አይጥ፤** 1ሳሙ. 6፥1-18፤ ኢሳ. 66፥17። «እንስሳት» ይመ.

**አደረ፤** 1. ሌሊትን በአንድ ቦታ ማሳለፍ፤ ዘፍ. 19፥2። 2. ሰዎችም ሆኑ መላእክት በእግዚአብሔር ጸጋና መንፈስ ሲሞሉ እግዚአብሔር አደረባቸው በሚል ቃል ይገለጣል፤ ይህም በመንፈስ ተሞልተዋል ማለት ነው፤ ራእ. 7፥15። 3. አደረ የሚለው አንቀጽ የቃልን ሰው መሆን (ትስብእት) ይገልጣል፤ ዮሐ. 1፥14።

**አዲስ ኪዳን፤** 1. በብሉይ ኪዳን የተተነበየ (ኤር. 31፥31-34) እና ክርስቶስ ደሙን አፍስሶ ያቆመው ቃል ኪዳን ነው፤ ሉቃ. 22፥19:20። አዲስ ኪዳን ብሉይ ኪዳንን ፍጹም አድርጎታል፤ በአሮጌውም ፈንታ አዲሱ ተተክቷል፤ ዕብ. 8፥13። አዲስ ኪዳን በድንጋይ ላይ ሳይሆን በልብ፥ በቀለም ሳይሆን በመንፈስ ተጻፈ፤ የኵነኔ ሳይሆን የጽድቅ አገልግሎት አለው፤ ለጊዜው ሳይሆን ለዘለዓለም ጸንቶ ይኖራል። አርነትንም ስለሚሰጥ ተቀባዮቹ ወደ ጌታ መልክ ይለወጣሉ፥ ስለዚህ ክብሩ ከፍ ያለ ነው፤ 2ቆሮ. 3፥4-18።

2. በሐዋርያት ሥልጣን የተጻፉት ቅዱሳት መጻሕፍት አዲሱን ኪዳን ስለሚገልጡ አዲስ ኪዳን ተብለዋል። እነዚህም መጻሕፍት ወንጌላት፥ የሐዋርያት ሥራ፥ መልእክታት፥ ራእይ ተብለው በአራት ክፍል ይከፈላሉ። «ቃል ኪዳን» ይመ.

**የአዲስ ኪዳን ስፍረ ዘመን፤** ስለ ዓመተ ምሕረትና ስለ ክርስቶስ የልደት ጊዜ አቈጣጠር «ዓመት» ይመ.። በአ.ኪ. የተተረኩ ብዙዎች ድርጊቶች በዓለም ታሪክ መዛግብት ውስጥ ጎልተው የማይታዩ ስለሆነ፥ የተፈጸሙባቸውን ዓመቶች በትክክል ለመወሰን ያዳግታል። ሆኖም ሊቃውንት በተለያዩ ምክንያቶች የክርስቶስ ሕማማት በ30 ወይም በ33 ዓ.ም. እንደነበረ ይገምታሉ፤ ዮሐ. 5፥1። ፋሲካን ወይም የዳስን በዓል ካመለከተ የክርስቶስ አገልግሎት ሦስት ዓመት ይሞላል። ጥምቀቱም በ26 ወይም በ29 ዓ.ም. ይሆናል፤ ዮሐ. 2፥13፤ 5፥1፤ 6፥4፤ 12፥1። ከሮማውያን የተገኙ ጽሑፎች የአግሪጳ ሞት በ44 ዓ.ም. (ሐ.ሥ. 12፥23)፥ በጋልዮስ ፊት የጳውሎስ መከሰስ በ52 ዓ.ም. (ሐ.ሥ. 18፥12) እንደሆነ ይገልጣሉ። ከዚህም የተነሣ በሐዋርያት ሥራ የተተረከ አንዳንድ ድርጊት የተፈጸመበትን ጊዜ ልንወስን እንችላለን።

የገላትያን መልእክትና የሐዋርያትን ሥራ ዘመናት በሁለት መንገድ ለማዛመድ ይቻላል። አንዳንዶች የጳውሎስን ሁለተኛ የኢየሩሳሌም ጕብኝት ከራብ እርዳታ ጕብኝት ጋር ሌሎችም ከኢየሩሳሌም ጉባኤ ጋር ያዛምዱታል፤ ገላ. 2፥1፤ ሐ.ሥ. 11፥30፤ 15። ጳውሎስ በሮም ታስሮ ሳለ እንደሚፈታ ተስፋ አደረገ፤ ሐ.ሥ. 28፥30:31፤ ፊል. 1፥25:26፤ ፊልሞና 22። ተፈትቶም ወደ ግሪክ አገርና ወደ ቀርጤስ ሄደ። ቀጥሎም እንደገና እንደሚታሰርና የሞት ፍርድ እንደሚፈረድበት ተረዳ፤ በሮም ሞተ ብለው ብዙዎች ይገምታሉ፤ 2ጢሞ. 4፥6:7:13:16:20፤ ቲቶ 1፥5። የሮም ንጉሥ ኔሮን ጴጥሮስንና ጳውሎስን እንዳስገደለ፥ ዮሐንስም እስኪሸመግል ድረስ በእስያ እንደኖረ በቤ.ክ. ታሪክ ይተረካል። የሚከተለው ሰንጠረዥ በአ.ኪ. ታሪክ ዋና ዋና ድርጊቶችና የአ.ኪ. መጻሕፍት የተጻፉበትን ዓመት በቅደም ተከተል ይገልጣል።

| ዓ.ም. | የአዲስ ኪዳን ታሪክ | የአዲስ ኪዳን መጻሕፍት |
|---|---|---|
| 26 | የኢየሱስ ጥምቀት፤ ዮሐ. 1÷32-34። | |
| 27 | ፋሲካ ፤ ዮሐ. 2÷13። | |
| 28 | ፋሲካ (ወይም የዳስ በዓል) ዮሐ. 5÷1። | |
| 29 | ፋሲካ ፤ ዮሐ. 6÷4። | |
| 30 | ፋሲካ÷የኢየሱስ ሞትና ትንሣኤ፤ ዮሐ. 12÷1። | |
| 33 | የጳውሎስ ወደ ጌታ መመለስ፤ ሐ.ሥ. 9÷1። | |
| 46 | የራብ እርዳታ፤ ሐ.ሥ. 11÷30፤ | ማቴዎስ (?) |
| 46-47 | 1ኛው የወንጌል ጕዞ፤ ሐ.ሥ. 13-14። | ገላትያ ÷ ያዕቆብ |
| 48 | የኢየሩሳሌም ጉባኤ፤ ሐ.ሥ. 15። | |
| 49-52 | 2ኛው የወንጌል ጕዞ፤ ሐ.ሥ. 16-18። | 1ኛና 2ኛ ተሰሎንቄ |
| 53-58 | 3ኛው የወንጌል ጕዞ፤ ሐ.ሥ. 19-21። | 1ኛና 2ኛ ቆሮንቶስ ÷ ሮም |
| 58-60 | ጳውሎስ በቂሣርያ ታሰረ፤ ሐ.ሥ. 22-26። | ማርቆስ÷ኤፌሶን÷ፊልጵስዩስ÷ ቆላስይስ |
| 61-63 | ጳውሎስ በሮም ታሰረ፤ ሐ.ሥ. 27-28። | ፊልሞና÷ሉቃስ÷የሐዋርያት ሥራ |
| | | 1ኛ ጢሞቴዎስ ÷ ቲቶ |
| 64-65 | ጳውሎስ ተፈትቶ በግሪክ አገር | 1ኛና 2ኛ ጴጥሮስ ÷ ይሁዳ |
| | | 2ኛ ጢሞቴዎስ |
| 67 | የጳውሎስና የጴጥሮስ ሞት። | ማቴዎስ (?) ÷ ዕብራውያን |
| 70 | የኢየሩሳሌም መፍረስ። | የዮሐንስ ወንጌል |
| | | 1ኛ÷ 2ኛና 3ኛ ዮሐንስ |
| 100 | የዮሐንስ ሞት | የዮሐንስ ራእይ |

**አዳም፤** አዳም ማለት ከመሬት የተፈጠረ ማለት ነው። ቃሉ ሰውን ወይም ሰዎችን ሁሉ ያመለክታል። ከዚህ በላይ ግን የመጀመሪያው ሰው የሚጠራበት ስም ሆነ፤ ዘፍ. 2፥19-25። አዳም በእግዚአብሔር መልክ ተፈጠረ፤ ዘፍ. 1፥27። እግዚአብሔርም እንዲያበጃትና እንዲጠብቃት በዔድን ገነት አኖረው። የምድርንም ፍጥረት እንዲገዛ ሥልጣን ሰጠው። ፈጣሪ አምላክ ሰውን ወንድና ሴት አድርጎ ፈጠረ። ሁለቱም አንድ ሥጋ ይሆናሉ በማለት አንድነታቸውን ባረከ፥ «ብዙ ተባዙ፤ ምድርንም ሙሉአት፤ ግዙአትም» አላቸው፤ ዘፍ. 1፥28፤ 2፥24። አዳምና ሚስቱ ለእግዚአብሔር ስላልታዘዙ፥ ከዔድን ገነት እንዲወጡ ተገደዱ፤ ዘፍ. 3። ሐዋርያው ጳውሎስ በሮም 5፥12-21 እንዳስተማረን በአዳም ውድቀት ምክንያት ኃጢአትና ሞት ወደ ሰው ሁሉ ደረሰ። ነገር ግን ኋለኛው አዳም በተባለው በክርስቶስ መልካም ሥራ በኩል በክርስቶስ ለሚያምኑበት ሁሉ ጽድቅና ሕይወት ተገኘ፤ 1ቆሮ. 15፥22:45።

**አዳራሽ፤** ሰፊ የቤት ክፍል። ኢየሱስና ደቀ መዛሙርቱ የፋሲካን እራት በደርብ ላይ ባለ ታላቅ አዳራሽ ውስጥ በሉ፤ ማር. 14፥15። በታው የት እንደሆነ አሁን አይታወቅም። ክርስቶስ በትንሣኤ ዕለት በዚህ ታይቷል (ዮሐ. 20፥19)፤ ምናልባት ደቀ መዛሙርቱ የመንፈስ ቅዱስን መምጣት ይጠባበቁበት የነበረው ቤት ይህ ሳይሆን አይቀርም፤ ሐ.ሥ. 1፥13:15። ይህ ቤት ብዙ ሰዎች ጴጥሮስ እንዲፈታ የጸለዩበት የማርቆስ እናት የማርያም ቤት ሊሆን ይችላል፤ ሐ.ሥ. 12፥12።

**አዳር፤** «ወር» ይመ.

**አዳኘ፤** አስጠነቀቀ፥ አጥብቆ ተናገረ። በዘካ. 3፥6 የማስጠንቀቂያ አሳብ አለበት።

**አዳኝ፤** «መድኃኒት» ይመ.

**አድመኛነት፤** ጠብን፥ ክርክርን፥ መለያየትን መፍጠር፤ በተለይ በእውነት ላይ ክርክርን ማንሣት። አድመኛነት የሥጋ ሥራ እንጂ የመንፈስ ፍሬ አይደለም፤ ገላ. 5፥20፤ ያዕ. 3፥16፤ 2ቆሮ. 12፥20። ፍርድን ያስከትላል፤ ሮም 2፥8።

**አገልጋይ፤** አጋዥ፥ ረዳት። ኢያሱ የሙሴ አገልጋይ ነበረ፤ ኢያሱ 1፥1። ካህናት የመቅደስ (ዘጸ. 28፥43)፥ ባለ ሥልጣናት የእግዚአብሔር አገልጋዮች ናቸው፤ ሮም 13፥4። ሐዋርያትና ተከታዮቻቸው የእግዚአብሔር (1ተሰ. 3፥2)፥ የክርስቶስ (ሮም 15፥15:16)፥ የወንጌል (ኤፌ. 3፥7)፥ የአ.ኪ. (2ቆሮ. 3፥6)፥ የቤ.ክ. (ቆላ. 1፥25) አገልጋዮች ናቸው። ከሁሉም በላይ ክርስቶስ የአገልግሎትን አርአያ አሳይቷል፤ ማር. 10፥42-45፤ ዮሐ. 13፥4:5። «የቤተ ክርስቲያን አስተዳደር» ይመ.

**አገልግሎት፤** እግዚአብሔርንና ሰውን ማገልገል የክርስቲያን መብት ነው፤ ዘኁ. 3፥6፤ ማር. 10፥44:45። «አምልኮ»፥ «አገልጋይ» ይመ.

**አጋር፤** የሣራ ግብጻዊት ገረድ። ሣራ ልጅ እንድትወልድለት ለአብርሃም ሚስት ትሆነው ዘንድ አጋርን ሰጠችው። አጋርም እስማኤልን ወለደችለት፤ ዘፍ. 16፥1-16። ይስሐቅ ከተወለደ በኋላ እግዚአብሔር እንዳዘዘው አብርሃም አጋርንና እስማኤልን አሳደደ። በበረሃ እግዚአብሔር ተናገራት፤ የውሃ ጉድጓድንም አሳያት፤ ዘፍ. 21፥8-21። ጳውሎስ ሕግን በመጠበቅ ራሳቸውን ለማጽደቅ የሚያስቡትን በአጋርና በእስማኤል መሰለ፤ ገላ. 4፥21-31።

**አጋቦስ፤** «በዓለም ሁሉ ታላቅ ራብ ይሆናል» ብሎ ትንቢት የተናገረ በኢየሩሳሌም የኖረ ነቢይ፤ ሐ.ሥ. 11፥27-30። ሐዋርያው ጳውሎስን ወደ ኢየሩሳሌም ብትሄድ ትታሰራለህ ብሎ አስጠነቀቀው፤ ሐ.ሥ. 21፥10-11፤ 24፥5-6።

**አጋና፤** አንድን ነገር ለመግዛትም ሆነ ለመሸጥ የሚደረግ የውል ስምምነት፥ የዋጋ ውሳኔ። እንደዚሁም የተዋሱትን ዕቃና የተበደሩትን ገንዘብ ለመመለስ እጅ በመምታት መሐላ ማድረግ አጋና ይባላል፤ ምሳ. 17፥18፤ 22፥26።

**አጋዘን፤** «እንስሳት» ይመ.

**አጋንንት፤** የጋኔን ብዙ ቍጥር ነው። «ጋኔን» ይመ.

**አግሪጳ፤** «ሄሮድስ» ይመ.

**አግዳሚ፤** ከግድግዳ እስከ ግድግዳ የሚጋደም ዋልታ ተሸካሚ እንጨት። ሠረገላም ይባላል፤ ለድንኳንና ለቤት ያገለግላል፤ 1ነገ. 7፥2:3።

**አግድመት፤** አጭር ርቀት። አንድ ምዕራፍ ያህላል፤ 2ነገ. 5፥19።

**አጓጉት፤** በሰው ገላ ላይ የሚወጣ፥ ወደ ሥጋ ውስጥ ጠልቆ የማይገባ፥ ዙሪያውን የሚያፈከፍክና የማይቈስል፥ ቆዳን የሚያገረጣ ነጭ በሽታ፤ ዘሌ. 13፥39።

**አጕረመረመ፤** አለመደሰትን በድምፅ፥ በሹክሹክታ፥ በስሞታ ወይም በግልጥ አሳየ፥ አንጐራጐረ። እስራኤል በሙሴ ላይ (ዘጸ. 15፥24፤ 16፥2-8፤ ዘኁ. 14፥2-36፤ 17፥5:10)፥ አይሁድ በክርስቶስ ላይ አጕረመረሙ፤ ሉቃ. 5፥30፤ 15፥2፤ ዮሐ. 6፥41-43:61፤ 7፥32። አማኞች እንዳያጕረመርሙ ታዝዘዋል፤ 1ቆሮ. 10፥10፤ ፊል. 2፥14፤ 1ጴጥ. 4፥9፤ ይሁዳ 16።

**አጠናጠነ፤** መልሶ መላልሶ አሰበ፤ አሰላሰለ፤ አወጣ አወረደ፤ አርቆ አሰበ፤ መዝ. 77፥5።

**አጣቢ፤** ጨርቅ ቀለም ከመግባቱ በፊት አጣቢው ዘይቱን ለማውጣት ጨርቁን ያጥብ ነበር። አጣቢዎች ከእንዶድ፥ ከናትር ከሌላም በተሠራ ሳሙና ተጠቅመዋል፤ ኢሳ. 7፥3፤ ኤር. 2፥22፤ ሚል. 3፥2፤ ማር. 9፥3። «ተግባረ እድ» ይመ.

**አጥንት፤** በምሳሌነት ሲገለጥ የሚከተሉትን ነገሮች ያመለክታል። 1. የሰው ኃይል፤ መዝ. 53፥5፤ ኢሳ. 38፥13። 2. የሰው ክብር፥ ስለዚህ የሰው አጥንት በጥንቃቄ መቀበር ይገባዋል፤ ዘፍ. 50፥25፤

ዕብ. 11፥22። 3. የቅርብ ዝምድና መግለጫ፤ ዘፍ. 29፥14፤ መሳ. 9፥2።

**አጨ፤** መተጫጨት። በመ.ቅ. እንደምናገኘው ሰዎች ከተጫጩ በኋላ እንደተጋቡ ሰዎች ሆነው ስለሚቈጠሩ ወደ ሌላ መሄድ አይፈቀድላቸውም ነበር፤ ዘፍ. 29፥21፤ ማቴ. 1፥18-20። እግዚአብሔር ለእስራኤል ያለው ፍቅርና ታማኝነት በመተጫጨት ተመስሏል፤ ሆሴዕ 2፥21:22። ብዙ ጊዜ የወንዱ ወላጆች ሴቲቱን ይመርጣሉ። አንዳንድ ጊዜም እንደ ሶምሶን ወንዱ ራሱ ሴቲቱን ይመርጣል፤ መሳ. 14፥1:2። ወይም ኑኃሚን ቦዔዝን ለሩት እንደመረጠችና ሳኦል ሜልኮልን ለዳዊት እንደሰጠ፥ የሴቲቱ ወላጆች ወንዱን ይመርጡ ነበር፤ ሩት 3፥1-4፤ 1ሳሙ. 18፥22። በመተጫጨት ጊዜ ሦስት ዐይነት ስጦታ ወይም እንግልግሎት ይሰጥ ነበር ፦ 1. ወንዱ ለሴቷ ቤተሰብ፤ ዘፍ. 29፥18፤ 34፥12። 2. ወንዱ ለሴቷ፤ ዘፍ. 24፥53። 3. የሴቷ ወላጆች ለሴቷ፤ መሳ. 1፥11-15። ይህም ሁሉ ከተደረገ በኋላ ማጨት በጋብቻ ይፈጸማል።

**አጨዳ፤** የዱር ሰዎች እህላቸውን በእጅ በመንቀልና በመስበር ይሰበስቡ ነበር። ቀጥሎም በባልጩት፥ የብረት ሥራም ከለመዱ በኋላ በብረት ማጭድ ማጨድ ጀመሩ። በደቦ ወይም በወበራ ያጭዱ ነበር፤ ሩት 2፥4-7፤ ማቴ. 13፥30። የንጉሥ አጨዳ ሕዝቡ በአዝመራ ጊዜ ለንጉሡ የሚውለው ኩዳድ ነው፤ አሞጽ 7፥1። አጨዳ ብዙ ጊዜ የሥራ ውጤት ምሳሌ ነው፤ ምሳ. 22፥8፤ ሆሴዕ 8፥7፤ 1ቆሮ. 9፥11፤ ገላ. 6፥7:8።

**አጭ፤** «እንስሳት» ይመ.

**አጵሎስ፤** ከእስክንድርያ ከተማ የመጣ፥ የተማረ አይሁዳዊ። በኤፌሶን ይኖሩ የነበሩት ጵርስቅላና አቂላ ስለ ክርስትና ሃይማኖት ካስተማሩት በኋላ ወደ ቆሮንቶስ ሄዶ፥ ታላቅ የወንጌል አስተማሪ ሆነ፤ ሐ.ሥ. 18፥24-28። በኋላም አማኞቹ ስለ ጳውሎስና ስለ አጵሎስ መሪነት ተከራክረው ተለያዩ። በአጵሎስና በጳውሎስ መካከል ግን መለያየት አልነበረም፤ 1ቆሮ. 1፥12፤ 3፥4-6:22፤ 16፥12፤ ቲቶ 3፥13።

**አጽናኝ፤** አስታራቂ፥ አማካሪ፥ የሚያበረታታና የሚያረጋጋ ማለት ነው። ክርስቶስ በምድር ሳለ የሐዋርያት አጽናኝ ነበረ፤ በኋላም አጽናኝ የሆነውን መንፈስ ቅዱስን ላከላቸው፤ በዚህ ምክንያት «ሌላ አጽናኝ» ተብሏል፤ ዮሐ. 14፥16:26፤ 16፥7። «መንፈስ ቅዱስ» ይመ.

**አፈከፈከ፤** የቍስል መላላጥ፥ ከዳነ በኋላ እንደገና መቍሰል፤ ኢዮብ 7፥5።

**አፋዛዥ፤** አንጸር፥ ትይዩ ማለት ነው፤ ዘኍ. 2፥2።

**አፌቅ፤** ሦስት ወይም አራት ከተሞች በዚህ ስም ተጠርተዋል። ነገር ግን ዛሬ የት እንደነበሩ በእርግጥ አይታወቅም። አንዱ ግን በአ.ኪ. ዘመን አንቲጳጥሪስ ተብሏል። እርሱም ከኢዮጴ 15 ኪ.ሜ. ርቆ በኤፍሬም አቅጣጫ ነበረ። ፍልስጥኤማውያን ታቦቱን ማርከው በአፌቅ አስቀመጡት፤ 1ሳሙ. 4፥1-11። ከዚህም ተነሥተው፥ ዘምተው ሳኦልን በጊልቦዓ ተራራ ላይ ገደሉት፤ 1ሳሙ. 29፥1፤ 31፥1-6።

**አፍ፤** የልብ አሳብ መግለጫ፥ የቃል መውጫ፤ መዝ. 119፥108፤ ማቴ. 12፥34። ቃሉ ከሰው አሳብ ለሚወጣው ድርጊት ሁሉ መታወቂያ ይሆናል፤ መዝ. 59፥12፤ ምሳ. 15፥14፤ ራእ. 19፥15። ከዚህም ሌላ አፍ ማለት የሚከተሉትን አሳቦች ይዞ ይገኛል፤ አስተርጓሚ (ዘጸ. 4፥16)፥ ቃል አቀባይ (ኤር. 15፥19)፥ ቃል (ማቴ. 18፥16)፥ መልካም ምኞትና ልመና፤ መዝ. 81፥10።

**አፍላል፤** የሥጋ መቀቀያ ትልቅ ማሰሮ፤ 1ሳሙ. 2፥14። የክፉ ነገር ምሳሌ ነው፤ ኤር. 1፥13።

**አፍሮዲጡ፤** ከፊልጵስዩስ ምእመናን ስጦታ ይዞ ወደ ጳውሎስ የተላከ መልእክተኛ፤ ፊል. 2፥25-30፤ 4፥18።

**አፎት፤** የፍላጻ መያዣ፤ ኢሳ. 22፥6። «የጦር መሣሪያ» ይመ.

**ኡሪምና ቱሚም፤** ሊቀ ካህናት በሚለብሰው በኤፉዱ ላይ ባለው የደረት ኪስ ውስጥ የሚከተቱ ሁለት ዕቃዎች፤ ዘጸ. 28፥30፤ ዘዳ. 33፥8። ኡሪምና ቱሚም ከምን እንደተሠሩ ወይም እንዴት ያሉ እንደነበሩ አልተገለጠም፤ በኡሪምና በቱሚም የእግዚአብሔር ፈቃድ ይጠየቅ ነበር፤ ዘኍ. 27፥21፤ ዕዝ. 2፥63። ዳዊት በኡሪም (በኤፉድ) እግዚአብሔርን በጠየቀ ጊዜ መልስ አገኘ፤ 1ሳሙ. 23፥6-12። ሳኦል ግን ቢጠይቅ መልስ አጣ፤ 1ሳሙ. 28፥6።



ኡሪምና ቱሚም የነበሩበት የኤፉድ የደረት ኪስ

**ኢምንት**፤ ባዶ፥ ሀልውና የሌለው፥ ያልነበረ፥ ከንቱ፥ ብላሽ፤ ኢሳ. 41፥29።

**ኢሳይያስ**፤ «እግዚአብሔር ደኅንነት ነው» ማለት ነው። በይሁዳ ነገሥታት በዖዝያን፥ በኢዮአታም፥ በአካዝና በሕዝቅያስ ዘመን ከ740-688 ከክ.ል. ትንቢት የተናገረ ነቢይ ነው። በአካዝና በሕዝቅያስ ዘመነ መንግሥት የቤተ መንግሥት አማካሪ ነበረ። አባቱ አሞጽ ይባላል፥ ሆኖም ከነቢዩ አሞጽ ሌላ ነው፤ 2ነገ. 19፥1-2፤ ኢሳ. 1፥1። ኢሳይያስ ነቢይ እንዲሆን የተጠራው ዖዝያን በሞተበት ዓመት ነው፤ ኢሳ. 6። በንጉሡ በአካዝ ዘመነ መንግሥት የሶርያና የሰማርያ ሠራዊት ወደ ይሁዳ በዘመቱ ጊዜ ኢሳይያስ የራሱን ልጆች ምልክት እያደረገ አካዝ በእግዚአብሔር እንዲታመን እንጂ እንዳይደነግጥ መከረው፤ አካዝ ግን ጠላቶቹን እንዲቋቋምለት ለማድረግ ለአሦር ንጉሥ ግብር ይልክለት ነበር፤ ኢሳ. 7፥1-17፤ 8፥1-4፤ 2ዜ.መ. 28፥16-21። የአሦር መንግሥት እየተስፋፋ ሲሄድ የይሁዳ አለቆች ለእርዳታ ወደ ግብጽ ተመለከቱ፤ ኢሳይያስም ወደ ውጭ መመልከታቸው በእግዚአብሔር አለማመን መሆኑን ገልጾ ተናገረ፤ ራሱንም ምልክት አደረገ፤ ኢሳ. 20፤ 30፥1-5። የአሦር ንጉሥ የይሁዳን ከተማዎች በእጁ አድርጎ በኢየሩሳሌም ላይ ዛቻ ሲናገር፥ ኢሳይያስ ስለ አሦራውያን መሸነፍ ተነበየ፤ እንደ ትንቢቱ ቃልም የአሦር ሠራዊት በቸነፈር ተመታ (2ነገ. 18፥13-19:37፤ 2ዜ.መ. 32፥16-21፤ ኢሳ. 36፤ 37)፤ ሕዝቅያስ በታመመ ጊዜ በኢሳይያስ ትንቢት መሠረት ከእግዚአብሔር ምልክት ተሰጠው (2ነገ. 20፥1-11)፤ በኋላም ኢሳይያስ የሕዝቅያስ ልጆች ወደ ባቢሎን ይማረካሉ ብሎ ትንቢት ተናገረ፤ ኢሳ. 39። «ያሱብ» ይመ.

**የኢሳይያስ ትንቢት**፤ ኢሳይያስ የነገሥታትን ታሪክ መጻሕፍትና የትንቢት መጽሐፍ ጻፈ፤ 2ዜ.መ. 26፥22፤ 32፥32፤ ኢሳ. 8፥1። ከጥንት ጀምሮ «ትንቢተ ኢሳይያስ» 700 ከክ.ል. ይነበረው ነቢይ በኢሳይያስ የተጻፈ መሆኑ ታምኖበታል። ባለፉት 200 ዓመታት ውስጥ ግን ብዙ ምርመራ ስለተደረገ፥ በዘመናውያን ሊቃውንት መካከል ልዩ ልዩ አሳብ ተገኝቷል። ኢሳይያስ ራሱ ከም. 1-39 ካሉት ትንቢቶች የሚበልጡትን ጽፎ ይሆናል እንጂ፥ ም. 40-55 በባቢሎን ምርኮ ጊዜ በነበረ በሌላ ነቢይ፥ 56-66 ደግሞ ከምርኮ በኋላ በነበረ በሌላ ነቢይ ተጽፏል የሚሉ አሉ። ሌሎች ደግሞ ም. 1-39ና ም. 56-66 በልዩ ልዩ ክፍል ክፍለው በብዙ ሰዎች እጅ የተጻፈ ይመስላል ይላሉ።

ለዚህ አሳብ ሁለት ሁለት ዋና ምክንያቶች ተሰጥተዋል። 1ኛ፥ አንድ ነቢይ በዘመኑ ለሚኖሩ ሰዎች ስለሚናገር፥ ኢሳይያስ ከዘመኑ በኋላ በባቢሎን ምርኮኞች ለሆኑት የጻፈ አይመስልም የሚል አሳብ አለ። ነገር ግን ነቢያት የሚናገረው የእግዚአብሔር መንፈስ ቅዱስ ሥራ በዚህ ዓይነት አሳብ የሚወሰን አይደለም። 2ኛ፥ በም. 1-39ና በም. 40-66 መካከል የአጻጻፍ ልዩነት፥ ሌላም ልዩነት ስለሚታይ ነው። ነገር ግን ከዚህ በታች እንደሚታየው የትንቢተ ኢሳይያስ መልእክት በየክፍሉ ስለሚመጣው መሲሕ ጠለቅ ያለና አንድ ዓይነት አሳብ አለው። ደግሞም ነቢዩ በተለያየ ዘመንና በተለያየ ርእስ ያቀረበው አጻጻፍ ቢለያይ አያስገርምም። ልዩነት ቢኖርም በየክፍሉ እርስ በርሳቸው የሚስማሙ አሉ። ለምሳሌ፥ ከሌሎች ነቢያት ይልቅ ኢሳይያስ «የእስራኤል ቅዱስ» በሚል አጠራር ስለ እግዚአብሔር ይናገራል፤ ኢሳ. 1፥4፤ 37፥23፤ 41፥16፤ 60፥14።

ከብ.ኪ. ዘመን ጀምሮ «ትንቢተ ኢሳይያስ» በዕብራይስጥ ቅዱሳት መጻሕፍት መካከል ተቈጥሯል። ከመጽሐፉ ጠቅላላው ክፍል በተጠቀሰ ጊዜም የነቢዩ ኢሳይያስ ቃል መሆኑ ተረጋግጧል። ለምሳሌ ሐዋርያው ዮሐንስ በወንጌሉ ከሁለቱ ዋና የመጽሐፉ ክፍሎች ሁለት ጥቅሶችን «ደግሞ» በመጥቀስ ኢሳይያስ እንደጻፋቸው ይገልጣል፤ ዮሐ. 12፥38-41ን ከኢሳ. 53፥1 እና ከ6፥9-10 ጋር ያስተያዩ።

የኢሳይያስ ዋና መልእክት፥ «የእስራኤል ቅዱስ» በዓለም ሁሉ ላይ ነግሦ፥ በዐመፀኞች ላይ በመፍረድ፥ የሚያምኑበትንም በማዳን ኃያል መሆኑን ማሳየት ነው። መጽሐፉን በሦስት ክፍል ልንከፍለው እንችላለን ፦

1ኛው ም. 1-39፤ በኢሳይያስ ዘመን በሆኑት ድርጊቶች ምክንያት የተጻፈ ነው። በዚህ ክፍል እግዚአብሔር ቅዱስ ስለሆነ ዐመፀኛ በሆነው ሕዝቡና በሌሎችም ላይ ፍርድ እንደማይቀር ሲገልጥ የመንግሥቱን ክብርና በረከት ያስረዳል።

2ኛው ም. 40-55፤ ከኢሳይያስ ዘመን በኋላ በሆነው በባቢሎን ምርኮ ምክንያት ተጽፏል። በዚህ ክፍል፥ እግዚአብሔር አዳኝ ነውና ሕዝቡን ወደ አገራቸው እንደሚያመጣቸው ሲገልጥ ከዚህ የበለጠውን መዳን ለዓለም ሁሉ እንደሚያደርስ ያሳያል።

3ኛው ም. 56-66፤ የጽዮንን ዘላለማዊ ክብር ያሳያል። በዚህ ክፍል ክፉትን የሚመርጡት እንደሚጠፉ፥ እግዚአብሔርም የእርሱ በሆኑት እንደሚደሰት ይናገራል።

ኢሳይያስ ስለሚመጣው መሢሕ በሰፊው ይናገራል፤ የአ.ኪ. ጸሐፊዎችም ኢሳይያስን እየጠቀሱ የተነበየለት ኢየሱስ እንደሆነ ያረጋግጣሉ። የሚመጣው ከድንግል እንደሚወለድ (7፥14፤ ማቴ. 1፥23)፥ መንግሥቱ ለዘለዓለም እንደሆነ (9፥6:7)፥ ሌላው መንገዱን እንደሚያዘጋጅለት (40፥3-5፤ ማቴ. 3፥3)፥ በገሊላ እንደሚሠራ (9፥1:2፤ ማቴ. 4፥14-16)፥ የእግዚአብሔር መንፈስ በእርሱ ላይ እንደሚሆን (61፥1፤ ሉቃ. 4፥17-19)፥ ሕመምተኞችን እንደሚፈውስ (53፥4፤ ማቴ. 8፥16:17)፥ በየዋህነት እንደሚሠራ (42፥1-3፤ ማቴ. 12፥18-21)፥ የእምነት መሠረት እንደሚሆን (28፥16፤ ሮም 9፥32:33)፥ አሕዛብን እንደሚያድን (65፥1:2፤ ሮም 10፥20) ኢሳይያስ ተናገረ። ከሁሉ በላይ ስለ መሢሕ ትንቢት የሚገኝበት ስለ እግዚአብሔር «ባሪያ» በሚናገረው ክፍል ነው፤ 42፥1-4፤ 49፥1-7፤ 50፥4-9፤

52፥13-53፥12። በተለይ ምዕራፍ 53 የክርስቶስን ሕማማት በትንቢት ይገልጻል፤ ይህ ቃል ብዙ ጊዜ በአ.ኪ. ተጠቅሷል፤ ሉቃ. 18፥31-33፤ ዮሐ. 12፥37:38፤ ሐ.ሥ. 8፥32-35፤ ሮም 4፥24:25፤ 1ጴጥ. 2፥24:25። ደግሞም የእስራኤል እልከኝነት ብዙ ጊዜ በኢሳይያስ ተገልጧል፤ በአ. ኪ.ም ተጠቅሷል፤ 1፥9ና ሮም 9፥29፤ 6፥9:10ና ማር. 4፥11:12፤ 29፥13ና ማቴ. 15፥8:9።

አከፋፈል ፦

1. ኢሳይያስ በራሱ ዘመን ስለሚሆኑት ድርጊቶች የተናገረው ትንቢት።

ሀ) ስለ ኢየሩሳሌምና ስለ ይሁዳ፤ ም. 1-12።

ለ) ስለ አሕዛብ፤ 13-23።

ሐ) ስለ እግዚአብሔር ዓላማና ፍርድ፤ 24-35።

መ) የአሦራውያን መሸነፍ፥ ስለ ባቢሎን ምርኮም የተነገረ ትንቢት፤ 36-39።

2. በባቢሎን ምርኮ ምክንያት የተነገረ ትንቢት። የእግዚአብሔር ሕዝብ መጽናናትና መመለስ፤ 40-55።

3. ስለ ጽዮን ዘለዓለማዊ ክብር የተነገረ ትንቢት። የከፉዎች መወገድና የእግዚአብሔር ሕዝብ ደስታ፤ 56-66።

**ኢስጦኢኮች፤** ከሦስት መቶ ዓመት ከክ. በ. በአቴና የተነሡ የፍልስፍና ተከታዮች። ኢስጦኢኮች ዓለም በአንድ ጠቅላላ ሕግ እንደተመሠረተና እንደተያዘ ያምናሉ። ስለዚህ ሰው እጅግ ሳያዝንና እጅግ ሳይደሰት በዚህ ሕግ ተመርቶ መኖር ይገባዋል ይሉ ነበር፤ ሐ.ሥ. 17፥18:32።

**ኢቆንዮን፤** በትንሹ እስያ በገላትያ ጠቅላይ ግዛት ያለች ከተማ። ጳውሎስ በዚህ ቦታ ወንጌልን አስተማረ፤ ሐ.ሥ. 13፥51፤ 14፥1-5፤ 16፥1-5፤ 2ጢሞ. 3፥11። ዛሬ ኮኒያ ትባላለች። ካ. 6በ።

**ኢታምር፤** ከአሮን አራት ልጆች ታናሹ፤ ዘጸ. 6፥23። ከወንድሞቹ ጋር ለክህነት ተለየ፤ ዘጸ. 28፥1፤ 1ዜ.መ. 24፥1-19 ይመ.

**ኢትዮጵያ፤** የቃሉ ትርጒም ጥቁር ማለት ነው፤ ኤር. 13፥23። በግሪክና በመ.ቅ. ጸሐፊዎች አስተሳሰብ ኢትዮጵያ ከግብጽ በስተደቡብ ጥቁር ዐባይና ነጭ ዐባይ እስከሚገናኙበት የነበረ አገርና መንግሥት ነው፤ በመ.ቅ. ከ40 ጊዜ በላይ ተጠቅሷል። «በኢትዮጵያ ወንዞች ማዶ ላለች ...» ሲል የአክሱም መንግሥት የነበረባትን ምድር ሊያመለክት ይችላል፤ ዘፍ. 2፥13፤ ኢሳ. 18፥1፤ ሶፎ. 3፥10።

ኢትዮጵያውያን በንጉሡ በአሳ ጊዜ ወደ እስራኤል አገር ሲዘምቱ ተሸነፉ፤ 2ዜ.መ. 14፥9-15። የኢትዮጵያ ንጉሥ ቲርሐቅ በሕዝቅያስ ጊዜ አሦርን ተቃወመ፤ 2ነገ. 19፥9። በኋላም የአሦር መንግሥት ኢትዮጵያውያንን አሸነፋቸው፤ ናሆም 3፥8-10። ናቡከደነፆር የግብጽንና የኢትዮጵያን ወታደሮች በከርከሚሽ ውጊያ አሸነፈ፤ ኤር. 46፥1-10። የፋርስ መንግሥት ኢትዮጵያን ገዛ፤ አስ. 1፥1፤ 8፥9።

ኢትዮጵያ በምሳሌነት የማይወሰን የእግዚአብሔርን ግዛት ይገልጣል። ኢትዮጵያም እጆችዋን ወደ እግዚአብሔር እንደምትዘረጋ ተተንበየ፤ መዝ. 68፥31፤ 87፥4፤ ሕዝ. 30፥4-9፤ አሞጽ 9፥7፤ ሶፎ. 2፥12። በኢትዮጵያና በዐረብ አገር መካከል የቀረበ ግንኙነት እንደነበረ ታውቋል፤ 2ዜ.መ. 21፥16። «ሳባ» ይመ.

**ኢን፤** የውሃ፥ የወይን፥ የዘይት መስፈሪያ፤ ሕዝ. 4፥11፤ ዘጸ. 29፥40፤ ዘሌ. 23፥13። «መስፈሪያ» ይመ.

**ኢኮንያን፤** በ597 ከክ.በ. የነገሠ የይሁዳ ንጉሥ። ዮአኪን ተብሎም ይጠራል። ማቴዎስ የኢዮስያስ ልጅ ይለዋል። ግን ኢዮስያስ አያቱ እንጂ አባቱ አይደለም። አባቱ ኢዮአቄም (ኤልያቄም) ነው፤ 2ነገ. 24፥8-17፤ ሕዝ. 1፥2፤ አስ. 2፥6፤ 1ዜ.መ. 3፥16:17፤ ኤር. 22፥24-30፤ ማቴ. 1፥11። «ዮአኪን» ይመ.

**ኢየሩሳሌም፤** የሰላም ከተማ ማለት ነው። የዮርዳኖስ ወንዝ ወደ ጨው ባሕር ከሚገባበት በምዕራብ 30 ኪ.ሜ. ከታላቁ ባሕር 50 ኪ.ሜ. ርቃ በተራራማ አገር የምትገኝ ከተማ። ኢየሩሳሌም ከባሕሩ ወለል 750 ሜትር ገደማ ከፍ ትላለች። ስለዚህም ቀጥተኛ የሆነ የንግድ መንገድ አልነበራትም። ካ. 3ሰ።

የኢየሩሳሌም ጥንታዊ ስም ሳሌም ነበረ (ዘፍ. 14፥18)፥ ቀጥሎም ኢያቡስ (ኢያሱ 15፥63፤ 18፥16)፥ ዖፌል (2ዜ.መ. 27፥3፤ 33፥14)፥ ጽዮን ተብላለች (መዝ. 137፥1)፥ ቅድስት ከተማም ተብላ ተጠርታለች፤ ነህ. 11፥1። ዳዊት ኢየሩሳሌምን ከኢያቡሳውያን ከወሰደ በኋላ የእስራኤል ሁሉ በተለይም የይሁዳ ዋና ከተማና መስገጃ አደረጋት፤ 2ሳሙ. 5፥6-10። ኢየሩሳሌም ለአይሁድና ለክርስቲያን አንደኛ፥ ለእስላምም ሦስተኛ ቅድስት ከተማ ናት።

<u>የኢየሩሳሌም ቅጥሮች፤</u>

የዳዊት ከተማ ዖፌል ብቻ ነበረ። ስፋቱም 600 በ100 ሜትር ያህል ይሆናል። ሰሎሞን ከተማይቱን አስፋፍቶ ቤተ መቅደስን ሠራ። የሰሎሞን ግቢ ዛሬ ኤል አቅሳ የሚባለው መስጊድ ያለበት ቦታ ነው። በኋላም ዖፌል ታችኛው ከተማ ተባለና ላይኛው ከተማ በስተምዕራብ ተሠራ። ሁለቱም ከተሞች በየራሳቸው ተቀጠሩ፤ በመካከልም የታይሮፒዮን ሸለቆ ነበረ። የላይኛው ከተማ ቅጥር በስተሰሜን አንደኛው ቅጥር ይባላል። ነህምያ ሁለቱን ከተማዎች በአንድ ቅጥር ውስጥ አደረገ። ሄሮድስ ከተማይቱን በሰሜን አስፋፍቶ ቅጥርን ሠራ። ይህም 2ኛ ቅጥር ተባለ። ሄሮድስ አግሪጳ 1ና2 እንደገና በሰሜን ሌላ 3ኛ ቅጥር ሠሩ። ክርስቶስ የተሰቀለበት ቀራንዮ የሚገኘው ሄሮድስ ከሠራው ከሁለተኛው ቅጥር ውጭ በኋላም ከተሠራው ከሦስተኛው ቅጥር ውስጥ ነው።

ዛሬ ጥንታዊት ከተማ የምትባለው ስፋትዋ 800 በ800 ሜትር ያህል ነው። በከተማይቱ ዙሪያ



በጌታችን ዘመን ደብረ ዘይት ላይ ሆኖ ኢየሩሳሌም ሲታይ

የሚታየው ቅጥር በ1540 ዓ.ም. ገደማ ተሠራ። ዛሬ ጥንታዊት የምትባለው ከተማ በክርስቶስ ጊዜ ከነበረችው በስተሰሜን ናት። ደግሞም ከተማይቱ በጦርነት ሰባት ጊዜ ስለፈረሰች፥ እንደገናም በፍርስራሹ ላይ ስለተሠራች ከክርስቶስ ዘመን ወዲህ መሬትዋ ስድስት ሜትር ያህል ወደ ላይ ከፍ ብሏል። በዚህ ምክንያት የዱሮ ዘመን ድርጊቶች የተፈጸሙባቸው በታዎች አይታዩም፤ በትክክል ለመወሰንም አይቻልም።

## የኢየሩሳሌም ታሪክ፤

ከሰሎሞን በኋላ በይሁዳ መንግሥት ዘመን ኢየሩሳሌም በጠላት ተይዛለች። በመጨረሻም ናቡከደነፆር በ587 ከክ.በ. አፈረሳት፤ 2ነገ. 25። ሰባ ዓመት ቆይቶ የፋርስ ንጉሥ ቂሮስ አይሁድ ተመልሰው እንዲሠሩአት ፈቀደ። እነዘሩባቤልም መጥተው ቤተ መቅደስን ሠሩ። ነህምያም በ445 ከክ.በ. ቅጥሩን ሠራ። ከ169-167 ከክ.በ. የሶርያ ንጉሥ አንጥያኮስ ከከተማውና ከቅጥሩ ብዙውን አፈረሰ። መቃብያን ግን እንደገና ሠሩአቸው። የፋርስና የሮም ወታደሮች ኢየሩሳሌምን ያዙ። በኋላም በሮም ፈቃድ የነገሠ ሄሮድስ ኢየሩሳሌምን ይዞ ከተማይቱን አስፋፋ፤ ቅጥሩንም አጠነከረ። ሄሮድስ ቤተ መቅደሱን አሳደሰና በሰሜን በኩል ከተማይቱን ለመጠበቅ ከፍ ያለውን የአንቶንያን ግንብ ሠራ። በዚህ ግንብ ክርስቶስ በጲላጦስ ፊት ተከሰሰ። የሮም ወታደሮች ከዚሁ ግንብ ውስጥ ወጥተው ጳውሎስን ከሚደበድቡት አዳኑት፤ ሐ.ሥ. 21፥31-36። ከጸፍጸፉ አንዳንድ ክፍል (ዮሐ. 19፥13)፥ እንደዚሁም የግንቡ ውሃ ጕድጓድና እስር ቤት እስከ ዛሬ ድረስ ይታያሉ። የቤተ መቅደስ አደባባይ በክርስቶስ ዘመን 500 በ300 ሜትር ያህል ነበረ፤ ዛሬ የሚታየው የአደባባይ ስፋት ከዚህ ትንሽ ይበልጣል። ኢየሱስ እንደተነበየው ከቤተ መቅደስ ድንጋዮች ድንጋይ በድንጋይ ላይ ተሠርቶ የነበረው ወድቋል፤ ማር. 13፥1:2። ዛሬ አይሁድ ስለ ቤተ መቅደስ መፍረስ የሚያለቅሱበት የቤተ መቅደስ ምዕራባዊ ቅጥር (የልቅሶ ግድግዳ) ራሱ የቤተ መቅደስ ግድግዳ ሳይሆን፥ ንጉሥ ሄሮድስ በምዕራብ በኩል ቤተ መቅደስ የቆመበትን ስፍራ ለማስፋፋት ያስቀመጣቸው የመሠረት ድንጋዮች ናቸው። ሮማውያን በ70 ዓ.ም. ከተማይቱን ፈጽመው አፈረሱ። በክርስቶስ ዘመን ከነበሩ ሕንፃዎች ከተማይቱን ያፈረሱ ወታደሮች ይኖሩበት የነበረው የሄሮድስ ግቢ ግንብ ብቻ ከመሬት በላይ ይታያል። ከዚያም ወዲህ ከተማይቱ አልፎ አልፎ እየፈረሰች ተሠርታለች።

## ኢየሩሳሌም ሰማያዊት፤

ኢየሩሳሌም የእግዚአብሔር ሕዝብ ከተማ ይልቁንም የታላቁ ንጉሥ የእግዚአብሔር ከተማ በመሆንዋ ሐዋርያት የእግዚአብሔርን መንግሥት ሁኔታ በኢየሩሳሌም ምሳሌነት ገልጠዋል፤ አሁንም ምእመናን ወደ ሳይኛይቱ ኢየሩሳሌም በእምነት ደርሰዋል፤ ማቴ. 5፥35፤ ገላ. 4፥25:26፤ ዕብ. 12፥22፤ ራእ. 3፥12፤ 21፥1-14።

**ኢየሱስ፤** ኢየሱስ ከዕብራይስጥ የተወረሰ የግሪክ ቃል ነው፥ ትርጕሙም አዳኝ ማለት ነው፤ ማቴ. 1፥21።

1. የኢየሱስ ስሞች። ክርስቶስ፤ በግሪክ ቋንቋ የተቀባ ማለት ነው፥ መሢሕ የሚለውን የዕብራይስጥ ቃል ይተረጕማል። ኢየሱስ በምድር ሳለ ክርስቶስ መሆኑን ለማንም እንዳይናገሩ ሰዎችን ከለከለ (ማቴ. 16፥20)፥ ምክንያቱም ሕዝቡ ምድራዊ መሪ ይፈልጉ ነበርና፥ የኢየሱስም መንግሥት ከዚህ ዓለም አልነበረም፤ «መሢሕ» ይመ.። ጌታ፤ ከሁሉ በላይ፥ አማኙ፥ ገዥ፥ ኀላፊ መሆኑን ያሳያል። ኢየሱስ የሰው ልጅ ብሎ ስለ ራሱ ተናገረ። በዚህ ስም መሠረት ሰው መሆኑን እናስተውላለን፤ ይህ ስም ብ.ኪ.ን ለሚያውቁ ኢየሱስ ለልዩ አገልግሎት በፈቃዱ ከእግዚአብሔር እንደተላከ ይገልጣል፤ ዳን. 7፥13:14፤ ሉቃ. 9፥26:27፤ 21፥27። የዳዊት ልጅ፤ ለዳዊት የተሰጠው ተስፋ በኢየሱስ

እንደሚፈጸም ያሳያል፤ (ማቴ. 21፥9፤ «ዳዊት» ይመ.። <u>የእግዚአብሔር ልጅ</u>፤ ከመጀመሪያ ጀምሮ ከእግዚአብሔር ጋር የነበረ መሆኑን፥ አምላክነቱንም ያሳያል፤ ማቴ. 11፥27፤ 24፥36፤ 27፥43። ዮሐንስ <u>ቃል</u> ብሎ ይጠራዋል። ይህ ስም ከዘለዓለም፥ አካላዊ፥ እግዚአብሔር፥ ፈጣሪ ሕይወትን ሰጭ፥ እውነትን ገላጭ፥ አስቀድሞ ሥጋ ያልነበረ በኋላ ግን ሥጋ እንደሆነ ይገልጣል፤ ዮሐ. 1፥1-4፡14፤ ራእ. 19፥13፤ «ቃል» ይመ.። <u>አማኑኤል</u>፤ «እግዚአብሔር ከእኛ ጋር» ማለት ነው፤ ኢሳ. 7፥14፤ 8፥8፤ ማቴ. 1፥23።

2. የኢየሱስ አካልና ባሕርይ። በእግዚአብሔር ዘንድ ሦስትነት አለ፥ ይህም ሦስት አካላት አሉ ማለት ነው፥ እነርሱም አብ፥ ወልድ፥ መንፈስ ቅዱስ ናቸው፤ «ሥላሴ» ይመ.። ከዘለዓለም የነበረ ከሦስቱ አካላት አንዱ ወልድ ሥጋንና ነፍስን ነሥቶ ሰው ሆነ፤ ሰውም በሆነ ጊዜ አምላክነቱ (መለኮት) እና ሰውነቱ በአንድ አካል ጸንተው ይኖራሉ። ስለዚህ ይህን አስመልክቶ በአብ.ክ. ብዙ ትምህርት አለ፥ ዋና ዋናዎቹ የሚከተሉት ናቸው።

(ሀ) <u>የኢየሱስ አምላክነት</u>።

ኢየሱስ ከፍጥረት ሁሉ በላይ፥ ከእግዚአብሔር በታች ሳይሆን እርሱ ራሱ ሕያው እግዚአብሔር ነው። ለእግዚአብሔር የሆነ መለኮታዊ ክብር ሁሉ ለእርሱም አለው፥ አንዳችም አይጐድለውም። መ.ቅ. ይህን ከሚያረጋግጥባቸው መንገዶች ዋና ዋናዎቹ የሚከተሉት ናቸው ፦ (1) ስለ እግዚአብሔር (በዕብራይስጥ ያህዌ) የተነገሩት ትንቢቶች በኢየሱስ ተፈጽመዋል፤ ኢዩ. 2፥32 እና ሐ.ሥ. 2፥21-22፡38፤ ሮም 10፥9-13፤ ኢሳ. 40፥3 እና ማር. 1፥1-3 ያነጻጽሩ። (2) ኢየሱስ ለእግዚአብሔር ብቻ የሚሰጠውን ክብር ተቀበለ፤ ማቴ. 16፥16፤ ዮሐ. 20፥28። (3) ኢየሱስ «አባቴ» ብሎ እግዚአብሔርን በመጥራት ራሱን ከእግዚአብሔር ጋር አስተካከለ፤ ዮሐ. 5፥17፡18፤ 10፥33። (4) እግዚአብሔር በቍጥቋጦው ውስጥ ለሙሴ «እኔ ... ነኝ» እንዳለ ሁሉ፥ ኢየሱስም ለአይሁድ «እኔ አለሁ» ብሏል፤ ዮሐ. 8፥58ን ከዘጸ. 3፥6 ጋር ያስተያዩ። በዚህም መሠረት ተከሰሰ፤ የሞት ፍርድም ተፈረደበት፤ ማቴ. 26፥64-66። (5) ሐዋርያት ኢየሱስን እግዚአብሔር ብለው ጠሩት፤ ዮሐ. 1፥1-4፤ ሐ.ሥ. 20፥28፤ ሮም 9፥5፤ ቲቶ 2፥13፤ 2ጴጥ. 1፥1፤ ዕብ. 1፥8። ሲያስተምሩም ኢየሱስ የእግዚአብሔር ብቸኛ የባሕርይ ልጁ መሆኑን አስረዱ፤ ዮሐ. 3፥16፤ 1ዮሐ. 4፥9። (6) ኢየሱስ በእግዚአብሔር የሚሠሩትን ሥራዎች ሁሉ ሠራ፤ ማቴ. 28፥18-20፤ ዮሐ. 5፥21፤ ፊል. 3፥21፤ ቆላ. 2፥9፤ ራእ. 1፥8።

(ለ) <u>የኢየሱስ ሰውነት</u> (ትስብእት)።

ኢየሱስ ተወለደ፤ አደገ፤ በላ፤ ጠጣ፤ ተናገረ፤ ደከመ፤ አንቀላፋ፤ ሐሤት አደረገ (ሉቃ. 10፥21)፤ አዘነ፥ ተቈጣ (ማር. 3፥5)፤ ሞተ፤ ተቀበረም። ታሪኩ የሰውነት ታሪክ ነው። ኃጢአትን ከመሥራት በቀር እንደ ሰው ኖረ። ኢየሱስ ራሱ ሰው መሆኑን ተናገረ፥ ከትንሣኤውም በኋላ ምግብ በመብላት አረጋገጠ፤ ሉቃ. 24፥38-43፤ ዮሐ. 8፥40። ሐዋርያት ኢየሱስ እንደ አዳም ሰው መሆኑን (ሮም 5፥15፤ 1ቆሮ. 15፥45)፥ በሥጋና በደም መካፈሉን አስተማሩ፤ ዕብ. 2፥14። ሰው ሆኖ ኃጢአታችንን ተሸከመ (1ጴጥ. 2፥24)፤ ምሳሌ ሆነልን (ፊል. 2፥5-8)፤ ይራራልናልም፤ ዕብ. 4፥15።

(ሐ) <u>የኢየሱስ አንድነት</u>።

ኢየሱስ ፍጹም አምላክ፥ ፍጹም ሰው ቢሆንም አንድ ክርስቶስ እንጂ ሁለት አይደለም። ቅድመ ዓለም (ከዘለዓለም) የነበረ ወልድ (ቃል) ሥጋንና ነፍስን ነሥቶ ሰው ሆነ። ዮሐንስ «ሆነ» እንጂ ተለወጠ አይልም፤ ዮሐ. 1፥14። እግዚአብሔርነቱ እንደ በፊቱ ነው። ግን በምድር ላይ ሰው ሆኖ በትሕትና ኖረ፤ ዮሐ. 17፥5፤ ፊል. 2፥7። ዮሐንስ «ሥጋ ሆነ» ሲል በጠቅላላ የሰውን ባሕርይ ነሣ እንጂ አስቀድሞ በነበረ በአንድ ሌላ ሰው ላይ አደረ ማለቱ አይደለም፤ ሥጋም የሆነው በማኅፀን ውስጥ ነው፤ ሉቃ. 1፥35፤ 2፥49፤ ማቴ. 2፥11፤ ገላ. 4፥4።

3. የኢየሱስ ታሪክ።

(ሀ) <u>ቀዳማዊነቱና መወለዱ</u>።

ኢየሱስ ከአብርሃም በፊት እንደነበረ ራሱ ገለጠ፤ ዮሐ. 8፥58። ከዚህም ጋር በሚክ. 5፥2 እና በዮሐ. 1፥1-4 ቀዳማዊነቱ ተገልጧል። ጊዜው ሲደርስ ሄሮድስ በይሁዳ ንጉሥ ሳለ («ዓመት» ይመ.) ኢየሱስ እንደ ገብርኤል ቃል ከቅድስት ድንግል ማርያም በቤተ ልሔም ተወለደ። ሲወለድ እረኞች ጐበኙት፤ ማቴ. 1፥18-25፤ ሉቃ. 1፥26-38፤ 2፥1-20።

(ለ) <u>ከሕግ በታች መኖሩና አድገቱ</u>።

ኢየሱስ በስምንተኛው ቀን ተገረዘ፤ በአርባኛው ቀን ወደ ቤተ መቅደስ ተወሰደ፤ እዚያም ስምዖን አቀፈው፤ ሐናም አየችው፤ ሉቃ. 2፥21-38። ሰብአ ሰገል ጐበኙት። በሄሮድስ ምክንያትም ኢየሱስ በመጀመሪያ ወደ ግብጽ፥ በኋላም ወደ ናዝሬት ተወሰደ፤ ማቴ. 2፥1-23። በናዝሬት ከሕግ በታች እየኖረ በእግዚአብሔርና በሰው ፊት በጥበብና በቁመት አደገ። የዐሥራ ሁለት ዓመት ልጅ ሲሆን ለፋሲካ በዓል ወደ ኢየሩሳሌም ወጣ፤ ሉቃ. 2፥39-52፤ ገላ. 4፥4። ከዚህም በኋላ እንደ ዮሴፍ አንጢት ጠራቢ ሆነ፤ በናዝሬትም ከእናቱ፥ ወንድሞቹና እኅቶቹ ከተባሉት ጋር ኖረ፤ ማቴ. 13፥54-55፤ ማር. 6፥3። ኢየሱስ ከተጠመቀ በኋላ ዮሴፍ በወንጌል ታሪክ ባለመጠቀሱ ቀደም ብሎ ሳይሞት አልቀረም።

(ሐ) <u>መጠመቁና መፈተኑ</u>።

መጥምቁ ዮሐንስ ለኢየሱስ መገለጥ ብዙ ሰዎችን ካዘጋጀ በኋላ ኢየሱስ ራሱ ተጠመቀ። ይህን ያደረገው ስለግዳን ሥራ ጽድቅን ሁሉ ለመፈጸምና ለሕዝቡ አርአያ መሆኑን ለማሳየት ነው እንጂ ከኃጢአት ራሱን ለማንጻት አይደለም። በዚህ ጊዜ አብ መሰከረለት፤ መንፈስ ቅዱስም በርግብ መልክ ወርዶ በእርሱ ላይ

ዐረፈ፤ ማቴ. 3፥13-17፤ ሉቃ. 3፥21-23፤ «ጥምቀት» ይመ.። ወዲያው በመንፈስ ቅዱስ ተመርቶ ወደ ምድረ በዳ ሄደ፥ በዚያም 40 ቀን ጾመ፥ በሰይጣንም ተፈተነ። ከቅዱሳት መጻሕፍት እየጠቀሰ ሰይጣንን በማሸነፉ ሰዎችን ከሰይጣን ኃይል አወጣ፤ ማቴ. 4፥11፤ 12፥29፤ ዕብ. 4፥15። «ፈተና» ይመ.

(መ) <u>ማስተማሩና ተአምራት ማድረጉ</u>።

ኢየሱስ ሦስት ዓመታት ያህል ሰበከ፤ «የአዲስ ኪዳን ስፍረ ዘመን»፥ «ወንጌል» ይመ.። ኢየሱስ በተለይ በገሊላ ሠራ፥ ሆኖም እንደ አይሁድ ሕግ በዓመት በዓላት ወደ ኢየሩሳሌም ሲመጣ ሥራውን ቀጠለ። የመጀመሪያው ምልክት ውሃን ወደ ወይን መለወጥ ነበረ፥ ከዚያም በኋላ እንጀራን በማበርከት፥ በውሃ ላይ በመራመድ፥ ነፋስን ጸጥ በማድረግ ሥልጣኑን አሳየ። ከብዙ ሰዎች አጋንንትን አወጣ። ሰዎችን ከብዙ ዓይነት ደዌና በሽታ ፈወሰ፤ ሦስት ሰዎችንም ከሞት አስነሣ። ከተአምራቱ ከሠላሳ በላይ የሚሆኑት ተዘርዝረዋል፥ ያልተተረኩትንም ብዙ ሌሎች ተአምራትን አደረገ፤ ማር. 1፥34፤ ዮሐ. 20፥30፤ 21፥25። «ተአምር»፥ «የኢየሱስ ተአምራት»፥ «ፈውስ» ይመ.

ኢየሱስ በተራራ ላይ፥ በመንገድ ሳለ፥ በባሕር ዳር፥ በሰው ቤት፥ በቤተ መቅደስና በምኵራብ አስተማረ። ትምህርቱ በሥልጣን ነበረና፥ ሕዝቡ ለረጅም ጊዜ ያዳምጥ ነበር። ትምህርቱም በብዙ ምሳሌ የተብራራ፥ በብዙ ዓይነት አቀራረብም የተሰጠ ነበር፤ «ምሳሌ»፥ «የኢየሱስ ምሳሌዎች»፥ «የእግዚአብሔር መንግሥት» ይመ.።

በሚያስተምርበት ጊዜ ደቀ መዛሙርትን አስከተለ፥ ከእነርሱም ዐሥራ ሁለቱን መረጠ። ሥልጣን ሰጣቸው፤ እንዲፈውሱና እንዲሰብኩም ላካቸው፤ «ሐዋርያ» ይመ.። ወደ መጨረሻም ሰባ ሰዎችን ላከ፤ ሉቃ. 10፥1-20። ሌሎችም ተከተሉት። በገንዘባቸው የሚያገለግሉት ሴቶችም ነበሩ፤ ሉቃ. 8፥1-3።

እስከ ሁለት ዓመት ድረስ የኢየሱስ ተከታዮች እየበዙ ሄዱ። በአንድ ጊዜ አምስት ሺህ ተከተሉት። ሊያነግሡትም ፈልገው ነበር። ኢየሱስ ግን አሳባቸውን አልተቀበለም። ከዚያ ጊዜ ጀምሮ ተከታዮች እያነሱ ሄዱ። ብዙዎችም ትምህርቱን ባለመቀበላቸው ተዉት፤ ዮሐ. 6፥10-14:60:66። ከመጀመሪያ ጀምሮ ባህላቸውንና ወጋቸውን ስላልጠበቀ ፈሪሳውያን ተቃወሙት፤ ማር. 3፥6። በመጨረሻም ፈሪሳውያንና ሰዱቃውያን ስለ አገራቸው ፈርተው ሊያጠፉት ወሰኑ፤ ዮሐ. 11፥48-50።

(ሠ) <u>የመጨረሻው ሳምንትና መያዙ</u>።

ኢየሱስ ለፋሲካ በዓል ሲመጣ በአህያ ተቀምጦ በብዙ ሕዝብ እየታጀበ ወደ ኢየሩሳሌም ገባ። በቤተ መቅደስ ውስጥ የሚነግዱትን አባረረ፤ ማቴ. 21፥1-13። በየቀኑ በቤተ መቅደስ አስተማረ፥ ሐዋርያትንም ለብቻቸው አስተማረ፤ ማቴ. 21፥14-25፥46። ሐሙስ ዕለት ማታ ከሐዋርያት ጋር ፋሲካን በላ። ከእራት በፊት እግሮቻቸውን አጠበ (ዮሐ. 13)፤ ከእራት በኋላም የቅዱስ ቍርባንን ሥርዓት ፈጸመ፤ ማቴ. 26፥26-29፤ «ቅዱስ ቍርባን» ይመ.። ቀጥሎም ከእነርሱ ተለይቶ የሚሄድ ስለመሆኑና መንፈስ ቅዱስን ስለመስጠቱ አስተማረ፤ ጸለየም፤ ዮሐ. 14-17። ከእራት ተነሥቶ ከሐዋርያት ጋር ወደ ጌቴሴማኒ ሄደ፥ በዚያም ጸለየ፤ ማቴ. 26፥36-46። የአስቆሮቱ ይሁዳ ሰዎችን አስከትሎ አስያዘው። ኢየሱስ ወደ ሊቀ ካህናቱ ግቢ ተወሰደ። በዚያም ሊቀ ካህናቱና የኢየሩሳሌም ሸንጎ በችኰላ የሞት ፍርድ ፈረዱበት፤ ማቴ. 26፥47-68።

ዐርብ ጥዋት ካህናት ኢየሱስን ለጲላጦስ አሳልፈው ሰጡት። እርሱ ኢየሱስን ለመፍታት ፈለገ። ነገር ግን ሁከትን ስለፈራ ለሞት አሳልፎ ሰጠው፤ ማቴ. 27፥15-26፤ ሉቃ. 23፥1-25፤ ዮሐ. 18፥28-19፥ 16።

(ረ) <u>መሞቱ</u>።

ኢየሱስ እንደ ሮማውያን ሥርዓት ተገረፈ። መስቀሉን ተሸክሞ ወደ ቀራንዮ ሄደ። ስምዖን መስቀሉን እንዲሸከምለት ተገደደ። ኢየሱስ በሁለት ወንበዴዎች መካከል ተሰቀለ። የሥቃይ ማደንዘዣ ሆምጣጤ ባቀረቡለት ጊዜ አልጠጣም። «የአይሁድ ንጉሥ የናዝሬቱ ኢየሱስ» የሚል ጽሕፈት በመስቀሉ ላይ ተለጠፈ።

ጭፍሮች የኢየሱስን ልብስ ወሰዱ፥ በእጀ ጠባቡም ዕጣ ተጣጣሉበት። መንገድ አላፊዎች፥ ካህናት ከእርሱም ጋር የተሰቀሉት ሰደቡት። እናቱና ሌሎችም ሰዎች ከመስቀሉ አጠገብ ቆመው ይመለከቱ ነበር። ኢየሱስ በመስቀል ላይ ሳለ ሰባት ቃላትን ተናገረ። ኢየሱስ በሦስት ሰዓት ተሰቀለ፥ ከስድስት እስከ ዘጠኝ ሰዓት ድረስ ከባድ ጨለማ ነበረ። በዘጠኝ ሰዓት ነፍሱን ሰጠ። የቤተ መቅደስ መጋረጃ ተቀደደ፤ ማቴ. 27፥27-51፤ ማር. 15፥21-39፤ ሉቃ. 23፥26-45፤ ዮሐ. 19፥17-30። «ስቅለት» ይመ.።

(ሰ) <u>መቀበሩ</u>።

የአርማትያስ ሰው፥ ዮሴፍና ኒቆዲሞስ ኢየሱስን ቀበሩት፤ ማቴ. 27፥57-61፤ ማር. 15፥42-46፤ ሉቃ. 23፥50-56፤ ዮሐ. 19፥38-42።

(ቀ) <u>ትንሣኤውና ዕርገቱ</u>።

ኢየሱስ አስቀድሞ እንደተናገረ በሦስተኛው ቀን ተነሣ። አርባ ቀን ለደቀ መዛሙርቱ እየታየ አስተማረ፤ «ትንሣኤ» ይመ.። በዚህ ጊዜ የብ.ኪ.ን መጻሕፍት እየተረጐመላቸው በሥጋ እንደተነሣ አረጋገጠ፤ ሥልጣንን ሁሉ እንደተቀበለና መንፈስ ቅዱስን እንደሚልክላቸው ነገራቸው። በዚህ መሠረት ወንጌልን በዓለም ሁሉ እንዲሰብኩ አዘዛቸው። ይህንም ፈጽሞ እጆቹን ዘርግቶ ባረካቸው፥ ወደ ሰማይ ከፍ ከፍ አለ፥ ደመናም ከዓይናቸው ሰውራ ተቀበለችው፤ ማቴ. 28፥18-20፤ ሉቃ. 24፥25-53፤ ሐ.ሥ. 1፥1-11። «ዕርገት» ይመ.።

(በ) <u>በእግዚአብሔር ቀኝ መቀመጡ</u>።

ኢየሱስ ፍጹም አምላክ ፍጹም ሰው ሆኖ ወደ ሰማይ ዐረገ። በክብርና በሥልጣን በአባቱ ቀኝ ተቀመጠ። ከዚያም ተስፋውን ለሚጠብቁ የመንፈስ ቅዱስን የተስፋ ቃል ከአብ ተቀብሎ በበዓለ ኀምሳ ቀን ሰጠ፤ ሐ.ሥ. 2፥32:33። አሁንም ዓለምን ይገዛል፥ የቤ.ክ. ራስ ነውና ለምእመናን አስፈላጊውን ሁሉ ያደርግላቸዋል፥ እስከ መጨረሻም ያድናቸዋል፤ ኤፌ. 1፥19-23፤ ዕብ. 7፥23-25፤ 1ዮሐ. 2፥1።

(ተ) መመለሱ።

በዓለም ፍጻሜ ኢየሱስ በክብር ይመለሳል፤ ሙታንን ያስነሣል፤ በሰዎች እንደ ሥራቸው ይፈርዳል፤ ሰይጣንንና ተከታዮቹን በእሳት ባሕር ይጥላል፤ ምእመናንን ይቀበላል፤ 1ቆሮ. 15፥23-28፤ «ሺህ ዓመት»፥ «ፍርድ»፥ «ዳግም ምጽአት» ይመ.

4. የኢየሱስ ሥራ። ኢየሱስ ሰው እንዲድን አስፈላጊ የሆነውን ሥራ ሁሉ ሠርቷል። በብ.ኪ. ዘመን እግዚአብሔር እስራኤልን በሦስት ዓይነት ሰዎች ያስተዳድር ነበር፥ እነርሱም ነቢያት፥ ካህናት፥ ነገሥታትም ናቸው። ኢየሱስ ሦስት ዓይነት ሥራ በአንድነት ይዞ የአ.ኪ. መካከለኛ ሆነ፤ «መካከለኛ» ይመ.። የኢየሱስ ሥራ በብዙ ዓይነት መንገድ ተገልጧል (ለምሳሌ እረኛ)፥ ግን እነዚህ ሦስት ዓይነት ሹመቶች የኢየሱስን ሥራ ያጠቃልላሉና ሥራውን በእነርሱ መሠረት ማጥናት ይቻላል።

(ሀ) ኢየሱስ ነቢይ ነው።

ሙሴ ስለሚመጣው ነቢይ የተናገረውን ኢየሱስ ፈጸመ፤ ዘዳ. 18፥15-19፤ ሐ.ሥ. 3፥22። ኢየሱስ ነቢይ ሆኖ መልእክቶችን ከአብ አቀረበ (ዮሐ. 8፥26-28)፥ የሚመጣውን ገለጠ (ሉቃ. 19፥41-44)፥ የእግዚአብሔርን ሕግ ተረጐመ (ማቴ. 5፥21-48)፥ ሰዎችን ስለ ኃጢአታቸው ወቀሰ (ሉቃ. 11፥42-46)፥ ስለ እምነታቸውም አበረታቸው (ማቴ. 8፥10-13)። አሁንም በእርሱ ፈንታ በላከው «ሌላ አጽናኝ» በተባለው በመንፈስ ቅዱስ ሥራውን ይፈጽማል፤ ዮሐ. 14፥26፤ 15፥26፤ 16፥7-13።

(ለ) ኢየሱስ ካህን ነው።

ኢየሱስ ከአሮን ወገን ያይደለ፥ እንደ መልከ ጼዴቅ ያለ ካህን እንደሚነሣ የተነገረውን ትንቢት ፈጸመ፤ መዝ. 110፥4፤ ዕብ. 5፥5:6፤ «መልከ ጼዴቅ» ይመ.። ካህን በተለይ ሁለት ነገሮችን ይሠራል።

1ኛ. መሥዋዕትን ያቀርባል፥ ኢየሱስም ራሱን የተወደደ መሥዋዕት አድርጎ አቀረበ። ይህንም በማድረጉ ስለ ኃጢአት ይደረግ የነበረውን የብ.ኪ.ን ሥን ሥርዐት ፈጸመ። ለሚያምኑበትም የመዳን መንገድን ከፈተ። በዚህ ምክንያት «የእግዚአብሔር በግ» ተብሏል፤ ዮሐ. 1፥29። የኢየሱስ ሞት ፦ ቤዛ፥ ማስተስረያ፥ መሥዋዕት ነው (በየርእሱ ይመ.)። በኢየሱስ ሞት የእግዚአብሔር ጽድቅና ፍቅር ተገልጧል፤ ሮም 3፥26፤ 5፥8። በአጠቃላይ አነጋገር ኢየሱስ በኃጢአተኞች ፈንታ ሞተ፤ በሞቱም ኃጢአታቸው ይደመሰሳል፤ ኢሳ. 53፥5:6፤ ማር. 10፥45፤ ሮም 5፥15፤ 1ጴጥ. 2፥24፤ 3፥18፤ ራእ. 1፥4:5።

2ኛ. ካህን ለሕዝቡ ይጸልያል፤ በእግዚአብሔርም ፊት ይገኝላቸዋል። ኢየሱስም በምድር ሳለ ለተከታዮቹ ማለደ (ሉቃ. 22፥32፤ ዮሐ. 17፥6-26)፥ አሁንም አዳኝ ሆኖ በእግዚአብሔር ቀኝ ለእነርሱ ይገኛል፤ ሮም 8፥34፤ ዕብ. 7፥23-25፤ 1ዮሐ. 2፥1:2፤ «ካህን»፥ «ሊቀ ካህናት» ይመ.።

(ሐ) ኢየሱስ ንጉሥ ነው።

ኢየሱስ ከዳዊት ቤት ለዘለዓለም ንጉሥ እንደማይጠፋ የተሰጠውን ተስፋ ፈጸመ፤ 2ሳሙ. 7፥12-16፤ ራእ. 22፥16። ኢየሱስ በሰማይና በምድር ሥልጣን አለው፤ የቤተ ክርስቲያንም ራስ ነው። መንግሥቱ ምድራዊ ሳይሆን ሰማያዊ ነው። በዓለምም ፍጻሜ መንግሥቱ ይገለጣል፤ በሰዎች ይፈርዳል፤ ለመንግሥቱም ፍጻሜ የለውም፤ ማቴ. 28፥18፤ ሉቃ. 1፥33፤ ዮሐ. 18፥36፤ ራእ. 20፥11-15።

**ኢዩ፤** 11ኛ የእስራኤል ንጉሥ የሆነው የእስራኤል ጦር ሠራዊት አለቃ። ኤልሳዕ፥ አስቀድሞ ለኤልያስ የተናገረውን የእግዚአብሔርን ቃል በመፈጸም፥ በመልእክተኛ እጅ ኢዩን ለንጉሥነት ቀባው። ሌሎችም የጦር ሠራዊት አለቆች ኢዩን ደገፉ። ከእነርሱም ጋር ወደ ኢይዝራኤል ተከታትሎ በመሄድ የአክዓብን ልጅ ንጉሥ ኢዮራምን፥ የልጅ ልጁ የሆነውንም የይሁዳን ንጉሥ አካዝያስን ገደለ። የአክዓብንም ሚስት ኤልዛቤልን አስገደለ። 70 የአክዓብን ልጆች፥ አለቆቹን እንዲሁም ከአካዝያስ ወንድሞች ብዙዎችን ፈጀ። በአልን የሚያመልኩትን በተንኰል ሰብስቦ አጠፋቸው። ነገር ግን ኢዮርብዓም ከደነገገው አምልኮ ባዕድ ኢዩ አልራቀም። እግዚአብሔርም፥ በአክዓብ ቤተሰብ ላይ የፍርድ ቃሉን ስለ ፈጸመ፥ «ልጆችህ እስከ አራት ትውልድ ድረስ ይነግሣሉ» አለው። ነገር ግን በፍጹም ልቡ ለእግዚአብሔር አልታዘዘምና የሶርያ ንጉሥ ከዮርዳኖስ በስተምሥራቅ የእስራኤልን ምድር መታ፤ 2ነገ. 9፥10፤ 1ነገ. 19፥15-17። ኢዩ በአክዓብ ላይ የተነገረውን የፍርድ ቃል በመፈጸም ከሚገባ በላይ ደም እንዳፈሰሰ በሆሴዕ 1፥4 ይታያል። ከ842-815 ከክ.ል. ነገሠ። ሥዕሉን በገጽ 168 ይመ.

**ኢዩኤል፤** ትርጉሙ «እግዚአብሔር አምላክ ነው» ማለት ነው። አባቱ ባቱኤል የሚባል እስራኤላዊ ነቢይ ነበረ።

**የኢዩኤል ትንቢት፤** ኢዩኤል የተናገረውን ትንቢት የያዘ መጽሐፍ። የተጻፈበትን ዘመን ለማረጋገጥ አልተቻለም፤ ኢዩኤል ትንቢት የተናገረው ከአሞጽ በፊት ነው የሚሉ ሊቃውንት አሉ፤ ከሚልክያስ በኋላ ትንቢት የተናገረ የመጨረሻ ነቢይ ነበረ የሚሉም አሉ፤ ትንቢቱን የተናገረው በኢየሩሳሌም ይመስላል፤ 2፥15:23። ጊዜው አስፈሪ የአንበጣ መቅሠፍት የመጣበት ወቅት ነው (1፥1-2፥27)፥ አንበጣዎችን «ሠራዊቱ» አድርጎ



ከአ.ዩ የተሳኩ እስራኤላውያን ለግልሣዊ ስልምናሶር ግብር ሲያቀርቡ፥ 841 ዓመታት ከክ.በ. ከተቀረጸ ሐውልት የተገኘ

በእስራኤል ላይ ይህን «ታላቅና ብርቱ ሕዝብ» የመራ እግዚአብሔር ነው ይላል፤ 2፥2:11። የዓለም ሕዝቦች ሁሉ ፍርድ ስለሚቀበሉበት «የእግዚአብሔር ቀን» ተብሎ ስለሚጠራው ስለ ታላቁ የፍርድ ቀን ይናገራል፤ 3፥14። ከኢዩኤል ትንቢት በጣም የታወቀው ክፍል እግዚአብሔር በሥጋ ለባሽ ሁሉ ላይ መንፈሱን ለማፍሰስ ተስፋ የሰጠበት ነው፤ 2፥28-32፤ ሐ.ሥ. 2፥16-21። የትንቢቱም ዋና ጥሪ «በፍጹም ልብ ወደ እግዚአብሔር ተመለሱ» የሚል ነው፤ 2፥13።

አከፋፈል ፦

1. የአንበጣ መቅሠፍት፤ 1፥1-12።

2. ንስሓ ለሚገቡ የእግዚአብሔር በረከት፤ 1፥13-2፥27።

3. የእግዚአብሔር መንፈስ መፍሰስ፤ 2፥28-32።

4. የዓለም ሕዝቦች ፍርድ፤ 3፥1-15።

5. የእግዚአብሔር ሕዝብ ብፅዕና፤ 3፥16-21።

**ኢያሪኮ፤** ከጨው ባሕር በስተሰሜን 15፥ ከኢየሩሳሌም በስተምሥራቅ 25 ኪ.ሜ. ርቆ የሚገኝ ከተማ። ሦስት ከተማዎች ኢያሪኮ ተብለዋል፤ እነርሱም በብ.ኪ. ዘመን የነበረ ከተማ፥ በክርስቶስ ዘመን የነበረ ከተማና አሁንም ያለው ከተማ ናቸው። ሦስቱም በታዎች ይቀራረባሉ። ይህም ከተማው ፈርሶ በሌላ ቦታ ሲቆረቆር በቀደመ ስሙ ተጠርቷል ማለት ነው። ኢያሪኮ ማለት የጨረቃ ከተማ ማለት ነው። በኢያሪኮ የኖሩ የጥንት ሰዎች ጨረቃን ሲያመልኩ ኖረዋል። ኢያሪኮ 250 ሜትር ከባሕሩ ጠለል ዝቅ ስለሚል፥ ከዓለም ከተሞች ሁሉ ዝቅተኛ ነው። በዙሪያው ብዙ ምንጮች ስላሉ 7000 ከክ.በ. ጀምሮ ሰዎች በኢያሪኮ መኖር ጀምረዋል፤ ዘዳ. 34፥3። ኢያሱ የፊተኛውን ከተማ አፈረሰ (ኢያሱ 6)፤ አኪኤል እንደገና ሠራው፤ 1ነገ. 16፥34። ሄሮድስ በኢያሪኮ ሞተ። ክርስቶስ በምድር ሳለ ብዙ ካህናት በኢያሪኮ ነበሩ፤ ሉቃ. 10፥30:31። ኢየሱስ በኢያሪኮ የበርጤሜዎስን ዓይን አበራ (ማር. 10፥46-52)፥ በዘኬዎስም ቤት ዋለ፤ ሉቃ. 19፥1-10። ሮማውያን ኢያሪኮን በ67 ዓ.ም. አፈረሱ። ካ. 2ለ።

**ኢያሱ፤** ትርጉሙ «እግዚአብሔር አዳኝ» ማለት ነው።

1. የነዌ ልጅ ኢያሱ ከሙሴ በኋላ የእስራኤል መሪ ሆኖ በራሱ መጽሐፍ እንደተጻፈው ሕዝቡን ወደ ከነዓን አሻግሮ ምድሩን አወረሳቸው። አያቱ ኤሊሳማ የኤፍሬም ነገድ አለቃ ነበረ፤ 1ዜ.መ. 7፥26:27፤ ዘኍ. 1፥4-10። ብላቴና ሆኖ ከግብጽ ወጣ፤ ሙሴም ከአማሌቅ ጋር እንዲዋጋ አዘዘው፤ አሸነፈም፤ ዘጸ. 17፥8-13። የሙሴ ሎሌ ሆነ፤ ዘጸ. 24፥13፤ 32፥17፤ 33፥11፤ ዘኍ. 11፥28። ከነዓንን ሊሰልሉ ከቃዴስ ከወጡት 12 ሰላዮች መካከል አንዱ ነበረ። እርሱና ካሌብ በእምነት፥ እንውጣ ስላሉ ወደ ከነዓን እንደሚገቡ ተስፋ ተሰጣቸው፤ ዘኍ. 13ና 14። በ13፥8 ስሙ «አውሴ» ተባለ። ከሙሴ በኋላ መሪ እንዲሆን ተመረጠ፤ ዘኍ. 27፥15-23፤ ዘዳ. 3፥28፤ 31፥23።

እግዚአብሔርም ቃል በቃልና በራእይ አደፋፈረው፤ ኢያሱ 1፥1-9፤ 5፥13-15። የእስራኤል ሕዝብ በኢያሱ መሪነት ዮርዳኖስን ተሻግረው ኢያሪኮን ያዙ፥ ዋና ሰፈራቸው ጌልገላ ሆነ። ከዚያም እየዘመቱ የከነዓንን ነገሥታት አሸነፉ። እግዚአብሔር ቀኑን በማስረዘም፥ በረዶ በማዝነብ ረዳቸው፤ ኢያሱ 10፥11-14። አገሩን ከያዙ በኋላ ኢያሱ መሬቱን ለእስራኤል ነገዶች አከፋፈለ። የሞቱ ጊዜ ሲቀርብ ሕዝቡን ሰብስቦ እግዚአብሔር ስላደረገላቸው ሁሉ አሳሰባቸው። ከሕዝቡም ጋር ቃል ኪዳን ተጋብቶ ለመታሰቢያ ታላቅ ድንጋይ በሴኬም



በ1600 ገደማ ከክ.በ. በኢያሪኮ የነበረ የቤት ዕቃ

አቆመ፤ ኢያሱ 24፥25-28። ኢያሱ በ110 ዓመቱ ሞተ፤ በርስቱ በኤፍሬም አገር ተቀበረ፤ ኢያሱ 24፥29-31።

2. የኢዮሴዴቅ ልጅ ኢያሱ። ከባቢሎን ምርኮ የተመለሰው የእስራኤል ካህናት አለቃ 537 ከክ.በ. በኢየሩሳሌም ከዘሩባቤል ጋር የእግዚአብሔርን ቤት መሥራት ጀመረ፤ ዕዝ. 2፥1:2፤ 3፥2:8። ከሳምራውያን ተቃውሞ የተነሣ ሥራው 16 ዓመት ዘገየ፤ ዕዝ. 4። 520 ከክ.በ. ሐጌና ዘካርያስ የተባሉት ነቢያት ባበረታቱአቸው ጊዜ ኢያሱና ዘሩባቤል ሥራውን ፈጸሙ፤ ዕዝ. 5፥2፤ ሐጌ. 1፥1:12:14፤ 2፥2፤ ዘካ. 3፤ 6፥9-15።

**የኢያሱ መጽሐፍ፤** ይህ መጽሐፍ የእስራኤል ሕዝብ በእግዚአብሔር ኃይልና በኢያሱ መሪነት ከነዓንን እንደያዙ ይተርካል። ኢያሱ ራሱ የሙሴን መጽሐፍ አነበበ፤ የሙሴን ሕግ በድንጋይ ጻፈ፤ በሕይወቱ መጨረሻም ከሕዝቡ ጋር ያደረገውን ቃል ኪዳን በጽሑፍ አሰፈረ፤ ኢያሱ 1፥8፤ 8፥32፤ 24፥26። ጠቅላላው መጽሐፍ በዚያ ዘመን የተጻፈ ይመስላል።

አከፋፈል ፡-

1. የከነዓን ምድር መወረር፤ ም. 1-12።

ሀ. የእስራኤል ሕዝብ ዝግጅትና የርዳኖስን መሻገር፤ 1-4።

ለ. የኢያሪኮ መያዝና የአካን ኃጢአት፤ 5-7።

ሐ. የእስራኤል መዝመትና የከነዓን ነገሥታት መሸነፍ፤ 8-12።

2. የከነዓን ምድር አከፋፈል፤ 13-22።

3. የኢያሱ ስንብት፤ 23-24።

**ኢያስጲድ፤** ቀይ ወይም አረንጓዴ ቀለም ያለው የከበረ ድንጋይ፤ ዘጸ. 39፥13፤ ራእ. 4፥3፤ 21፥10:11።

**ኢያቡሳውያን (ኢያቡሴዎን)፤** ከከነዓን የተገኙ ወገን፤ ዘፍ. 10፥16። በኢየሩሳሌም ተራራዎች ይኖሩ ነበር። ኢያሱ ንጉሣቸውን ገደለ። ጽዮን የተባለው አንባቸው ግን ዳዊት እስኪይዘው ድረስ በእጃቸው ነበረ፤ ኢያሱ 10፥23-27፤ 15፥63፤ 2ሳሙ. 5፥7:8።

**ኢያቡስ፤** ኢያቡሳውያን ይኖሩበት የነበረ፤ የኢየሩሳሌም ስም ወይም በጽዮን የነበረ የአንባ ስም፤ ኢያሱ 15፥63፤ መሳ. 19፥10።

**ኢያቡስቴ፤** የንጉሥ ሳኦል ልጅ። ሳኦል ከሞተ በኋላ አበኔር የተባለው የጭፍራ አለቃ የንጉሡን ልጅ ኢያቡስቴን ወስዶ የእስራኤል ንጉሥ ይሆን ዘንድ አነገሠው፤ 2ሳሙ. 2፥8-10። ነገር ግን ዘመነ መንግሥቱ ሁለት ዓመት ያህል ብቻ ሆነ። በእርሱና በአበኔር መካከል አለመግባባት ስለተፈጠረ፥ አበኔር ኢያቡስቴን ከድቶ ከዳዊት ጋር ተባበረ፤ 2ሳሙ. 3። በመጨረሻም የዳዊት ጭፍራ አለቆች የሆኑ ሁለት ሰዎች ኢያቡስቴን ገደሉት፤ ራሱንም ቆርጠው ወደ ዳዊት ወሰዱት። ዳዊትም የኢያቡስቴን ራስ እንዲቀበር አደረገ፤ 2ሳሙ. 4፥1-12።

**ኢያኔስ ኢያንበሬስ**፤ ሙሴን የተቃወሙ ጠንቋዮች። ስማቸው በብ.ኪ. አይገኝም። በዘጸ. 7 እና 8 የተጠቀሱት ጠንቋዮች በእነዚህ ስሞች በአይሁድ መካከል ተጠርተዋል፤ 2ጢሞ. 3፥8።

**ኢያዔል**፤ የቄናዊው የሔቤር ሚስት። በድንኳን ካስማ ሲሣራን ገደለች፤ መሳ. 4፥17-24፤ 5፥24-27።

**ኢይዝራኤል**፤ ትርጉሙ «እግዚአብሔር ይዘራል» ማለት ነው። የሆሴዕ ታላቅ ልጅ ነው። እግዚአብሔር የኢዩን ነፍሰ ገዳይነት («የኢይዝራኤልን ደም») በዘሮቹ ላይ እንደሚበቀል የሚያመለክት ስም ነበር፤ ሆሴዕ 1፥4:5።

**ኢይዝራኤል**፤ 1. የይሁዳ ከተማ፤ ኢያሱ 15፥56፤ 1ሳሙ. 25፥43። 2. በይሳኮር ርስት ድርሻ ውስጥ ነበረ። በከተማውም አቅራቢያ ያለው ሰፊ ሸለቆ በዚህ ስም ተጠራ፤ ኢያሱ 19፥18፤ ሆሴዕ 1፥5። የናቡቴ ወይን ቦታ በዚያ ነበረ፤ 1ነገ. 20። በዚያም ኢዩ የአክዓብን ቤተ ሰዎችና አለቆች አስፈጀ፤ 2ነገ. 9፥17-10፥11። ካ. 4ሀ።

**ኢዮሣፍጥ**፤ ትርጉሙ «እግዚአብሔር ፈርዷል» ማለት ነው። ከ870-845 ከክ.በ. ከአባቱ ከአሳ በኋላ የነገሠ አራተኛው የይሁዳ ንጉሥ። እግዚአብሔርን የሚፈራ፥ የከበረም ነበር። አምልኮ ባዕድን አስወገደ፤ ሕዝቡ የእግዚአብሔርን ሕግ እንዲማሩና ዳኞችም በቅንነት እንዲፈርዱ አደረገ። እየተዘዋወሩ የእግዚአብሔርን ሕግ መጽሐፍ የሚያስተምሩ 16 ሌዋውያንን መደበ። ነገር ግን ክፉዎች የሆኑትን የሰማርያን ነገሥታት አክዓብንና ልጁን ስለረዳቸው በሁለት ነቢያት ተወቀሰ። ለልጁ ለኢዮራም የአክዓብን ልጅ በማጋባቱ ተሳሳተ። በጠላትነት በተነሡበት በሞዓብና በአሞን ሰዎች ላይ በእምነት ትልቅ ድል ነሣ፤ 2ዜ.መ. 17-20፤ 1ነገ. 22፤ 2ነገ. 3። በዚህ ስም አራት ሌሎች ሰዎች ተጠሩ፤ 2ሳሙ. 8፥16፤ 1ነገ. 4፥17፤ 2ነገ. 9፥2:14፤ 1ዜ.መ. 15፥24።

**የኢዮሣፍጥ ሸለቆ**፤ በኢየሩሳሌምና በደብረ ዘይት መካከል የቄድሮን ወንዝ የሚፈስበት ሸለቆ ነው። ኢዮሣፍጥ ጠላቶቹን ካሸነፈና ብዙ ምርኮ ከወሰደ በኋላ በዚህ ሸለቆ እግዚአብሔርን አመሰገነ፤ 2ዜ.መ. 20፥24-27። ኢዮሣፍጥ «እግዚአብሔር ፈርዷል» ማለት ነውና ኢዩኤል ትንሣኤና የመጨረሻ ፍርድ በዚህ ሸለቆ እንደሚሆን ገልጧል፤ ኢዩ. 3፥2:12። ዛሬ ብዙ የአይሁድና የእስላም መቃብር በዚህ ሸለቆ ይገኛል።

**ኢዮራም**፤ ትርጉሙ «እግዚአብሔር ከፍ ከፍ አለ» ማለት ነው። 1. ከአባቱ ከኢዮሣፍጥ በኋላ፥ ከ848 እስከ 841 ከክ.በ. የነገሠ አምስተኛው የይሁዳ ንጉሥ ነው። የአክዓብን ልጅ አግብቶ ነበርና እንደ አክዓብ ክፉ ሥራ ሠራ። ነቢዩ ኤልያስ ሊገሥጸው ጻፈለት። ደብዳቤውን መቼ እንደጻፈው ሁለት አስተያየቶች አሉ ፦ 1. ኤልያስ ካረገ በኋላ ነው፤ 2. ከማረጉ በፊት ነው ይላሉ። ብዙ ጠላቶችም ተነሡበት፤ በሚያሠቃይ በሽታ ታምሞ በሕዝቡ ሁሉ ተጠልቶ ሞተ፤ 2ዜ.መ. 21፤ 2ነገ. 8፥16-24።

2. ሁለተኛው የአክዓብ ልጅ። ወንድሙ አካዝያስ ከሞተ በኋላ፥ ከ852 እስከ 841 ከክ.በ. በሰማርያ በእስራኤል ላይ ነገሠ። የበኣልን ሐውልት አፈረሰ እንጂ ኢዮርብዓም ያቆመውን አምልኮ ባዕድ መከተል አላተወም። ከዚህም የተነሣ ኤልሳዕ ገሠጸው፤ 2ነገ. 3። የሶርያን ንጉሥ ሲዋጋ ቈሰለ። ኢዩም እስከ ኢይዝራኤል ድረስ አሳዶ ገደለው፤ 2ነገ. 8፥25-9፥26።

**ኢዮርብዓም**፤ ትርጉሙ «ሕዝቡ እየበዛ ይሄዳል» ማለት ነው። 1. የናባጥ ልጅ፤ ሰሎሞን ሹመትን የሰጠው ትጉህ ኤፍሬማዊ ነበረ። ነቢዩ አኪያ፥ በሥሩ ነገዶች ላይ ትነግሣለህ ካለው በኋላ ሰሎሞን እስኪሞት ድረስ በግብጽ ተቀመጠ። የሰሎሞን ልጅ ሮብዓም በነገሠ ጊዜ በእርሱ ላይ በማመፅ ዐሥሩን ነገዶች ይመራ ነበር። በዚህም ጊዜ እስራኤል በሁለት መንግሥታት ተከፈለ። ኢዮርብዓም የሰሜናዊው መንግሥት የመጀመሪያ ንጉሥ ሆኖ ከ931 እስከ 910 ከክ.በ. በሴኬም ነገሠ። እግዚአብሔርም፥ ለእኔ ብትታዘዝ መንግሥትህን አጸናለሁ አለው። እርሱ ግን፥ ሕዝቡ ወደ ሮብዓም ግዛት እንዳይመለሱና ወደ ኢየሩሳሌም እንዳይመላለሱ፥ በቤቴልና በዳን የወርቅ ጥጆዎችን አቁሞ፥ ወደ አምልኮ ባዕድ መራቸው። ከዚህም የተነሣ ታላቅ ልጁ ሞተ፤ አኪያም የመንግሥቱን ውድቀት ተነበየ። በልጁም ዘመን መንግሥት ጊዜ ለእርሱ የነበሩ ሁሉ ተገደሉ። ከእርሱ በኋላ የነገሡ የሰሜናዊ መንግሥት ነገሥታት ሁሉ፥ አንድ ሳይቀሩ በናባጥ ልጅ በኢዮርብዓም የኃጢአት መንገድ ሄዱ፤ 1ነገ. 11፥26-14፥20፤ 15፥29:30።

2. ኢዮርብዓም 2ኛ፤ በሰማርያ በእስራኤል ላይ አርባ አንድ ዓመት የነገሠ የዮአስ ልጅ የኢዩ የልጅ የልጅ ልጅ። በዮናስ ትንቢት መሠረት (2ነገ. 14፥25) ሶርያን ድል ነሥቶ የዱሮውን የእስራኤል ግዛት መለሰ፤ 2ነገ. 14፥23-29። በእርሱ ዘመን መንግሥት ዮናስ፥ አሞጽና ሆሴዕ ተነሡ። ኃያል ንጉሥ ቢሆንም፥ የናባጥ ልጅ ኢዮርብዓም ያቆመውን አምልኮ ባዕድ አላተወም፤ አሞጽ 2፥6-16፤ 5፥6-12። በአሞጽ 7፥9 የተጻፈው በኢዮርብዓም ልጅ ዘመን ተፈጸመ።

**ኢዮስያስ**፤ ትርጉሙ «እግዚአብሔር ይደግፋል» ማለት ነው። 16ኛው የይሁዳ ንጉሥ የንጉሥ አሞጽ ልጅ። የስምንት ዓመት ወጣት ከነበረበት ጊዜ ጀምሮ 31 ዓመት (ከ639-609 ከክ.በ.) ነገሠ። ከዳዊት ቤት ከነበሩት መልካም ነገሥታት የመጨረሻው ነበረ። ከይሁዳ ጀምሮ እስከ ገሊላ ድረስ አምልኮ ባዕድን አስወገደ። በ1ነገ. 13፥2 ያለውን ትንቢት ፈጸመ። በነገሠ በ18ኛው ዓመት የእግዚአብሔርን ቤት ሲያሳድስ፥ ጠፍቶ የነበረው የሕግ መጽሐፍ ተገኘ። ኢዮስያስም በዚህ መጽሐፍ መሠረት ሕዝቡን ሰብስቦ ለእግዚአብሔር ለመታዘዝ ቃል ኪዳን እንዲገቡ አደረገ። ፋሲካንም በታላቅ ክብር አስከበረ። በእርሱ ዘመን ኤርምያስ ነቢይ እንዲሆን ተጠራ፤ ኤርምያስም ስለ ኢዮስያስ ቅን ፍርድ መሰከረ፤ ኤር. 1፥2፤ 22፥15:16። የግብጹ ንጉሥ

ኒካው በአገሩ አልፎ ለሰልፍ በሄደ ጊዜ ኢዮስያስ ሊዋጋው ወጥቶ በውጊያው ወቅት ተገደለ። ትልቅ ልቅሶም ተደረገለት፤ 2ዜ.መ. 34ና 35፤ 2ነገ. 21፥24-23፥30።

**ኢዮቤልዩ፤** ቀንደ መለከት ማለት ነው። በእስራኤል ከሰባት ጊዜ ሰባት ዓመት በኋላ አምሳኛው ዓመት የተቀደሰ ነበረ፤ በቀንደ መለከትም ይታወጅ ነበር። በኢዮቤልዩ ከእስራኤል ወገን ለባሪያዎች ነፃነት ይሰጥ፥ ርስት የተያዘባቸው ሰዎች ርስታቸው ይመለስና መሬትም ለአንድ ዓመት አይታረስም ነበር፤ ዘሌ. 25።

**ኢዮብ፤** ብዙ መከራ የደረሰበት እግዚአብሔርን ይፈራ የነበረ ሰው። «መጽሐፈ ኢዮብ» ሀብታምና የተከበረ ሰው መሆኑን ይናገራል። በድንገት ሀብቱ ሁሉ፥ ልጆቹም ጠፉበት፤ በታላቅ ደዌ ተመታ፤ በሰውም ዘንድ የተናቀ ሆነ። ጠቢባን ነን የሚሉ ወዳጆቹ እንኳ በሰውር ስለበደለህ ነው እያሉ ተከራከሩት። የመጽሐፉ አንባቢ፥ የኢዮብ ቅንነት ይገለጽ ዘንድ በሰይጣን እንዲፈተን እግዚአብሔር እንደፈቀደ ያውቃል። ኢዮብ ግን ይህን አላወቀም፤ ከሁሉም ይልቅ ያስጨነቀው እግዚአብሔር ራሱ የተነሣበት ስለመሰለው ነበረ። በመጨረሻም እግዚአብሔር ጥበቡንና ኃይሉን በገለጠለት ጊዜ ኢዮብ፥ እንደዚህ ባለ አምላክ ለመታመን እንጂ መንገዶቹን ለማስተዋል ለሰው እንዳልተሰጠ ተረዳ፤ መከራከሩንም ተወ። ከዚያም በኋላ ቀድሞ ከነበረው ይልቅ የበለጠ ሀብት ተሰጠው፤ ረጅምም ዕድሜ በሰላምና በክብር ኖረ።

በምን ዘመን እንደኖረ ወይም ዖፅ የተባለው አገሩ የት እንደነበረ ለማረጋገጥ አልተቻለም። ሆኖም ከኑሮው ሁኔታ ለመገመት እንደሚቻለው በጥንት አባቶች ዘመን የኖረ ይመስላል፤ ኢዮብ 1፥1-5። ኢዮብ እንደ ኖኅና እንደ ዳንኤል ስለ ሌሎች የሚጸልይ ሰው ነበረ፤ ኢዮብ 42፥8:10፤ ሕዝ. 14፥14:20።



ሰዎች ወዳጃቸውን ሲያጽናኑ

**የኢዮብ መጽሐፍ፤** የመጽሐፉ የመጀመሪያውና የመጨረሻው ክፍሎች በስድ ንባብ ተጻፉ፤ ከም. 3 እስከ 42፥6፤ ድረስ ያለው ግን በግጥም ተጽፏል። በውስጡ ከሚገኘው የጥበብ ጥልቀትና ከሥነ ጽሑፍ ውበቱ የተነሣ የተደነቀ ነው። ጸሐፊው ማን እንደነበረ አልታወቀም። የኢዮብ ዝና ከጥንት ጀምሮ ቢታወቅም («ኢዮብ» ይመ.)፥ እስከ አሁን ድረስ የቆየው «መጽሐፈ ኢዮብ» ለብዙዎች በሰሎሞን ዘመን ወይም ከዚያ በኋላ የተጻፈ ይመስላቸዋል።

ሌሎች በአብርሃምና በይስሐቅ ዘመን የተጻፈ ነው ይላሉ። ሙሴ ግን የእስራኤል ሕዝብ የመጀመሪያ መሪና ነቢይ ስለነበረ፥ ከአምስቱ «ኦሪት» መጻሕፍት ጥምር መጽሐፈ ኢዮብን የጻፈው እርሱ እንደሆነ የሚገምቱ አሉ። እንደ «መጽሐፈ ምሳሌ» እና እንደ «መጽሐፈ መክብብ» የጥበብ መጻሕፍት ከተባሉት አንዱ ነው። ጳውሎስ ከም. 5፥13 ጠቅሶታል፤ 1ቆሮ. 3፥19። መጽሐፉ የተጻፈው የእግዚአብሔር አሳብና መንገድ ግሩምና ረቂቅ ነውና በሰዎች ጠባብ አስተያየት የሚተረጐም እንዳይደለ ለማሳየት ነው። በተለይም እግዚአብሔር እጅግ የሚምር ሆኖ፥ እንደ ኢዮብ መከራን ታግሠው የሚታመኑትን እንደሚባርካቸው ያስረዳል፤ ያዕ. 5፥10:11።

አከፋፈል ፦

1. የኢዮብ መፈተን፤ ም. 1ና 2።
2. ሕይወቴ ለምን ነው? የሚለው የኢዮብ ጥያቄ፤ 3።
3. ሦስት ወዳጆቹ ያቀረቡት ክርክር፤ 4-31።
4. የኤሊሁ አስተያየት፤ 32-37።
5. የእግዚአብሔር መልስ፤ 38-41።
6. የኢዮብ መጸጸትና መጽናናት፤ 42።

**ኢዮአስ፤** ትርጉሙ «እግዚአብሔር ሰጥቷል» ማለት ነው። ስምንተኛው የይሁዳ ንጉሥ። አባቱ የይሁዳ ንጉሥ አካዝያስ ከተገደለ በኋላ፥ ከወንድሞቹ ጋር እንዳይሞት አክስቱ ሸሸገችው። 7 ዓመት በሆነው ጊዜ፥ ከ835 ከክ.በ. ጀምሮ፥ አርባ ዓመት ነገሠ። የእግዚአብሔርንም ቤት አሳደሰ። ያሳደገው ካህን ዮዳሄ ከሞተ በኋላ እግዚአብሔርን ካደ፤ የገሠጸውንም የዮዳሄ ልጅ ዘካርያስን አስገደለ። ታምሞ ሳለ ባሪያዎቹ ገደሉት፤ 2ነገ. 11ና 12፤ 2ዜ.መ. 22፥10-24:27። በዚህ ስም ሁለት ሌሎች ሰዎች ተጠርተዋል፤ መሳ. 6፥11፤ 1ነገ. 22፥26።

**ኢዮአቄም፤** ትርጉሙ «እግዚአብሔር አቆመ» ማለት ነው። አስቀድሞ ኤልያቄም የተባለው የኢዮስያስ ልጅ። ፈርዖን ኒካው በወንድሙ በኢዮአክስ ምትክ በይሁዳ አንግሦ ኢዮአቄም ብሎ ሰየመው። ኢዮአቄም አስቀድሞ ለግብጽ፥ በኋላም ለባቢሎን ተገዛ። በ11 ዓመት የንግሥ ዘመኑም (ከ609-598 ከክ.በ.) ክፉ አደረገ፤ ኤር. 22፥13-19። የእግዚአብሔርን ቃል በመናቅ የኤርምያስን መጽሐፍ አቃጠለ፤ ኤር. 36። ናቡከደነፆር አስሮ ወደ ባቢሎን ሲወስደው በመንገድ ላይ ከኢየሩሳሌም ውጭ በመጥፎ ሁኔታ የሞተ ይመስላል፤ 2ዜ.መ. 36፥4-8፤ 2ነገ. 23፥34-24፥6፤ ኤር. 22፥18:19።

**ኢዮአብ፤** ትርጉሙ «እግዚአብሔር አባት ነው» ማለት ነው። የዳዊት የጦር ሠራዊት አለቃ የሆነ የጽሩያ ልጅ። ጽሩያ የዳዊት የእናቱ ልጅ ነበረች፤ የኢዮአብም ወንድሞች አቢሳና አሣሄል ይባሉ ነበር፤ 2ሳሙ. 17፥25፤ 1ዜ.መ. 2፥16። አበኔር ምንም

እንኳ ተገድዶ አሣሄልን ቢገድለውም፥ ኢዮአብ በተንኰል አበኔርን በመግደል ዳዊትን አሳዘነው፤ 2ሳሙ. 2፥12-32፤ 3፥21-39፤ ቍ. 39 ከም. 16፥10ና ከ19፥22 ጋር ይነጻጸር። ኢየሩሳሌምን ከኢያቡሳውያን እጅ በቀዳሚነት ነጥቆ በመያዙ ዳዊት የጦር ሠራዊት አለቃ አደረገው፤ 1ዜ.መ. 11፥6። በብልሃትም እየተዋጋ ድል ይነሣ ነበር፤ 2ሳሙ. 10፥7-11፥1፤ 12፥26። በዳዊት ትእዛዝ መሠረት ኦርዮን ለማስገደል አሳመነታም፤ 2ሳሙ. 11፥6-26። አቤሴሎምን ከስደት እንዲመለስ፥ ከዳዊትም ጋር እንዲታረቅ ረዳው፤ 2ሳሙ. 14። ዳዊት ሳይፈቅድ አቤሴሎምን ገደለ (2ሳሙ. 18፥5:10-16)፤ ዳዊትንም እንዳያለቅስለት ገሠጸው፤ 2ሳሙ. 19፥1-8። በእርሱ ምትክ የሠራዊት አለቃ እንዲሆን የተሾመውን የአክስቱን ልጅ አሜሳይን በተንኰል ከገደለው በኋላ በአለቅነቱ ጸና፤ 2ሳሙ. 17፥25፤ 19፥13፤ 20፥8-23። ሕዝቡን እንዳይቈጥር ዳዊትን መከረው፤ 2ሳሙ. 24፥3-9፤ 1ዜ.መ. 21። አዶንያስን ለማንገሥ አሰበ፤ 1ነገ. 1፥7። ንጹሕ ደም ስላፈሰሰ በሰሎሞን ትእዛዝ ተገደለ፤ 1ነገ. 2፥5:6:22:28-34።

**ኢዮአታም**፤ ትርጕሙ «እግዚአብሔር ፍጹም ነው» ማለት ነው። 1. የማስጠንቀቂያ ምሳሌ የተናገረ የጌዴዎን ታናሽ ልጅ፤ መሳ. 9፥5-57። 2. 12ተኛ የይሁዳ ንጉሥ የሆነው የዖዝያን (የዓዛርያስ) ልጅ። አባቱ በለምጽ ከተቀሠፈ በኋላ በሕዝቡ ላይ ዳኛ ሆነ። 740 ከክ.በ. አባቱ ሲሞት ነገሠ። መንገዱን በእግዚአብሔር ፊት አቀና፤ በረታም፤ 2ነገ. 15፥5:32-38፤ 2ዜ.መ. 26፥21-27፥9። በዘመኑ ኢሳይያስና ሚክያስ ትንቢት ይናገሩ ነበር፤ ኢሳ. 1፥1፤ ሚክ. 1፥1።

**ኢዮአካዝ**፤ ትርጕሙ «እግዚአብሔር ይዟል» ማለት ነው። ከ814-796 ከክ.በ. በሰሜናዊው የእስራኤል መንግሥት ላይ የነገሠ የኢዩ ልጅ ነበረ። ክፉ አደረገ። በዘመኑ የሶርያ ነገሥታት እስራኤልን አስጨነቁ። ኢዮአካዝ በጸለየ ጊዜ እግዚአብሔር ሰማው፤ 2ነገ. 10፥35፤ 13፥1-9።

**ኢዮአክስ**፤ ትርጕሙ «እግዚአብሔር ይዟል» ማለት ነው። አባቱ ኢዮስያስ በሞተ ጊዜ በይሁዳ ላይ የነገሠ። በ608 ከክ.በ. ሦስት ወር ነገሠ። የግብጽ ንጉሥ አስሮ ወደ ግብጽ ወሰደው፤ በዚያም ሞተ፤ 2ነገ. 23፥30-35። በ1ዜ.መ. 3፥15ና በኤር. 22፥10-12 ሰሎም በሚል ስም ይጠራል።

**ኢዮጴ**፤ ከኢየሩሳሌም 55 ኪ.ሜ. ርቆ በታላቁ ባሕር ዳር የሚገኝ ወደብ። የነገደ ዳን ርስት ድንበር እስከ ኢዮጴ ነበረ፤ ኢያሱ 19፥46። ከሰሎሞን በቀር የእስራኤል ነገሥታት አልያዙትም፤ 2ዜ.መ. 2፥16። ዮናስ በኰበለለ ጊዜ ከኢዮጴ በመርከብ ሄደ፤ ዮናስ 1፥3። ጴጥሮስ በኢዮጴ ዶርቃን ከሞት አስነሣ፤ ከዚያም በስምዖን ቤት ራእይ አየ፤ ሐ.ሥ. 9፥36-43፤ 10፥5-16። ዛሬ ቦታው ያፍ ይባላል፤ ከቴልአቢብ ከተማ ክፍል ነው፤ አሁን ግን ወደብነቱ ቀርቷል። ካ. 5መ።

**ኢጡርያስ**፤ ከገሊላ ባሕር በስተሰሜናዊ ምሥራቅ የነበረች ቦታ። ይኖሩባት የነበሩት ሰዎች ከእስማኤል ልጅ ከኢጡር የተወለዱ ነበሩ፤ ዘፍ. 25፥15። ፊልጶስ በዚያ ገዥ ነበረ፤ ሉቃ. 3፥1። ዛሬ ይህች ቦታ በሶርያ ውስጥ ትገኛለች።

**ኢጣልያ**፤ መናገሻ ከተማው ሮም የሆነ፥ ከታላቁ ባሕር በስተሰሜን ያለ ታላቅ አገር። የአቂላና የጵርስቅላ አገር ነው፤ ሐ.ሥ. 18፥2። ጳውሎስ ወደ ቄሣር ይግባኝ ሲል ወደ ኢጣልያ ተላከ (ሐ.ሥ. 27፥1:6)፥ እዚያም ታስሮ ሁለት ዓመታት ቆየ፤ ሐ.ሥ. 28፥16:31። በቦታው ቤተ ክርስቲያን ተመሥርታ ነበር፤ ዕብ. 13፥24። ካ. 7ሀ።

**ኢፍ**፤ መጠነኛ መስፈሪያ። ሰዎች ያለ አግባብ ስለተጠቀሙበት የከፋት መስፈሪያ ተባለ፤ ዘካ. 5፥6-10። እህል ይሰፍሩበት ነበርና እንዳያሳንሱ ትእዛዝ ተሰጣቸው፤ ዘሌ. 19፥36፤ አሞጽ 8፥5። «መስፈሪያ» ይመ.

**ኤሉል**፤ «ወር» ይመ.

**ኤሊ**፤ «እንስሳት» ይመ.

**ኤሊዔዘር**፤ ትርጕሙ «እግዚአብሔር ረድኤት ነው» ማለት ነው። የአብርሃም ቤት መጋቢ። ይህ ሰው በግእዝ ኢያውብር ይባላል። ለልጁ ለይስሐቅ ሚስት ይፈልግ ዘንድ አብርሃም ወደ መስጴጦምያ በላከው ጊዜ በጉዳዩ እግዚአብሔርን ለምኖ ርብቃን አገኘ። እርስዋም ከኤሊዔዘር ጋር ለመሄድ ተስማማችና ወደ ከነዓን አገር አብራ መጥታ ይስሐቅን አገባች፤ ዘፍ. 15፥2፤ 24፥1-67።

**ኤላ**፤ የአድባር ዛፍ ማለት ነው። በጌት አቅራቢያ ከኢየሩሳሌም በስተምዕራብ በኩል 40 ኪ.ሜ. ርቆ የሚገኝ ሸለቆ። በዚህ ሸለቆ ዳዊት ጎልያድን በወንጭፍ ድንጋይ ወርውሮ ገደለው፤ 1ሳሙ. 17።

**ኤል**፤ «እግዚአብሔር» ይመ.

**ኤልሳቤጥ**፤ የካህኑ የዘካርያስ ሚስት። ካረጀች በኋላ መጥምቁ ዮሐንስን ወለደች (ሉቃ. 1)፤ እርስዋም የቅድስት ድንግል ማርያም ዘመድ ነበረች። ፀንሳ ሳለች ማርያም በጐበኘቻት ጊዜ በመንፈስ ቅዱስ ተሞልታ አስደናቂ ቃል ተናገረች፤ ሉቃ. 1፥39-56።

**ኤልሳዕ**፤ ትርጕሙ «እግዚአብሔር ደኅንነት ነው» ማለት ነው። አቤልምሖላ በተባለው አገር ሣፋጥ ከተባለ ሰው የተወለደ እስራኤላዊ ነቢይ፤ 1ነገ. 19፥16። ነቢዩ ኤልያስ ከእግዚአብሔር በተገለጠለት መሠረት ኤልሳዕን ጠራው። እንደተጠራም ኤልሳዕ ሥራውን ትቶ ኤልያስን እየተከተለ ያገለግለው ነበር፤ 1ነገ. 19፥16-21፤ 2ነገ. 3፥11።

ኤልያስ በእሳት ሠረገላ ወደ ሰማይ በተወሰደ ጊዜ ኤልሳዕ አየው፤ ስለዚህ ኤልሳዕ የኤልያስ መንፈስ አድሮበት ለረጅም ጊዜ በእስራኤል እግዚአብሔርን አገለገለ፤ ተአምራትንም አደረገ፤ 2ነገ. 2፥1-14። ብዙዎች በምክሩ ይጠቀሙ ነበር፤ ተአምራትንም በማድረግ የተቸገሩትን ይረዳ ነበር። ለምሳሌ ያህል

የኢያሪኮን ውሃ ወደ ጣፋጭነት ለወጠ፤ 2ነገ. 2፥19-21። የሰደቡትን አጠፋ፤ 2ነገ. 2፥23-24። ባልዋ ለሞተባት ባልቴት የቤትዋን ችግር አስወገደላት፤ 2ነገ. 4፥1-7። የነቢያትን ልጆች ይረዳ ነበር፤ 2ነገ. 4፥38-44፤ 6፥1-7። ለሱነማዊቱቱ ሴት የሞተውን ልጅዋን አስነሣላት፤ 2ነገ. 4፥8-37። በቃሉ መሠረት ንዕማን የተባለው የሶርያ ንጉሥ ሠራዊት አለቃ ከለምጽ ተፈወሰ፤ 2ነገ. 5፥1-14። የሶርያ ንጉሥ እስራኤልን ለመዋጋት በወጣ ጊዜ ንጉሥ ኢዮራምን በምክር ረዳው፤ 2ነገ. 6፥8-23። በገና እያስደረደረ፥ መዝሙርም እያስዘመረ ትንቢት ይናገር ነበር፤ 2ነገ. 3፥15:16።

ኤልሳዕም ኢዮራም፥ ኢዩ፥ ኢዮአካዝና ዮአስ በተባሉት በአራት ነገሥታት ዘመነ መንግሥት ከአምሳ ዓመት በላይ አገለገለ፤ በመጨረሻም ታምሞ ሊሞት ሲል ዮአስን በፍርሃቱ ምክንያት ወቀሰው፤ ከሞተም በኋላ አፅንቱን የሞተ ሰው ነክቶ ሕያው ሆኗል፤ 2ነገ. 13፥14-21።

**ኤልዛቤል**፤ የሲዶናውያን ንጉሥ የኤትበአል ልጅ፥ የእስራኤል ንጉሥ የአክዓብ ሚስት፤ 1ነገ. 16፥31። ባልዋን በአልን እንዲያመልክ፥ ክፋትንም እንዲያደርግ ገፋፋችው፤ 1ነገ. 20፥25፤ 16፥32:33። 450 የበአልን ነቢያት ትቀልብ ነበር (1ነገ. 18፥19)፤ የእግዚአብሔርን ነቢያት ግን ትገድላቸው ነበር (ቍ. 4:13)። ኤልያስም የበአልን ነቢያት ስላስገደለ፥ በእርሱ ላይ ዛቻ ተናገረች፤ 1ነገ. 19፥1:2። ናቡቴን አስገደለች (1ነገ. 20፥5-15)፤ «ውሾች ይበሉሻል» የሚል ትንቢት ተነገረባት፤ ይህም ፍርድ የተፈጸመው በኢዩ ትእዛዝ ከመስኮት ከተጣለች በኋላ ነበር፤ 2ነገ. 9፥30-37። ስምዋ የርኵሰትና የአምልኮተ ጣዖት ምሳሌ ሆነ፤ ራእ. 2፥20-23።

**ኤልያስ**፤ ትርጕሙ «እግዚአብሔር አምላክ ነው» ማለት ነው። ኤልያስ በጣም ከታወቁት ከብ.ኪ. ነቢያት አንዱ ነው። የተወለደው ከዮርዳኖስ ወንዝ በስተምሥራቅ በሚገኘው ቴስቢ በሚባለው ቀበሌ ነው። ቴስቢ ከገለዓድ አገር ቀበሌዎች አንዱ ነው።

ንጉሥ አክዓብ ኤልዛቤል በተባለችው ሚስቱ መገፋፋት ምክር በእስራኤል አገር የበአልን ጣዖት አምልኮ ከጀመረ በኋላ፥ ነቢዩ ኤልያስ ጽኑ የሆነ የትግሣጽ ቃል ተናገረው። ንጉሡም ንስሓ ለመግባት ባለመፈለጉ በዝናብ እጦት ምክንያት ረጅም ድርቅ አገሩን እንደሚያጠቃው በእግዚአብሔር ስም ነገረው፤ 1ነገ. 17፥1። እግዚአብሔርም በነቢዩ አፍ የተናገረው ነገር ደርሶ አገሩ ራብ ስለጸናበት፥ ኤልያስ ዮርዳኖስን ተሻግሮ ኮራት በሚባለው ፈፋ ተቀመጠ። በዚያም ቁራዎች ይመግቡት ነበር፤ 1ነገ. 17፥2-7። የፈፋው ውሃ ከደረቀ በኋላ ወደ ሰራፕታ ተጕዞ ከአንዲት ባልቴት ጋር ተቀመጠ፤ 1ነገ. 17፥8-24። ይህም ከሆነ በኋላ በንጉሡ አማካይነት ከአራት መቶ አምሳ የበአል ነቢያት ጋር በቀርሜሎስ ተራራ ላይ እንዲገናኝ ተወሰነ። ነቢዩም ወደ ሕዝቡ ቀርቦ «እስከ መቼ ድረስ በሁለት አሳብ ታነክሳላችሁ? እግዚአብሔር አምላክ ቢሆን እርሱን ተከተሉ፤ በአል ግን አምላክ ቢሆን እርሱን ተከተሉ» አለ፤ 1ነገ. 18፥20:21።

ከዚያም በኋላ የእግዚአብሔርን ኃይል ከበአል ኃይል ጋር በማወዳደር የበአል ነቢያት በበኩላቸው መሥዋዕት አዘጋጅተው በላዩ ላይ ወይፈን እንዲያርዱና፥ ኤልያስም በበኩሉ ፈርሶ የነበረውን የእግዚአብሔርን መሠዊያ እንደገና አበጅቶ በላዩ ላይ የወይፈኑን ብልት እንዲያኖር ስምምነት አደረጉ። በሰማይ በእሳት የሚመልስልን አምላክ እርሱ በእውነት አምላክ ነው በሚል አሳብ ላይ የተመሠረተ ዝግጅት ነው። ከሰማይም በእሳት የመለሰ የኤልያስ አምላክ ነው። እግዚአብሔር ክብሩን ገለጠ። የበአል ነቢያትም ተገደሉ። ኤልያስ ወደ ቀርሜሎስ ራስ ወጥቶ ደመና እስኪታይ ሰባት ጊዜ ጸለየ፤ ወዲያውም ከባድ ዝናብ ዘነበ፤ 1ነገ. 18፥1-46።

የበአል ነቢያት በኤልያስ ትእዛዝ ስለሞቱ፥ ኤልዛቤል ተናድዳ ነቢዩን ለመግደል ባሰበች ጊዜ፥ ሕይወቱን ለማዳን እስከ ኮሬብ ተራራ ድረስ ሸሸ። እግዚአብሔር ግን በዚያ ተገናኝቶት ያለ ፍርሃት ከተደበቀበት ስፍራ እንዲመለስ አዘዘው። ተመልሶም የሶርያ ንጉሥ ይሆን ዘንድ አዛሄልን፥ የእስራኤልም ንጉሥ ይሆን ዘንድ ኢዩን እንዲቀባ ትእዛዝ ተቀበለ። ይህም የሆነበት ምክንያት እነዚህ ነገሥታት የአክዓብን ቤት በማጥፋት በላዩ ላይ የእግዚአብሔርን ፍርድ እንዲፈጽሙበት ነው፤ 1ነገ. 19፥1-21። አክዓብና ኤልዛቤል የወይን ስፍራውን በግፍ ለመውሰድ እንዲመቻቸው ናቡቴ የተባለውን ሰው አስገድለውት ነበር። ሁለቱም አስገዳዮች ተመሳሳይ በሆነ አሟሟት እንደሚሞቱ ነቢዩ ነገራቸው፤ 1ነገ. 20፥1-29። የአክዓብ ልጅ አካዝያስ ታሞ ሳለ፥ ብዔልዜቡልን ለመጠየቅ መልእክተኞችን በላከ ጊዜ፥ ኤልያስ እንደሚሞት ነገረው፤ 2ነገ. 1፥1-18። ከዚህ ዓለም መለየቱ በተቃረበ ጊዜ ኤልያስ የነቢይ አገልግሎቱን በእግዚአብሔር ፈቃድ ለኤልሳዕ አስረከበ። ከዚያም በኋላ በሥጋ ሳይሞት በሕይወት እያለ በእሳት ሠረገላ ወደ ሰማይ ተወሰደ፤ 2ነገ. 2፥1-12። ኤልያስ ለኢዮራም የተግሣጽ ደብዳቤ ጻፈለት፤ «ኢዮራም» ይመ.

ሚልክያስ «የእግዚአብሔር ቀን ሳይመጣ ነቢዩን ኤልያስን እልካላችኋለሁ» ብሎ ተነበየ፤ ሚል. 4፥5። በዚህ መሠረት ሰዎች መንፈሳዊ ኃይሉን አይተው ክርስቶስን «ኤልያስ ነው» ይሉት ነበር፤ ማር. 8፥28። ኢየሱስ ግን መጥምቁ ዮሐንስ የኤልያስን ዓይነተኛ ሥራ በመሥራቱ ትንቢቱን እንደፈጸመ መሰከረለት፤ ማቴ. 11፥14፤ 17፥10-13፤ ሉቃ. 1፥17። ኢየሱስ በተራራ ላይ ክብሩን በገለጠ ጊዜ ኤልያስ ከኢየሱስ ጋር ሲነጋገር ታየ፤ ሉቃ. 9፥30:33። ኤልያስ ምእመናን በብቸኝነታቸውና በድካማቸው ተስፋ እንዳይቆርጡ ምሳሌ ሆኖ ቀርቧል፤ ሮም 11፥2-4፤ ያዕ. 5፥17:18።

**ኤልያቄም**፤ ትርጕሙ «እግዚአብሔር ያስነሣል» ማለት ነው።

1. የኬልቅያስ ልጅ የንጉሥ ሕዝቅያስ የቤቱ አዛዥ። አሦራውያን ኢየሩሳሌምን በወረሩአት ጊዜ ከተማይቱን በልመናና በምክር ያድኑአት ዘንድ ንጉሥ

ሕዝቅያስ ከላካቸው መልእክተኞች አንዱ ነበረ፤ 2ነገ. 18፥18-37፤ ኢሳ. 36፥3-22። ከአሦር ንጉሥ ወኪል ያገኙትን መልስ ይዘው ወደ ነቢዩ ኢሳይያስ በሄዱ ጊዜ እግዚአብሔር ከዚህ ትልቅ መከራ እንደሚያድናቸው ገለጠላቸው፤ 2ነገ. 19፥2፤ ኢሳ. 37፥2።

2. የንጉሥ ኢዮአቄም የመጀመሪያ ስም። ስሙን የለወጠለት ለጊዜው በይሁዳ መንግሥት ላይ ያየለው ኒካው የተባለው የግብጽ ንጉሥ ነው፤ 2ነገ. 23፥34፤ 2ዜ.መ. 36፥4። በዚህ ስም የተጠሩ ሌሎችም አሉ፤ ነህ. 12፥41፤ ሉቃ. 3፥30:31፤ ማቴ. 1፥13።

**የኤሎን ሸለቆ**፤ ከኢየሩሳሌም በስተሰሜንና በሰተምዕራብ 16 ኪ.ሜ. ርቆ የተዘረጋ ሸለቆ። ኢያሱ በዚህ ቦታ የገባዖንን ጠላቶች እስኪያሸንፍ ድረስ ፀሐይንና ጨረቃን እንዲቆሙ በእግዚአብሔር ስም አዘዛቸው፤ ኢያሱ 10፥12-14።

**ኤማሁስ**፤ በኢየሩሳሌም አቅራቢያ ያለ ከተማ። ዛሬ ከኢየሩሳሌም በስተሰሜን 12 ኪ.ሜ. ያህል ርቀው የሚገኙ 3 ከተማዎች ምናልባት ቀድሞ ኤማሁስ ተብለው ይጠሩ እንደነበር ይታሰባል። የቀለዮጳ ቤት በኤማሁስ ይገኝ ነበር። ክርስቶስ ከተነሣ በኋላ በዚህ ቦታ ተገለጠ፤ ሉቃ. 24፥13-32።

**ኤርምያስ**፤ ትርጒሙ «እግዚአብሔር ከፍ ያደርጋል» ማለት ነው። ከእስራኤል ታላላቅ ነቢያት አንዱ። በኢየሩሳሌም አቅራቢያ ካለው ከተማ ከዓናቶት፥ ከካህናትም ወገን ነበረ።

አባቱ በኢዮስያስ ዘመን የሕጉን መጽሐፍ ያገኘው ኬልቅያስ መሆኑን ብዙ ሊቃውንት ያምናሉ። ለእስራኤል ብቻ ሳይሆን ለአሕዛብም ጭምር ነቢይ እንዲሆን በተጠራ ጊዜ ደንገጠ፤ «ብላቴና ነኝ» በማለት አመነታ። በኋላ ግን በተሰጠው ተስፋ መሠረት በረታ። የተጠራውም 626 ከክ.ል.፥ የይሁዳ ንጉሥ ኢዮስያስ በነገሠ በ13ኛው ዓመት ነበር። በኢዮስያስም ልጆች ዘመን ትንቢት እየተናገረ ቆይቶ፥ ከተጠራ ከ40 ዓመት በኋላ የኢየሩሳሌምን መማረክ አየ፤ ኤር. 1፥1-10። በዚህም ዘመን አምስት ነገሥታት ነገሡ።

1. ኢዮስያስ ከይሁዳ ደግ ነገሥታት የመጨረሻው ነበረ፤ አምልኮ ባዕድን ለማስወገድ፥ የእግዚአብሔርን ቤትና አምልኮ ለማሳደስ ብዙ ደከመ። በሞቱም ኤርምያስ አለቀሰ፤ 2ዜ.መ. 34ና 35።

2. የኢዮስያስ ልጅ ኢዮአክስ (ሰሎም) በነገሠ በ3ኛው ወር ወደ ግብጽ ተማርኮ ሄደ፤ 2ዜ.መ. 36፥1-4፤ ኤር. 22፥10-12።

3. ወንድሙ ኢዮአቄም አስቀድሞ ለግብጽ፥ በኋላም ለባቢሎን ተገዛ፤ 2ዜ.መ. 36፥4-8። እጅግም ክፉ ነበረ (ኤር. 22፥13-19)፤ ኤርምያስን ተቃወመው፤ መጽሐፉንም አቃጠለበት፤ ኤር. 36።

4. የኢዮአቄም ልጅ ዮአኪን (ኢኮንያን) በነገሠ በ3ኛው ወር ከብዙዎች የይሁዳ ሰዎች ጋር ወደ ባቢሎን ተማረከ፤ 2ነገ. 24፥8-17፤ ኤር. 22፥24-30። የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደነፆር አጐቱን ሴዴቅያስን አነገሠ።

5. ሴዴቅያስ የኤርምያስን ምክር ይጠይቅ ነበር እንጂ አልተቀበለውም፤ ኤር. 37። በከፋቱም ጸና፤ ኤርምያስ በተናገረው ትንቢት መሠረት ሴዴቅያስ ተማረከ፤ ኤር. 34፥2-5። በ11ኛ ዓመቱ ኢየሩሳሌም ተይዛ ስትቃጠል ኤርምያስ ታስሮ ነበር። ናቡከደነፆር በይሁዳ ላይ ከሾመው ገዥ ከጎዶልያስ ጋር እንዲኖር እንጂ ወደ ባቢሎን እንዳይማረክ ፈቀደለት። ጎዶልያስ ከተገደለ በኋላ የቀሩት አይሁድ በግድ ወደ ግብጽ ወሰዱት፤ ኤር. 39-43። በግብጽ እንኳ ትንቢት ከመናገር ዝም አላለም፤ ኤር. 43፥8-44፥30። ስለ አሟሟቱ የተጻፈ ነገር የለም።

በ«ትንቢተ ኤርምያስ» የትንቢቱ ቃል ብቻ ሳይሆን፥ ስለ ራሱ ስለ ኤርምያስ ስለደረሰበትም መከራ ብዙ ነገር ስለተጻፈ፥ ከሌሎች ነቢያት ይልቅ ጠባዩና ሁኔታው ተገልጿል። ኢየሩሳሌምን ሕዝቡንም ምንም ቢወድ (ኤር. 8፥18-9፥1፤ 13፥17)፥ መማረካቸው እንደማይቀር ሊነግራቸው ተገደደ። ከዚህም በላይ፥ ለባቢሎን ንጉሥ እጅ ስጡ፤ ተገዙም፤ ምርኮኞችም እስከ 70 ዓመት ድረስ አይመለሱም ብሎ የተገለጠለትን የእግዚአብሔርን ቃል ስለተናገረ ተጠላ። ብዙዎች ሊገድሉት አሰቡ፤ ኤር. 11፥21፤ 26፥11፤ 36፥26፤ 38፥6-10። ተመታ፤ በእግር ግንድ ተያዘ፤ በጭቃ ጕድጓድ ተጣለ፤ ታሰረም፤ 20:2፤ 37፥13-15፤ 38፥28። አብዷል ተባለ፤ 29፥26:27። ከዚህም ሁሉ ጋር ለሕዝቡ ምልክት እንዲሆን ሚስት እንዳያገባ፥ ወደ ግብዣ ወይም ወደ ልቅሶ እንዳይሄድ ተከለከለ፤ ኤር. 16። የተሰማው ጭንቀት፥ የጸለየውም ጸሎት በም. 1፥4-10፤ 8፥18-9፥2፤ 11፥18-12፥6፤ 15፥10-21፤ 17፥12-18፤ 18፥18-23፤ 20፥7-18 ተጽፏል። በደረሰበትም ሁሉ እግዚአብሔር እንደ ተስፋው ይጠብቀው ነበር፤ 1፥18:19፤ 15፥20:21።

**የኤርምያስ ትንቢት**፤ ኤርምያስ በአምስት የይሁዳ ነገሥታት ዘመናት ትንቢት ተናገረ፤ «ኤርምያስ» ይመ.። ኤርምያስን በጠራው ጊዜ እግዚአብሔር የይሁዳ ሕዝብ እኔን ትተው ሌሎችን አማልክት ስላመለኩ ከሰሜን ጠላት አስነሣባቸዋለሁ ብሎ ነገረው፤ ኤር. 1፥13-16። ኤርምያስም፥ ሕይወታቸው ወደ ሆነው ወደ እግዚአብሔር እንዲመለሱ እስከ 23 ዓመት ድረስ ሳያቋርጥ ይጠራቸው ነበር፤ እነርሱ ግን አልሰሙትም፤ 25፥3-7። በዚያም፥ በተጠራ በ23ኛው ዓመት ከሰሜን የሚመጣባቸው ንጉሥ፥ ናቡከደነፆር በባቢሎን ላይ ነገሠ፤ 25፥1። እርሱም በይሁዳ ላይ ብቻ ሳይሆን በብዙ ሕዝቦች ላይ እንደሚመጣ፥ እስከ 70 ዓመትም ድረስ እነዚህ ሕዝቦች ለባቢሎን እንደሚገዙ ተነበየ፤ 25፥8-11። ከዚያም በኋላ ባቢሎን እንደሚወድቅ ገለጠ፤ 25፥12-14። ይህን ከባድ የፍርድ መልእክት ለመናገር የበቃው በአምላኩ ኃይል እንጂ በራሱ ችሎታ አልነበረም፤

1፥6-10:17-19። በእነዚህም 23 ዓመታት የተናገረው ትንቢት ሁሉ ተጽፎ ሲነበብለት ንጉሥ ኢዮአቄም ጽሑፉን ቆራርጦ አቃጠለው። ኤርምያስ እንደገና በባሮክ እጅ አስጻፈው፤ ም. 36።

ሴዴቅያስ ከነገሠ ጊዜ ጀምሮ ኤርምያስ፥ ሴዴቅያስን «ለባቢሎን ንጉሥ ተገዙ፤ በሕይወትም ትኖራላችሁ፥ ኢየሩሳሌምም አትጠፋም» ይለው ነበር፤ 27፥12:13:17፤ 38፥17:18። ሴዴቅያስ ግን በግብጽ ስለተማመነ (37፥3-10)፤ ደግሞም ስላመነታ (38፥19) ለባቢሎን ንጉሥ እጅ አልሰጠም። ከዚህም የተነሣ በእርሱና በኢየሩሳሌም ላይ የደረሰው ፍርድ የባሰ ሆነ፤ 39፥1-10፤ 2ዜ.መ. 36፥11-21።

ኤርምያስ የፍርድን መልእክት ብቻ ሳይሆን፥ የተስፋን መልእክት ተናግሯል። እግዚአብሔር ሕዝቡን ከምርኮ እንደሚመልስ፥ ኢየሩሳሌምም ታድሳ «እግዚአብሔር ጽድቃችን» እንደምትባል (33፥16)፥ እግዚአብሔርም ከሕዝቡ ጋር አዲስ ኪዳንን እንደሚያደርግ፥ ከዳዊት ዘር የሆነው ንጉሥ ነግሦ፥ ስሙ «እግዚአብሔር ጽድቃችን» እንደሚባል ተነበየ፤ ም. 30-33፤ 23፥1-6። ኤርምያስ በቃል ብቻ ሳይሆን በልዩ ልዩ ድርጊትና ምሳሌ መልእክቱን ይገልጥ ነበር። የመታጠቂያ (ም. 13)፥ የሸክላ ሠሪ (ም. 18)፥ የገምቦ (ም. 19፤ 20)፥ የእስራትና የቀንበር (ም. 27፤ 28)፥ የእርሻ (ም. 32)፥ የሬካባውያን (ም. 35)፥ የድንጋዮች (43፥8-13)፥ እንዲሰጥም የተደረገው መጽሐፍ ምሳሌዎች (51፥59-64)፤ ያያቸውም የለውዝ በትር፥ የእፍላል፥ የበለስም ቅርጫት ራእዮች (1፥11-13፤ 24)፤ እነዚህ የትንቢቱ መግለጫዎች ናቸው።

የኤርምያስ ዋና መልእክት፥ እግዚአብሔር ታላቅና ቅዱስ ነውና ሕዝቡ ከክፋት ተመልሰው በፍጹም ልብ እንጂ በሐሰት እንዳያመልኩት ነው። በኢዮስያስ ዘመነ መንግሥት ይሁዳ በእውነት ሳይሆን፥ በአፍ ወደ እግዚአብሔር ተመለሰ፤ 3፥10። ካህናትና ነቢያትም፥ «የእግዚአብሔር ቤት እዚህ ነው፥ እናንተም ሕዝቡ ናችሁ፤ አይዞአችሁ፥ ምንም አይደርስባችሁም» እያሉ ሕዝቡን ያታልሉ ነበር እንጂ እግዚአብሔርን ስለ መፍራት፥ በቅንነትም ስለ መኖር አይናገሩም ነበር፤ 7፥3-11፤ 14፥13-18፤ 23፥9-40። እግዚአብሔር የሚያየው ግን የሰውን ልብ ነው (17፥9:10)፤ በፍጹምም ልብ እግዚአብሔርን የሚፈልጉ ያገኙታል፤ 29፥13። እግዚአብሔር ሕጉን በሕዝቡ ልብ የሚጽፍበትን ጊዜ በተስፋ ይመለከት ነበር፤ 31፥33፤ 32፥39:40። የኤርምያስ አጻጻፍ ዜና መዋዕልን በመጠበቅ ሳይሆን፥ በየአርእስቱ የተደረደረ ነው።

አከፋፈል :-

1. የነቢዩ መጠራት፤ ም.1።

2. ወደ እግዚአብሔር ተመለሱ የሚሉ የጥሪና የማስጠንቀቂያ መልእክቶች፤ 2-20።

3. ዮአኪን ከተማረከ በኋላ ለነገሥታት፥ ለሕዝቡና ለምርኮኞች የተሰጡ መልእክቶች፤ 21-29፥ ከም. 35፤ 36፤ 45 ጋር።

4. የኢየሩሳሌም ልማትና የአዲስ ኪዳን ተስፋ፤ 30-33።

5. የኢየሩሳሌም መከበብና ውድቀት፤ 34፤ ከ37-39 ጋር።

6. ኤርምያስ በይሁዳ ከቀሩት አይሁድ ጋር መኖሩ፤ 40-42።

7. ኤርምያስ በግብጽ መኖሩ፤ 43፤ 44።

8. በአሕዛብ ላይ የተነገሩ ትንቢቶች፤ 46-51።

9. ተጨማሪ የታሪክ ክፍል፤ የኢየሩሳሌም መውደቅ፤ 52።

**የኤርምያስ መልእክት**፤ ነቢዩ ኤርምያስ ኢየሩሳሌም ሳለ በባቢሎን ለተማረኩት አይሁድ ላከላቸው የተባለው መልእክት ነው። በኢትዮጵያ አርቶዶክስ ቤ.ክ. መ.ቅ. የሰ.ኤ. 6ኛ ምዕራፍ ነው።

**ተረፈ ኤርምያስ**፤ «መጽሐፈ ባሮክ» ይመ.

**ኤርሞን**፤ ኤርሞን አንድን ዐይነት ትልቅ ዛፍ የሚያመለክት የዕብራይስጥ ቃል ነው፤ ዘፍ. 30፥37። በሕዝ. 31፥8 ቃሉ «አስታ» ተብሎ ቢተረጐም እንኳ፥ ኤርሞን የሚባለው ዛፍ በኢትዮጵያ ውስጥ ስለማይገኝ፥ ልዩ የአማርኛ መጠሪያ ስም የለውም።

**የኤርትራ ባሕር**፤ ከሲና ልሳነ ምድር በስተምዕራብ፥ በስተምሥራቅና በስተደቡብ ያለ ባሕር፤ ዘጸ. 10፥19፤ 23፥31፤ ዘኍ. 33፥11፤ 1ነገ. 9፥26። እስራኤል የኤርትራን ባሕር የተሻገሩበት መልካ በየት በኩል እንደሆነ ዛሬ ለመወሰን ያስቸግራል፤ ዘጸ. 13፥18፤ መዝ. 106፥9። አንዳንድ መምህራን በታው በሱኮት አጠገብ ያለው ሐይቅ ይሆናል ይላሉ። ከ. 2ሸ። «ባሕር» ይመ.

**ኤሽኮል**፤ ዘለላ ማለት ነው። ከኬብሮን በስተደቡብ በቢርሳቤህ መንገድ ያለ ሸለቆ። በአብርሃም ወዳጅ በኤሽኮል የተሰየመ ይመስላል፤ ዘፍ. 14፥13። 12 የእስራኤል ሰላዮች ከዚህ ሸለቆ የወይን ዘለላ አረግ ወሰዱ፤ ዘኍ. 13፥23:24።

**ኤታኒም**፤ «ወር» ይመ.

**ኤዊያውያን**፤ (ኤዊያን)፤ ከከነዓን የተገኘ ወገን፤ ዘፍ. 10፥17። ዋና አገራቸው በሊባኖስ ነበረ፤ መሳ. 3፥3። ኢያሱ ድል አድርጎቸዋል፤ ኢያሱ 11፥3። ሰሎሞንም ገባሮች አድርጎአቸው ነበር፤ 2ዜ.መ. 8፥7-8።

**ኤውላጥ (ሐዊላ)**፤ 1. የአገር ስም፥ ሀ) በዔድን አካባቢ የነበረው (ዘፍ. 2፥11-12)፥ ለ) በሲና አካባቢ የነበረው፤ ዘፍ. 25፥18። 2. የሰው ስም፤ ዘፍ. 10፥7:29።

**ኤዶማውያን**፤ ከዔሳው የተገኙ በኤዶም አገር ይኖሩ የነበሩ ሕዝቦች፤ ዘዳ. 23፥7። በኤዶም ኤዶማውያን ተብለዋል። ዔሳው ወደ ሴይር ከገባ በኋላ

ዘሩ ዋና ሕዝብ ሆነ፤ ዘፍ. 36፤ ዘዳ. 2፥12። እስራኤል በአገራቸው እንዲያልፍ አልፈቀዱም፤ ዘኍ. 20፥14-21። ሳኦል ከኤዶምያስ ጋር ተዋጋ፤ ዳዊት አሸነፋቸው፤ ከነገሥታትም ጋር ይጣሉ ነበር፤ 1ሳሙ. 14፥47፤ 2ሳሙ. 8፥14፤ 1ነገ. 11፥14-22፤ 2ዜ.መ. 21፥8-10፤ 25፥11-15፤ ኢሳ. 34፤ 63፥1-3፤ ኤር. 49፥17። መቃብያን ኤዶማውያንን አስገርዘው ወደ እስራኤል አስገቡአቸው። የሄሮድስ ቤተሰብ ከኤዶምያስ የመጣ ነበር።

**ኤዶም፤** 1. ዔሳው የተሰየመበት ስም። በአማርኛ ኤዶም ቀይ ተብሎ ይተረጐማል። ይህንም ስም ሊያገኝ የቻለው ከአደን ደክሞ ሲመለስ፥ ወንድሙ ያዕቆብ ያዘጋጀውን ቀይ ወጥ በመመኘቱና ብኩርናውን በመሸጥ ገዝቶ በመብላቱ ነው፤ ዘፍ. 25፥30። 2. በፊት ሴይር የተባለው ኤዶማውያን ይኖሩበት የነበረው አገር ስም። አገሩ ከጨው ባሕር በስተደቡብ በኩል ነበረ። ካ. 2ረ።

**ኤዶምያስ፤** የኤዶም አገር የግሪክ አጠራር፤ ማር. 3፥8።

**ኤጺስ ቆጶስ፤** «ጳጳስ» ይመ.

**ኤጳፍራ፤** ከጳውሎስ ጋር አብሮ የሠራና የታሰረ። ጳውሎስ በኤፌሶን ሲያስተምር ሳለ ኤጳፍራ በቆላስይስ፥ በሎዶቅያ፥ በኢያራም ወንጌልን ሰበከ፤ ቤተ ክርስቲያንንም አቋቋመ። ከዚያም ወደ ጳውሎስ ደረሰ፤ የቤተ ክርስቲያንንም ሁኔታ ነገረውና ጳውሎስ ወደ ቆላስይስ መልእክት ጻፈ፤ ቆላ. 1፥7፤ 4፥12-13፤ ፊልሞና 23-24።

**ኤፉድ፤** በብሉይ ኪዳን፥ በወገብ የሚታሰር የካህናትና ለእግዚአብሔር አምልኮት የተለዩ ሰዎች የሚለብሱት ልብስ፤ 1ሳሙ. 22፥18፤ 2ሳሙ. 6፥14። ሊቀ ካህናቱ መሥዋዕት ሲያቀርብ ይለብስ የነበረው ልዩ ዓይነት ኤፉድ ከደረት እስከ ጭን የሚደርስ ነው። በደረቱም ላይ ልዩ ኪስ አለው፤ በጫንቃዎችና በወገብ በኩል ይታሰራል፤ ዘጸ. 39፥1-21። በጌዴዎን ዘመን ሕዝቡ ለወርቅ ኤፉድ እየሰገዱ ኃጢአትን ይሠሩ ነበር፤ መሳ. 8፥27። በዳዊት ዘመን እግዚአብሔርን በኤፉድ ፊት ይለምኑት ነበር፤ 1ሳሙ. 23፥9፤ 30፥7።

**ኤፌቆሮስ፤** 341 ከክ.በ. የተወለደ የግሪክ ፈላስፋ። ኤፌቆሮስ ዋና የሰው ዓላማ በዚህ ዓለም ደስታን ማግኘት እንደነበረ አስተማረ። ደስታም የሚገኘው ከዓለም በመራቅ፥ የዚህን ዓለም ነገር ሁሉ ችል በማለት ነው፤ ከሞትም በኋላ ሕይወት የለም ብሎ አስተማረ፤ ሐ.ሥ. 17፥18-32።

**ኤፌሶን፤** በአዲስ ኪዳን ዘመን ኤፌሶን በሮም መንግሥት ሥር ሆና እስያ በምትባል አውራጃ በኤጂያን ባሕር ዳር የምትገኝ ወደብ ነበረች። አገሪቱ ዛሬ ቱርክ ትባላለች፤ ከተማይቱም ሳልዝክ ትባላለች። በዚያን ዘመን 360 ሺህ ሰዎች የሚኖሩባት፥ እንደ እስክንድርያና እንደ አንጾኪያ ታላቅ የንግድ ከተማ ነበረች። በከተማይቱ ሠላሳ ሺህ የሚያህሉ ወንበሮች የሚገኙበት ትልቅ የጨዋታ ስፍራ (እስቴድየም) ተሠርቶ ነበር። አርጤምስ ለምትባል አምላክ ትልቅ መቅደስ ታንጾ ነበር፤ ብዙ የዝሙት ሥራ በአምልኮትዋ ስም ይደረግ ነበር፤ ሐ.ሥ. 19፥24:27። ዛሬ ግን የባሕሩ አሸዋ የድሮይቱን ከተማ ሸፍኖአታልና ሰው አይኖርባትም፤ የዛሬይቱም ከተማ ከባሕሩ 12 ኪ.ሜ. ያህል ትርቃለች። ካ. 7ሰ።



በኤፌሶን የነበረ የአርጤምስ ቤተ መቅደስ፥ ምስልና ገንዘብ

**የኤፌሶን ቤተ ክርስቲያን፤** ክርስትና ወደ ኤፌሶን የመጣው በጵርስቅላና በአቂላ አማካይነት ነው፤ ሐ.ሥ. 18፥18:19። ቢሆንም፥ ሐዋርያው ጳውሎስ በኋላ ወደ ኤፌሶን እንደመጣና 3 ዓመት ያህል እያስተማረ ብዙውን ሕዝብ ወደ ክርስቶስ እንደመለሰ እናውቃለን፤ ሐ.ሥ. 19፥8-27፤ 20፥17-35። ቤ.ክ. በዚያ ጊዜ ተቋቁማ ይሆናል። በኋላ ደግሞ ጢሞቴዎስ ተልኮላቸዋል፤ 1ጢሞ. 1፥3:4። ነገር ግን ስለ ኤፌሶን ቤ.ክ. የምንሰማው መጨረሻው ነገር አሳዛኝ ነው። ሐዋርያው ዮሐንስ በእስያ ወደሚገኙት ሰባት አብ. ክ. መልእክትን ሲልክ የመጀመሪያውን መልእክት ወደ ኤፌሶን ልኮ «የቀደመውን ፍቅርህን ትተሃል» ብሎ የመንፈስ ቅዱስ ወቀሳ ያስተላልፋል፤ ራእ. 2፥4:5።

**የኤፌሶን መልእክት፤** ቅዱስ ጳውሎስ በሮም ታስሮ ሳለ በ63 ዓ.ም. ገደማ ይህን መልእክት ጻፈ። የተጻፈው በኤፌሶን ከተማ ለነበሩት ምእመናን ነው፤ ቢሆንም በመጀመሪያዎቹ ረቂቆች ላይ ለማን እንደተጻፈ በቍ. 1 ላይ አልተገለጠምና አንዳንዶች ለኤፌሶን ብቻ ሳይሆን በእስያ ለነበሩት አብ.ክ. ሁሉ የተጻፈ እንደሆነ ያስባሉ፤ ሐ.ሥ. 19፥26።

ሐዋርያው ብዙ ጊዜ መልእክቶችን የጻፈው በአብ.ክ. ውስጥ በተፈጠሩ ስሕተቶችና በሚነሡ ጥያቄዎች ምክንያት ነው። በኤፌሶን መልእክት ግን ምንም ዓይነት የቤ.ክ. ስሕተት በግልጥ አልተጠቀሰም። ቢሆንም ከአይሁድ፥ ከአስማተኞች፥ ከአርጤምስ አምላኪዎችና ከነጋዴዎች ከባድ ተጽእኖ በቤ.ክ. ላይ እንደነበረ ከሐ.ሥ. ም. 19 እንማራለን፥ ከዚህም ሁሉ በስተጀርባ ክፉ ኃይላት ነበሩ፤

1፥19-21፤ 2፥1-2፤ 3፥10፤ 6፥11-12። እንግዲህ ምእመናን እንዲጸኑ ሐዋርያው በመጀመሪያ በም. 1-3 ስለ እግዚአብሔር ዕቅድ ሰፊና ጥልቅ ማብራሪያ ይሰጣል። ከዚያም ቀጥሎ በም. 4-6 ጳውሎስ እንደተለመደው ትምህርቱን ከተግባር ጋር በማዛመድ፥ ክርስቲያኖች የእግዚአብሔርን ውሳኔ በተመለከተ ምን ዓይነት ሰዎች መሆን እንደሚገባቸው ያሳስባል። ይህን መልእክት መረዳት የሚችሉ ሰዎች ወደ ስሕተት ቶሎ አይገቡም፥ ሐሰተኞችን መቃወም ይችላሉ፤ በክፉ ቀንም ጸንተው ይቆማሉ።

አከፋፈል ፦

1. ሰላምታ፤ 1፥1-2።

2. ሁሉን ለመጠቅለል የሥላሴ ዕቅድ፤ 1፥3-23።

ሀ) አብ በክርስቶስ ምእመናንን ባረከ፥ መረጠና ወሰነ (4-6)፥ ለ) ወልድ በደሙ ስለዋጃቸው የእግዚአብሔር ጸጋና ጥበብ ተገልጧል (7-10)፥ ሐ) መንፈስ ቅዱስ በእግዚአብሔር አብ ውሳኔ መሠረት ያመኑትን አትሟል፥ ባለ ርስቶች መሆናቸውን አረጋግጦላቸዋል (11-14)፥ መ) ክርስቲያኖች የእግዚአብሔርን ዕቅድና ኃይል እንዲያስተውሉ መጸለይ ይገባቸዋል፤ 15-23።

3. የእግዚአብሔር ዕቅድ ሲፈጸም የሚታዩ ሂደቶች፤ ም. 2 እና 3።

ሀ) እያንዳንዱ አማኝ በክርስቶስ ሕይወትን ተቀብሏል (2፥1-10)፥ ለ) አይሁድና አሕዛብ በክርስቶስ መስቀል ታርቀዋል (2፥11-18)፤ አንድ ቤተሰብ ሆነዋል (2፥19-22)፥ ሐ) በቤ.ክ. የእግዚአብሔር ጥበብ ይገለጣል (3፥1-13)፥ መ) በይበልጥ ምእመናን በክርስቶስ እንዲጐለምሱና ፍቅሩን እንዲያውቁ መጸለይ ይገባቸዋል፤ 3፥14-21።

4. በቤ.ክ. የእግዚአብሔር ዕቅድ የሚፈጸምባቸው መንገዶች፤ 4፥1-6፥20።

ሀ) አንድነት (4፥1-6)፥ ለ) ብስለት (4፥7-16)፥ ሐ) የግል መንፈሳዊ ሕይወት ተሐድሶ (4፥17-5፥20)፥ መ) የባሎችና የሚስቶች፥ የልጆችና የወላጆች፥ የአገልጋዮችና የአሠሪዎች ግንኙነት የአክብሮት አጠባበቅ (5፥21-6፥9)፥ ሠ) የመንፈሳዊ ትግል ወታደራዊ አቋም፤ 6፥10-20።

5. መደምደሚያ፤ የጳውሎስ ሁኔታና ቡራኬ፤
6፥21-24።

**ኤፍራታ**፤ የይሁዳ ቤተ ልሔም የሚገኝበት አካባቢ፤ 1ዜ.መ. 2፥50-51፤ መዝ. 132፥6፤ ሚክ. 5፥2።

**ኤፍራጥስ**፤ ከዔድን የሚነሣ ወንዝ፤ ዘፍ. 2፥10-14። በመስጴጦምያ ካሉ ሁለት ታላላቅ ወንዞች አንዱ፤ ርዝመቱ 2850 ኪ.ሜ. ነው። በባቢሎን አገር ታላቁ ወንዝ ይባል ነበር፤ ይህ ወንዝ በዳዊትና በሰሎሞን ጊዜ የእስራኤል መንግሥት ድንበር ነበረ፤ ዘዳ. 1፥7:8፤ 1ዜ.መ. 18፥3፤ 2ዜ.መ. 9፥26። ካ. 1ለ።

**ኤፍሬም**፤ በግብጽ አገር ዮሴፍ ከአስናት የወለደው ሁለተኛ ልጅ፤ ዘፍ. 41፥52። የምናሴ ታናሽ ወንድም። ያዕቆብ የዮሴፍን ልጆች በባረከ ጊዜ ታላቁን ምናሴን ሁለተኛ አድርጎ የበረከቱን ቃል አስቀድሞ በኤፍሬም ላይ ተናገረ። እንደ በኵር ልጅ እንደ ሮቤል ቈጠረው፤ ዘፍ. 48፥5-22። የእስራኤል ልጆች ከነዓንን በወረሱ ጊዜ የነገደ ኤፍሬም ድርሻ በስተሰሜን ሆኖ በደቡብ በኩል ከብንያም አገር ጋር የሚዋሰን ሆነ። ካ. 3ሰ።

መንግሥትም በሁለት ከተከፈለ በኋላ ኤፍሬም በእስራኤል መንግሥት ነገዶች መካከል የመሪነትን ስፍራ ስለወሰደ፥ መላው እስራኤል አንዳንድ ጊዜ ኤፍሬም በሚለው ስም ይጠራ ነበር፤ 1ነገ. 12፤ ኢሳ. 7፥5፤ ሕዝ. 37፥16፤ መዝ. 78፥9። ከዚሀ ወገን ኢያሱ ተወለደ፤ ኢያሱ 24፥29:30። «ነገድ» ይመ.

**እህል**፤ ለሰው ምግብ የሚሆንና ኃይል የሚሰጥ የሕይወት ድጋፍ፤ ዘሌ. 26፥26፤ መዝ. 104፥15። ዕብራውያን በተለይ በስንዴና በገብስ ይኖሩ ነበር። «ምግብ»፥ «እንጀራ» ይመ.

**እልል**፤ እልልታ፤ የደስታ ጩኸት፥ ደስታን የተሞላ ድምፅ። በብ.ኪ. ዘመን ሰዎች ለእግዚአብሔር ክብር በእልልታ ይዘምሩ ነበር። ቃሉ በዳዊት መዝሙር ብዙ ጊዜ ተጠቅሷል፤ መዝ. 47፥5፤ 95፥1-2፤ 150፥5።

**እልዋሪቆን**፤ ከመቄዶንያ በስተሰሜን የነበረች የሮም መንግሥት ክፍለ አገር። ጳውሎስ ከኢየሩሳሌም እስከ እልዋሪቆን ወንጌልን ሰበከ፤ ሮም 15፥19:20። ዛሬ ይህች ቦታ በዩጎዝላቪያ አገር ትገኛለች።

**እሑድ**፤ የሳምንቱ መጀመሪያ ቀን፥ የክርስቶስ ትንሣኤና የጰንጠቆስጤ ቀን መታሰቢያ፤ ዮሐ. 20፥1-25፤ ሐ.ሥ. 2፥1-41። ከክርስቶስ ዕርገት በኋላ የዕብራውያን አማኞች በሰባተኛውና በአንደኛው ቀን በሁለቱ ይሰበሰቡ ነበር። በኋላ ግን የአሕዛብ አብ. ክ. እየበረከቱ ሲሄዱ የሰባተኛው ማለት የሰንበት ቀን ስብሰባ ቀረ። በጢሮአዳ ያሉት አማኞች በእሑድ ቀን ይሰበሰቡ ነበር፤ ሐ.ሥ. 20፥7። ጳውሎስ ለቆሮንቶስ ቤ. ክ. ሲጽፍ በሳምንቱ መጀመሪያ ቀን ገንዘባቸውን እንዲያዋጡ አዘዛቸው፤ 1ቆሮ. 16፥2። እሑድ የጌታ ቀን በመባል ይታወቃል፤ ራእ. 1፥10። «ሰንበት» ይመ.

**እመቤት**፤ በአንድ ቤተሰብ መካከል አስተዳዳሪና ኀላፊ የሆነች ታላቅ ሴት ወይዘሮ፤ ምሳ. 30፥23፤ ኢሳ. 47፥5:7። ቃሉ ቤ. ክ.ን ሊያመለክት ይችላል፤ 2ዮሐ. 1:2:5።

**እምቢልታ**፤ ከቀርከሃ ወይም ከሌላ የሚሠራ እንደ ዋሽንት ያለ የዜማ ዕቃ፤ ኢዮብ 21፥12፤ 30፥31። የቃል ኪዳኑ ታቦት ሲከብር ይዘመርበት ነበር፤ 1ዜ.መ. 15፥28። ብዙ ጊዜ የዳዊት መዝሙር በእምቢልታ ይዘመር ነበር፤ መዝ. 150፥4።

**እምነት**፤ እግዚአብሔር ታማኝ አምላክ በመሆኑ የተናገረውን በፍጹም ልብ ተቀብሎ በእግዚአብሔር የተስፋ ቃል ላይ ማረፍ ነው፤ 2ጢሞ. 2፥13፤ ቲቶ 3፥8። ስለዚህ ክርስቲያናዊ እምነት የሚመሠረተው በእግዚአብሔር ቃል ላይ ብቻ ነው፤ ሮም 10፥17። አብርሃም እግዚአብሔር የሰጠውን የተስፋ ቃል አመነ፤ እምነቱም ጽድቅ ሆኖ ተቈጠረለት፤ ዘፍ. 15፥6፤ ሮም 4፥16-21። በእምነትና በድፍረት መካከል ልዩነት አለ፤ ድፍረት ከእግዚአብሔር የተስፋ ቃል ውጭ እንዲሁ በዘፈቀደ ይሆናል የሚል አቋም መያዝ ሲሆን፥ እግዚአብሔር በሰጠው የተስፋ ቃል መተማመንና መደገፍ ግን እምነት ነው። እምነት በእግዚአብሔር ቃል ላይ ስለሚመረኰዝ፥ የእግዚአብሔር ቃል ወይም የክርስትና ትምህርት «እምነት» ወይም «ሃይማኖት» የሚለውን ስያሜ ይዟል፤ ይሁዳ 3። የክርስትና ሃይማኖት በሰው ነፍስ ውስጥ የሚተከለው፥ ሰው የሃይማኖት ዘር የሆነውን የወንጌል ቃል በእምነት ሲቀበል ነው። ይህም የወንጌል ቃል «ጌታ ኢየሱስ ክርስቶስ ኃጢአተኞችን ሊያድን መጣ።» የሚለው ሲሆን፥ ምእመኑም «ጌታዬ ኢየሱስ ክርስቶስ ለእኔ የሚገባውን ኵነኔ ወስዶ በእኔ ምትክ በመስቀል ላይ ስለተሰቀለ፥ በእግዚአብሔር ፊት ያለ ኵነኔ ነኝ» የሚል አቋም ይይዛል፤ ሮም 8፥1፤ 2ቆሮ. 5፥21፤ 1ቆሮ. 15፥3-4፤ ዮሐ. 3፥16።

እምነት ሁለት ነገሮችን ሊያመለክት ይችላል።

1. ስለ አምላክ ወይም ስለ ሰው ዕውቀት ወይም አሳብ። በዚህ ዓይነት ብዙ ሰዎች የኢየሱስን ተአምራት አይተው መሢሕ መሆኑን አመኑ፤ ነገር ግን በሕይወታቸው ለውጥ አይታይም፤ ዮሐ. 2፥23-25። እንደዚሁም አጋንንት እግዚአብሔር እንዳለ ያውቃሉ፤ ያዕ. 2፥19። ይህ ዓይነት እምነት የሞተ ነው፤ ሥራን አያስከትልም፤ ያዕ. 2፥17:26።

2. በአምላክ ወይም በሰው ፍጹም ተስፋ ማድረግ። ይህ ዓይነት እምነት ሥራን ያስከትላል። ብዙ ጊዜ መ.ቅ. እምነት ሲል ስለዚህ እውነተኛ እምነት ነው። ሰው በእምነት ሲኖር፥ በእግዚአብሔር ቃል ይመራል። ምንም እንኳን ነገሩ የማይቻል ወይም የማይሆን ቢመስልም፥ አማኙ ይታዘዛል፤ ሳይጠራጠርም ለእግዚአብሔር ክብር እየሰጠ እግዚአብሔር ቃሉን እስኪፈጽም ድረስ በተስፋ ይኖራል። የብ.ኪ. ሰዎች፥ በተለይም አብርሃም የእምነትን መንገድ አሳይተዋል፤ ሮም 4፥16-22፤ ዕብ. 11።

ሰዎች በአ.ኪ. ዘመን ክርስቶስ በኃጢአታቸው ምክንያት እንደሞተ እንደተነሣም አምነው ተጠመቁ፤ በዚህም መሠረት ሊኖሩ ጀመሩ፤ ሐ.ሥ. 2፥22-47፤ 16፥29-34። ሰው በልቡ ሲያምን ይጸድቃል፤ ሮም 4፥3-5፤ 10፥9-10፤ ገላ. 2፥16። የዘለዓለም ሕይወት ይኖረዋል፤ ዮሐ. 3፥16:36፤ መንፈስ ቅዱስንም ይቀበላል፤ ሐ.ሥ. 2፥38፤ 19፥2፤ ኤፌ. 1፥13። ሰው ወንጌልን ሰምቶ ያምናል ሆኖም በእምነት እያደገ ይሄዳል፤ ማር. 9፥24፤ ሮም 4፥19-21። ትልቅ እምነት፥ ጕድለት ያለበትም እምነት አለ፤ ማቴ. 8፥10፤ 14፥31፤ 17፥20። እምነት በመከራ ይፈተናል፤ 1ጴጥ. 1፥6:7፤ ያዕ. 1፥12። ሐዋርያት «እምነት ጨምርልን» ባሉ ጊዜ፥ ኢየሱስ የመጨመርን ጉዳይ ሳይሆን አስቀድሞ መሠረታዊ እምነት እንዲኖራቸው ነገራቸው፤ ሉቃ. 17፥5:6።

እምነት የእግዚአብሔር ስጦታ ነው፤ ከመንፈስ ቅዱስም ይገኛል፤ ገላ. 5፥23፤ ኤፌ. 2፥8፤ 2ተሰ. 2፥13። ሰው በእምነት ይጸድቃል፤ ሮም 3፥28፤ ገላ. 2፥16። ነገር ግን በእምነት ከክርስቶስ ጋር ስለሚተባበር፥ የእግዚአብሔርን ሥራ መሥራት ይጀምራል፤ ኤፌ. 2፥8-10። ስለዚህ ሰው እውነተኛ አማኝ መሆኑ የሚታወቀው በሥራው ነው፤ ያዕ. 2፥18-26።

**እረኛ**፤ በጎችና ፍየሎችን ከብቶችንም የሚያሰማራ (መዝ. 23፥2)፥ የጠፋውን የሚፈልግ (ሉቃ. 15፥3-7)፥ ከአውሬዎችም የሚጠብቅ (1ሳሙ. 17፥34:35)። አንዳንድ ጊዜ የዕብራውያን እረኞች መንጋቸውን በውሾች ያስጠብቁ ነበር፤ ኢዮብ 30፥1። እረኛ በጎቹን በስም ያውቃልና ከበረት ሲወጡ ይከተሉታል፤ ዮሐ. 10፥3:4። መልካም እረኛ ስለ መንጋው ነፍሱን እስኪሰጥ ድረስ ይጠብቃል፤ ዮሐ. 10፥11:15።

እረኛ ኀላፊነት ላለባቸው ሁሉ ምሳሌ ነውና፥ የእግዚአብሔርን ሕዝብ የማይጠብቁ ባለሥልጣኖች ከባድ ፍርድ ይኖርባቸዋል፤ ኤር. 23፥ 1-4፤ 25፥32-38፤ ሕዝ. 34፥1-10። እግዚአብሔር የሕዝቡ እረኛ ስለሆነ ሕዝቡን ይጠብቃል፤ መዝ. 23፥1፤ ሕዝ. 34፥11-24። በብ.ኪ. ስለ እግዚአብሔር አብ እረኝነት የተነገረው ሁሉ በአ.ኪ. ለክርስቶስ ተነግሯል። ይህም ክርስቶስ ራሱ እግዚአብሔር መሆኑን ያመለክታል፤ ዮሐ. 10፥14:15፤ ዕብ. 13፥20፤ 1ጴጥ. 2፥25።



እረኛ በጎቹን አስከትሎ ሲሄድ

**እሬት፥ እሬቶ**፤ በጣም የሚመር እንጨት። የመከራና የሞት ምሳሌ ሆኖ ተጠቅሷል፤ ኤር. 9፥15፤ 23፥15። ዮሐንስ በራእይ ያየው ኮከብ እሬቶ ተብሏል። ይህም መቅሠፍትንና ሕማምን ያመለክታል፤ ራእ. 8፥11።

**እርም**፤ ለእግዚአብሔር ተብሎ የተተወ ነገር። ኢያሱ በጦርነት ያገኘውን ምርኮ ሁሉ ለእግዚአብሔር እርም አደረገ፤ ኢያሱ 6፥18-21። «ምርኮ» ይመ.

**እርሳስ**፤ (እረር)፤ ከመሬት ተቆፍሮ የሚገኝ ክብደት ያለው ዐይነት ማዕድን። ጽሑፍ እንዳይጠፋ ለማድረግ የእርሳስ ጽላት በብረት መጻፊያ ይቀረጻል፤ ዘጸ. 15፥10፤ ኢዮብ 19፥24። ዛሬ ግን እርሳስ የምንለው መጻፊያ ከሌላ ዓይነት ማዕድን የሚሠራ ነው።

**እርሾ**፤ የአዲስ ሊጥ ማቡኪያ፥ የቆየ ሊጥ። እርሾ በፋሲካ ጊዜ ለእህል ቍርባን አልተፈቀደም፤ ዘጸ. 12፥15:20፤ ዘሌ. 2፥11። እርሾ ለእግዚአብሔር መንግሥት እንደዚሁም ለክፋት ምሳሌ ይሆናል፤ ማቴ. 13፥33፤ 16፥6፤ 1ቆሮ. 5፥6-8።

**እርቦ**፤ አንድ አራተኛ ወይም ከአራት አንድ ማለት ነው፤ ዘኍ. 23፥10።

**እርከን**፤ ወደላይ መወጣጫ፥ ደረጃ፤ 2ዜ.መ. 9፥18።

**እርኩም**፤ ሹል መንቁሪያ አፍ ያለው ትልቅ አሞራ፤ ዘሌ. 11፥17። «ወፎች» ይመ.

**እርያ**፤ (እሪያ)፤ ሰኰናው እንደ በሬ ስንጥቅ፥ ነገር ግን የማያመሰኳ፥ ለአይሁዶች ርኩስ የሆነ እንስሳ፥ አሳማ። በብዙ አገር የቤት እንስሳ በአፍሪቃ ግን የዱር አውሬ ነው፤ ዘሌ. 11፥7፤ ሉቃ. 8፥32፤ 15፥15፤ መዝ. 80፥13።



**እርዳታ (ርዳታ)**፤ ሰዎችን ለመርዳት ለቤተ ክርስቲያን የተሰጠ የጸጋ ስጦታ፤ 1ቆሮ. 12፥28። «ረዳት» ይመ.

**እርድ**፤ የተቀለበ የሥጋ ከብት፤ ዘፍ. 43፥16።

**እሳት**፤ በብ.ኪ. ዘመን ሁለት እንጨቶችን እርስ በእርስ በመሰበቅ ወይም ድንጋይና ድንጋይን እንዳንዱም ድንጋይን በብረት ላይ በመምታት እሳት ይገኝ ነበር። እሳት እንዳይጠፋ ሰዎች ይዘውት ይጓዙ ነበር፤ ዘፍ. 22፥6፤ ኢሳ. 30፥14። እሳት ለማብሰያ (ዮሐ. 21፥9)፥ ለማሞቂያ (ሉቃ. 22፥55)፥ ለማጥፊያ (ኢያሱ 6፥24)፥ ለብረት ማቅለጫ ይጠቅም ነበር፤ ዘጸ. 32፥24። እግዚአብሔር ብዙ ጊዜ ራሱን በእሳት ይገልጥ ነበር፤ ዘጸ. 3፥2፤ 13፥21፤ 19፥18፤ ሐ.ሥ. 2፥3። የመሠዊያ እሳት አይጠፋም ነበር፤ ዘሌ. 6፥13፤ 9፥24። እግዚአብሔር ካዘዘው በቀር ሌላ እሳት በማዕጠንት እንዲጨመር አልተፈቀደም፤ ዘሌ. 10፥1:2። እሳት ከሰማይ እየወረደ የአንዳንድ ሰዎችን መሥዋዕት ይበላ ነበር፤ 1ነገ. 18፥38፤ 2ዜ.መ. 7:1-3። እሳት የእግዚአብሔርን ክብር (ሕዝ. 1፥4:13)፥ ሕዝቡንም የመጠበቁን ሁኔታ ያመለክታል፤ 2ነገ. 6፥17። እሳት በምሳሌነት የእግዚአብሔርን ቅድስና፥ ጽድቅና ቍጣ ያሳያል፤ ዘዳ. 4፥24፤ ዘካ. 13፥9፤ ኢሳ. 66፥15:16፤ ዕብ. 12፥29። ደግሞም እሳት የፈተና (1ጴጥ. 1፥6:7)፥ የፍርድ ምሳሌ ነው፤ 1ቆሮ. 3፥12-15።

**እሴይ**፤ የኢዮቤድ ልጅ፥ የዳዊት አባት። አያቶቹም በዔዝና ሞዓባዊቷ ሩት ነበሩ፤ ሩት 4፥22። በቤተ ልሔም ኖረ፤ ስምንት ልጆችም ነበሩት፤ 1ሳሙ. 16፥1፤ 17፥12-14፤ 1ዜ.መ. 2፥12-17።

**እስማኤላውያን**፤ የእስማኤል ነገድ። ዮሴፍን ገዝተው ሸጡት፤ ዘፍ. 37፥25-28፤ 39፥1።

**እስማኤል**፤ ትርጕሙ «እግዚአብሔር ይሰማል» ማለት ነው። የሣራ ገረድ አጋር ለአብርሃም የወለደችለት ልጅ። አጋር ከፀነሰች በኋላ ሣራን አቃለለች። ሣራም እስክትሸሽ ድረስ አሠቃየቻት። እግዚአብሔር የአጋርን ችግር ሰምቶ የምትወልጅው ልጅ እስማኤል ተብሎ ይጠራ አላት፤ ዘፍ. 16፥1-16። እስማኤል 13 ዓመት በሆነው ጊዜ ተገረዘ፤ ዘፍ. 17፥23-27። እንደ እግዚአብሔር የተስፋ ቃል ይስሐቅ ከተወለደ በኋላ እስማኤል በሕፃኑ ቀንቶ ሳቀ (ገላ. 4፥29)፤ አሳደደውም። እግዚአብሔር እንዳዘዘው አብርሃም አጋርንና እስማኤልን አሳደደ።

እግዚአብሔር እስማኤልን በሕይወት ጠበቀው፤ ዘፍ. 21፥8-21። በኋላም ከወንድሙ ከይስሐቅ ጋር አባቱን ቀበረ፤ ዘፍ. 25፥9። እግዚአብሔር ስለ እርሱ እንደተናገረው (ዘፍ. 17፥20) የትልቅ ሕዝብ አባት ሆነ፤ ዘፍ. 25፥12-18። ጳውሎስ ሕግን በመጠበቅ ራሳቸውን ለማጽደቅ የሚያስቡትን በአጋርና በእስማኤል መስሎ ተናገረ፤ ገላ. 4፥21-31። ዛሬ ዐረቦች እስማኤልን እንደ አባታቸውና እንደ ተስፋ ልጅ አድርገው ይቈጥሩታል። በዚህ ስም ሌሎች አምስት ሰዎች ተጠርተውበታል።

**እስራኤል**፤ 1. የአብርሃም የልጅ ልጅ ያዕቆብ ከእግዚአብሔር ጋር ታግሎ ካሸነፈ በኋላ «ካልባረከኸኝ አልለቅህም» ባለ ጊዜ እግዚአብሔር «እስራኤል» ብሎ ሰየመው። ትርጓሜውም «ከእግዚአብሔር ጋር ይታገላል፤ ያሸንፍማል» ማለት ነው፤ ዘፍ. 32፥22-32።

2. ከያዕቆብ ዐሥራ ሁለት ልጆች የተገኙት «እስራኤል» (ዘፍ. 49፥7፤ ዘጸ. 14፥30)፥ «የእስራኤል ልጆች» (ዘጸ. 3፥9)፥ ወይም «ዐሥራ ሁለት የእስራኤል ነገዶች» (ዘፍ. 49፥28) ይባላሉ።

3. ከሰሎሞን ዘመን በኋላ ከነገዶቹ ዐሥሩ በሮብዓም ላይ ባመፁ ጊዜ ያቋቋሙአት ሰሜናዊት መንግሥት እስራኤል ተባለች፤ 1ነገ. 12፥16:17። ይህችም ሰሜናዊት መንግሥት እስከ 200 ዓመት ብቻ ጸንታ በአሦር ንጉሥ እጅ ወደቀች፤ 2ነገ. 17። «የእስራኤል መንግሥት» ይመ.

4. ከልዩ ልዩ ነገዶች በተለይ ከይሁዳና ከብንያም ነገዶች ከምርኮ የተመለሱት እስራኤላውያን ብዙ ጊዜ አይሁድ ይባሉ ነበር (ዕዝ. 1፥5፤ 5፥1፤ ማቴ. 2፥1)፥ ደግሞም በጥንት ስማቸው እስራኤል ተብለው ይጠሩ ነበር፤ ዕዝ. 2፥2፤ ዘካ. 9፥1፤ ሚል. 1፥1፤ 2፥11፤ ማቴ. 2፥20።

5. «ከእስራኤል የሚወለዱ ሁሉ እስራኤል አይደሉም» እንደተባለው (ሮም 9፥6፤ 2፥28:29)፥ «የእግዚአብሔር እስራኤል» የአብርሃምን የእምነት ፍለጋ የሚከተሉ ናቸው፤ ሉቃ. 19፥8:9፤ ሮም 4፥12። ይህም ማለት ከአይሁድ ብቻ ሳይሆን፥ ከማንኛውም ሕዝብ በክርስቶስ በማመን አዲስ ፍጥረት የሆኑ ሁሉ ማለት ነው፤ ገላ. 3፥6-14:29፤ 6፥15:16፤ 2ቆሮ. 5፥17፤ መዝ. 73፥1፤ ኢሳ. 56፥8 እና ዮሐ. 10፥16፤ ዮሐ. 1፥48፤ ራእ. 7፥9።

**የእስራኤል መንግሥት**፤ ሙሴ ቤተ እስራኤልን ከግብጽ እስከ ዮርዳኖስ መራቸው። ኢያሱ ወደ ከነዓን አገባቸው። በመሳፍንት፥ በሳሙኤልና በሳኦል እየተመሩና ከጠላቶቻቸው ጋር እየተዋጉ በከነዓን ኖሩ። ዳዊት ጠላቶችን ሁሉ አሸነፈ። ኢየሩሳሌምን ይዞ መናገሻ ከተማ አደረገ። መንግሥቱንም አስፋፋ። ሰሎሞንም መንግሥቱን በንግድ አበለጸገ፤ በጥበብም አሳወቀ። ነገር ግን በሕዝቡ ላይ አገዛዙን በማክበድ መንግሥቱን አደከመ፤ ሰሎሞን ከሞተ በኋላ እንደ አኪያ ቃል ዐሥሩ ነገዶች በሮብዓም ላይ ዐምፀው ኢዮርብዓምን አነገሡ። መንግሥቱ ብዙ ጊዜ በእስራኤል ስም አንዳንድ ጊዜም ከዐሥሩ ነገዶች ዋና በሆነው በኤፍሬም ስም ይጠራ ነበር። የእስራኤል ሕዝብ ወደ ኢየሩሳሌም እንዳይወጡ ኢዮርብዓም የወርቅ ጥጃዎችን ሠርቶ በቤቴልና በዳን አኖራቸው። የእስራኤል ነገሥታት ሁሉ ይህን ኃጢአት ተከትለው ብዙ ባዕድ አምልኮት ፈጸሙ። በተለይም የበአልን ጣዖት ሠርተው አመለኩ።

እግዚአብሔር ነቢያትን ለእስራኤል ላከ። ከእነርሱም የታወቁት ኤልያስ፥ ኤልሳዕ፥ አሞጽና ሆሴዕ ናቸው። እስራኤል ግን ወደ እግዚአብሔር ስላልተመለሱ፥ መጀመሪያ በሶርያውያን፥ ቀጥሎም በአሦራውያን ተወረሩ። የአሦር ነገሥታት ቴልጌል ቴልፌልሶርና ስልምናሶር እስራኤላውያንን ወደ አሦር አፈለሱ። በመጨረሻ የአሦር ንጉሥ ሰማርያን ይዞ መንግሥትን አስቀረ። በእስራኤላውያን ፈንታ ሌላ የምሥራቅ ሕዝብ በአገራቸው አሰፈረ፤ ዕዝ. 4፥2:10። ስለ እስራኤል ነገሥታት ዝርዝርና ዘመነ መንግሥት «የይሁዳ መንግሥት» ይመ.

ከዚህ በኋላ የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደነፆር የይሁዳን አገር ነዋሪዎች አፈለሰ። በምርኮ ሳሉ ሕዝቅኤልና ዳንኤል ትንቢት ተናገሩ። እነዘሩባቤል በቂሮስ አዋጅ መሠረት ከባቢሎን ወደ ኢየሩሳሌም ተመለሱ። ከተመለሱት የሚበዙት ከይሁዳ ነገድ ነበሩ። ሲመለሱ፥ ልዩ ነገድነታቸው በአስተዳደር በኩል ልዩነትን አላመጣምና ሁሉም እስራኤል ተባሉ («ነገድ» ይመ.)። ተመልሰውም በሐጌና በዘካርያስ ቀስቃሽነት ቤተ መቅደስን ሠሩ። በዕዝራና በነህምያ ጊዜ የኢየሩሳሌም ቅጥር ተሠራ፤ የአይሁድ ሥርዓት ጸና። ሆኖም እስራኤል መጀመሪያ በፋርስ፥ በኋላ በግሪክ፥ ቀጥሎም በሮም ግዛት ሥር ዋለች። የሮም መንግሥት በ70 ዓ.ም. ኢየሩሳሌምን አፈረሰ። ቤተ እስራኤልም ተበታተኑ።

ብዙ እስራኤላውያን ከባቢሎን ምርኮ በኋላ ወደ አገራቸው አልተመለሱም፥ ስለዚህም በየአገሩ ምኵራብ እየሠሩ ሃይማኖታቸውን ይጠብቁ ነበር። ሐዋርያት እየተዘዋወሩ ወንጌልን ሲያስፋፉ አስቀድመው በእስራኤል መካከል ሰበኩ። ከእስራኤል ብዙዎች አመኑ። ግን በጠቅላላው አስተያየት እስራኤል ወንጌልን አልተቀበሉም። ሆኖም ጳውሎስ በሮም. ም. 11 ወንጌል በአሕዛብ ከተስፋፋ በኋላ ከእስራኤል ብዙዎች እንደሚድኑ መተንበዩን ብዙ ሊቃውንት ይተረጕሙታል።

**እስቤት**፤ «እንስሳት» ይመ.

**እስታቴር**፤ የሮም መንግሥት ብር ምንዛሪ፤ ማቴ. 17፥27። «ገንዘብ» ይመ.

**እስኩቴስ**፤ ከአሦር በስተሰሜን ይኖር የነበረ ያልሠለጠነ ዘላን ሕዝብ፤ ቆላ. 3፥11።

**እስጢፋኖስ**፤ በኢየሩሳሌም ቤ. ክ. ከተሾሙት ሰባት አገልጋዮች አንዱ ነበረ። ብዙ ተአምራትን አደረገ። ከግሪክ አገር የመጡ አይሁድ ሲከራከሩት መልስ አሳጣቸው። በሸንጎ ፊት በሐሰት ከሰሱት፤ ሸንጎውም በድንጋይ እንዲወገር ፈረደበት። እስጢፋኖስ ስለ ክርስቶስ በመጀመሪያ የተገደለ ሰማዕት ነው። ጳውሎስ በእስጢፋኖስ ሞት ተስማምቶ ነበር። እስጢፋኖስ በሚሞትበት ጊዜ ኢየሱስ እንደጸለየው፥ ክፉ ላደረጉበት ጸለየላቸው። «ጌታ ኢየሱስ ሆይ፥ ነፍሴን ተቀበል» በማለቱም የኢየሱስን ከአብ ጋር እኩልነት መሰከረ፤ ሐ.ሥ. 6-7።

**እስክንድር**፤ ታላቁ እስክንድር የመቄዶንያ ንጉሥ የፊልጶስ ልጅ። ከ336-323 ከክ. ል. ነገሠ። የፋርስን መንግሥት ድል ነሥቶ እጅ አደረገው። ሲሞት መንግሥቱ በጦር መሪዎቹ ተከፈለ። ዳንኤል ስለዚህ ተነበየ፤ ዳን. 8፥21:22።

**እስክንድርያ**፤ በ332 ከክ. ል. በታላቁ ባሕር ዳር በታላቁ እስክንድር የተቈረቈረ የግብጽ ወደብ፤ ሐ.ሥ. 27፥6፤ 28፥11። የንግድ ሥራና የዚያ ዘመን

ትምህርት እጅግ በጣም የተስፋፋበት የግብጽ መናገሻ ከተማ ሆነ። ብዙ አይሁድ በእስክንድርያ ታላላቅ ምኩራቦች ሠሩ፤ ሐ.ሥ. 6፥9። የግብጽ ሰዎች በበዓለ ኀምሳ ቀን በኢየሩሳሌም ነበሩ። ከዚያን ጊዜ ጀምሮ የክርስትና ሃይማኖት ወደ እስክንድርያ እንደገባ ይታመናል፤ ሐ.ሥ. 2፥10። አጵሎስም የእስክንድርያ ሰው ነበረ፤ ሐ.ሥ. 18፥24። ከዚህ በቀር ቤ.ክ. በእስክንድርያ እንዴት እንደተቋቋመች መ.ቅ. አይገልጥም። በተለይ ግን ማርቆስ በእስክንድርያ እንደሠራ በቤ. ክ. ታሪክ ተጽፏል። «የቅዱሳት መጻሕፍት ትርጉም» ይመ.። ካ. 7ተ።

**እስያ፤** 1. እስያ ከአውሮፓ በስተምሥራቅ ያለው ክፍለ ዓለም ነው።

2. ትንሹ እስያ በጥቁር ባሕርና በታላቁ ባሕር መካከል ይገኛል። ዛሬ ቱርክ ይባላል።

3. አዲስ ኪዳን እስያን ሲጠቅስ ከትንሹ እስያ በስተደቡባዊ ምዕራብ ስላለው የሮም ጠቅላይ ግዛት ይናገራል። በዮሐንስ ራእይ ለሰባቱ የእስያ አብ. ክ. መልእክት ተጻፈ፤ ራእ. 1፥11። የእስያ መናገሻ ከተማ ኤፌሶን ነበረች። ጳውሎስ እዚህ ወንጌልን አስተማረ፤ ሐ.ሥ. 19። ካ. 6ቀ።

**እሸት፤** የበሰለና የጐመራ የእህል ፍሬ። ሰው ከባልንጀራው እርሻ ውስጥ ገብቶ በማጭድ ሳይሆን፥ በእጁ ቀጥፎ እሸት መብላት በሙሴ ሕግ የተፈቀደ ነበር፤ ዘዳ. 23፥25። ፈሪሳውያን ይህን እንደ ሥራ ስለቈጠሩት፥ በሰንበት እሸት እንዳይቀጠፍ ከለከሉ፤ ማቴ. 12፥1:2።

**እሾህ፤** በከነዓን ብዙ ዓይነት እሾህ ይገኛል። ለእሳት መነሾ ምክንያት ነው (ዘጸ. 22፥6፤ ኢሳ. 10፥17)፤ ለአጥር ያገለግላል፤ ምሳ. 15፥19። የክፉ ሰዎች ምሳሌ ነው፤ ዘኍ. 33፥55፤ ናሆም 1፥10። እሾህ የሰውን ሥራ ከንቱ ሊያደርግ ይችላልና እንቅፋት ነው፤ ዘፍ. 3፥18፤ ምሳ. 24፥31፤ ኤር. 12፥13፤ ማቴ. 13፥7። ወታደሮች የእሾህ አክሊል በክርስቶስ ራስ ላይ አኖሩ፤ ማቴ. 27፥29።

**እቅፍ፤** ጭንና ደረት፥ እንዲሁም የእጆችና የደረት ክበብ። ቃሉ መቀራረብንና ፍቅርን ያመለክታል፤ ሉቃ. 16፥22፤ ዮሐ. 1፥18፤ 13፥23።

**እባብ፤** እግር የሌለው፥ በሆዱ የሚሄድ፥ መርዛም የሆነ የሰው ጠላት፥ ተንኰለኛ አውሬ። ሰይጣን በእባብ ተመስሎ ሔዋንን አታለለ፤ ዘፍ. 3፥1-5:14:15፤ ራእ. 20፥2። እግዚአብሔር የሙሴን በትር ወደ እባብነት ለመለወጥና ሕዝቡንም ለመቅጣት ተናዳፊ እባብ ላከባቸው፤ ዘጸ. 4፥2-5፤ 7፥10-12፤ ዘኍ. 21፥6። ደግሞም የጥበብ ምሳሌ ነው፤ ማቴ. 10፥16።

**እባብ፤** የናስ እባብ፤ እስራኤል በምድረበዳ ሳሉ በማጕረምረማቸው ምክንያት በእባብ መቅሠፍት ተቀጡ። በኋላ ግን ሙሴ የናስ እባብ ሠርቶ በዓላማ ላይ እንዲሰቅል ታዘዘ፤ እባብም የነደፈው ሁሉ የናሱን እባብ ባየ ጊዜ ዳነ፤ ዘኍ. 21፥4-9። ከዚያም በኋላ



እስራኤል የናሱን እባብ አመለኩ። ሕዝቅያስ ግን «ነሑሽታን» ብሎ ሰባበረው። ነሑሽታን ማለት ነሐስ ብቻ ማለት ነው፤ 2ነገ. 18፥4። ክርስቶስ የራሱን ስቅለት ከናስ እባብ መሰቀል ጋር አነጻጽሮ አስተማረ፤ ዮሐ. 3፥14:15።

**እባጭ፤** እንደ መ.ቅ. አባባል ቃሉ በሥጋ ቍርበት ላይ የሚታይ ማናቸውንም ዓይነት እባጭ ያመለክታል፤ 2ነገ. 20፥7፤ ኢሳ. 1፥6። «በሽታ» ይመ.

**እብሪት፤** የኃይልና የክፋት ሥራት። ሌላው ክፉ እንዳደረገ እኔም ሳድርግ ማለት እብሪት ነው፤ ምሳ. 8፥13።

**እቴጌ፤** 1. የንጉሥ ሚስት። 2. የንጉሥ እናት። የእስራኤል ነገሥታት ብዙ ሚስቶችን ያገቡ ነበርና የንጉሡ እናት ከሴቶች ሁሉ እንደ ታላቅ ሆና ትቈጠር ነበር፤ 1ነገ. 2፥19፤ 15፥13፤ ኤር. 13፥18።

**እትብት፤** ፅንስ በማኅፀን ከእናቱ ሆድ ምግብን የሚቀበልበት ከፅንሱ ጋር የተያያዘ መረብ። ሕፃኑ ሲወለድ እትብቱ ይቈረጣል፤ ሕዝ. 16፥4።

**እቶን፤** በጥንት ዘመን እቶን በጭቃ የተለሰነ ጕድጓድ ነበረ። ሰዎች በውስጡ እሳት ካነደዱ በኋላ በዳር በዳሩ ሊጥ በማስቀመጥ ዳቦ ያበስሉ ነበር፤ ዘሌ. 2፥4። አንዳንድ እቶን ሰፊ ነበረና ጡብ ይሠራበት ወይም ማዕድናት ይቀልጡበት ነበር፤ ዘዳ. 4፥20፤ ራእ. 9፥2። በባቢሎን ሰዎች በእቶን ውስጥ እየተጣሉ ይቀጡ ነበር፤ ዳን. 3፥6:19-23። እቶን የፈተናና የፍርድ ምሳሌ ነው፤ ኢሳ. 48፥10፤ ማቴ. 13፥42።

**እኅት፤** በወላጆች አንድ የሆነች፥ ደግሞም በሥጋና በመንፈስ ወይም በሥራ የወዳጅነትና የመረዳዳት አንድነት ያላት እኅት ትባላለች። እኅትነት በምንና በምን እንደሆነ እንደሚከተለው እንመለከታለን። 1. በአባት ወይም በእናት በኩል (ዘፍ. 20፥12)፥ 2. በሚስትነት (መ.መ. 4፥9)፥ 3. በአገር (ዘኍ. 25፥18)፥ 4. በጐሳ (ኤር. 3፥7)፥ 5. በክርስቶስ (ሮም 16፥1)።

**እኅት ሚስት፤** እኅትነት ያላት ሚስት፤ ሁለት ወንድና ሴት ክርስቲያኖች ከጋቡ በፊት ወንድም-እኅት ይባባላሉ። እነዚህ ሰዎች ሲጋቡ «እኅት ሚስት-ባል ወንድም» ይባላሉ፤ 1ቆሮ. 9፥5።

**እናት፤** የወለደች ተንከባክባና መግባ ያሳደገች፥ ደግሞም በሥጋና በመንፈስ የእናትነትን ሥራ የፈጸመች። ቃሉ የሚከተሉትን አሳቦች ያመለክታል። 1. በሥጋ ወላጅ፥ 2. በትውልድ የምትገኝ የቅርብ ወይም የሩቅ ወላጅ (ዘፍ. 3፥20)፥ 3. በመንፈስም በሥጋም ምእመናንን የምትረዳ (ሮም 16፥13)፥ 4. በምድራዊት ኢየሩሳሌም (ጽዮን) አንጻር ሰማያዊት ኢየሩሳሌም፤ መዝ. 87፥5፤ ገላ. 4፥26። «ወላጅ» ይመ.

**እንስላል፤** እየተቀቀለ ለምግብና ለመድኃኒት የሚሆን ተክል፤ ማቴ. 23፥23።

**እንስሳት፤** 1. በመሬት ላይ የሚኖሩ እንስሳት፥ አውሬዎችና የምድር ተንቀሳቃሾች የሚከተሉት ናቸው ፦ ሙጭልጭላ (ዘሌ. 11፥29)፥ ሚዳቋ (ኢሳ. 51፥20)፥ ሽኮኮ (መዝ. 104፥18)፥ ቀበሮ (መሳ. 15፥4)፥ በራይሌ (ዘዳ. 14፥5)፥ በቅሎ (2ሳሙ. 13፥29)፥ በግ፥ ጠቦት (ዘፍ. 4፥2፤ 27፥9)፥ ብሖር (መዝ. 18፥33)፥ ተኩላ (መዝ. 91፥13)፥ ነብር (ኤር. 13፥23)፥ አህያ፥ ውርንጫ (ዘፍ. 12፥16፤ ማር. 11፥2)፥ አርጃኖ (ዘሌ. 11፥30)፥ አቆስጣ (ዘጸ. 25፥5)፥ አንበሳ (1ሳሙ. 17፥34)፥ አይጥ (ዘሌ. 11፥29)፥ አዞ (ኢዮብ 40፥25)፥ አጋዘን (ዘዳ. 14፥5)፥ አጭ (ዘዳ. 14፥5)፥ ኤሊ (ዘሌ. 11፥30)፥ እርያ (ዘሌ. 11፥7፤ ሉቃ. 15፥15)፥ እስስት (ዘሌ. 11፥30)፥ እንሽላሊት (ዘሌ. 11፥29)፥ እባብ (ዘጸ. 7፥10)፥ እፉኝት (ዘዳ. 32፥33)፥ ከብት፥ ላም፥ በሬ፥ እምቦሳ፥ ኮርማ፥ ወይፈን፥ ጊደር፥ ጥጃ፥ ፊሪዳ (ዘሌ. 22፥28፤ ዘጸ. 20፥17፤ መዝ. 69፥31፤ ኢዮብ 21፥10፤ ኤር. 50፥27፤ ኢሳ. 7፥21፤ ዘፍ. 18፥7፤ ሉቃ. 15፥23)፥ ዋላ (መዝ. 104፥18)፥ ውሻ (ኢሳ. 56፥10)፥ ዝሆን (1ነገ. 10፥18)፥ ዘንዶ (መዝ. 91፥13)፥ ዝንጀሮ (1ነገ. 10፥22)፥ የሌሊት ወፍ (ዘሌ. 11፥19)፥ የሜዳ አህያ (ኢዮብ 39፥5)፥ የበረሀ ፍየል (ኢዮብ 39፥1)፥ የዱር እርያ (መዝ. 80፥13)፥ ድብ(1ሳሙ. 17፥34)፥ ድኩላ (ዘዳ. 14፥5)፥ ጃርት (ኢሳ. 14፥23)፥ ገበሎ (ዘሌ. 11፥30)፥ ጉማሬ (ኢዮብ 40፥15)፥ ግመል (ዘፍ. 24፥10)፥ ጎሽ (ኢዮብ 39፥9)፥ ጓጉንቸር (ዘጸ. 8፥2)፥ ጥንቸል (ዘሌ. 11፥6)፥ ፈረስ (1ነገ. 4፥26)፥ ፍልፈል (ኢሳ. 2፥20)፥ ፍየል (ዘጸ. 12፥5፤ ዕብ. 9፥12)።

2. በውሃ ውስጥ የሚኖሩ እንስሳት ፦ ሰፍነግ (ማቴ. 27፥48)፥ አንበሪ (ዘፍ. 1፥21)፥ ዓሣ (ዘፍ. 1፥26)፥ ዛጎል (ዘጸ. 30፥34)። «ርኩስ» ይመ.

**እንስሶች፤** አራት እንስሶች። «ኪሩብ» ይመ.

**እንሽላሊት፤** «እንስሳት» ይመ.

**እንቅልፍ፤** 1. የድካም ማሳረፊያ ዕረፍት፤ መዝ. 4፥8፤ 127፥2። 2. ሞትን ያመለክታል፤ ዮሐ. 11፥11-14፤ 1ቆሮ. 11፥30፤ 1ተሰ. 4፥13። 3. የመንፈሳዊ ስንፍና ምሳሌ ነው፤ ማቴ. 25፥5፤ ሮም 13፥11።

**እንቆቅልሽ፤** የሰው ጥበብ መፈተኛ ተረት፥ ጨዋታ ወይም ምሳሌ፤ መሳ. 14፥12-19፤ 1ነገ. 10፥1።

**እንቢተኛ፤** እልኸኛ፤ ዓመጸኛ፤ ዘጸ. 16፥28፤ ዕብ. 12፥25፤ ያዕ. 3፥6።

**እንባ፤** ሰው በሚያጋጥመው ሁኔታ በአግባቡ አዝኖ እንባ ያፈሳል፤ ኢዮብ 16፥20፤ ዮሐ. 11፥35።

**እንክርዳድ፤** በስንዴ መካከል የሚበቅልና የሚያፈራ፥ ሲበሉት ራስን የሚያዞር መርዝነት ያለው አረም። የሰይጣን ልጆች ምሳሌ፤ ማቴ. 13፥25:39።

**እንኮይ፤** ፍሬው የሚበላ፥ በቆላ የሚበቅል ዛፍ፤ ዘፍ. 30፥14-17፤ ምሳ. 25፥11፤ መ.መ. 2፥3።

**እንድርያስ፤** ከዐሥራ ሁለቱ ሐዋርያት አንዱ፤ ማቴ. 10፥2። እንደ ወንድሙ ጴጥሮስ ዓሣ አጥማጅ ነበረ። እንድርያስ የመጥምቁ ዮሐንስ ደቀ መዝሙር ሳለ፥ ዮሐንስ ኢየሱስን አሳይቶት ከኢየሱስ ጋር ዋለ። ጴጥሮስንም ወደ ኢየሱስ አመጣው፤ ዮሐ. 1፥35-46። ዓሣ ከሚያጠምድበት ቦታ ኢየሱስ ጠራው፤ ማር. 1፥16:17። ኢየሱስን ሲያገለግል አምስት እንጀራ የያዘውን ብላቴናና፥ ግሪኮችንም ወደ ኢየሱስ አደረሰ፤ ዮሐ. 6፥8:9፤ 12፥21:22። ስለ ኢየሩሳሌም መፍረስ ከጠየቁት ደቀ መዛሙርት አንዱ ነበረ፤ ማር. 13፥3:4። ከዕርገት በኋላ ከሌሎች ጋር የመንፈስ ቅዱስን ተስፋ ጠብቆ ተቀበለ፤ ሐ.ሥ. 1፥13። «ሐዋርያ» ይመ.

**እንዶድ፤** በአማርኛ ልብስን የሚያነጣ የሐረግ ፍሬ። በመ.ቅ. የተጠቀሰው ግን አንድ የጨው ዐይነት ነው። ይህም ከመሬት ይሰበሰብና በአረፋው ውስጥ ልብስ ይታጠባል፤ ኤር. 2፥22።

**እንጀራ፤** እስራኤላውያን ከስንዴና ከገብስ ዱቄት እንጀራ ይጋግሩ ነበር። አንዳንድ ጊዜም ባቄላ፥ ምስር፥ ጤፍና አጃ በአንድነት ይጋግራሉ፤ ሕዝ. 4፥9። እንጀራውን በጨው ያጣፍጣሉ፤ ዘሌ. 2፥13። እርሾም ይጨመር ነበር፤ ሉቃ. 13፥21። ያለ እርሾ ሲጋገር ቂጣ ይባላል፤ ዘጸ. 12፥15። እንጀራ በምድጃ ወይም በእቶን ይጋገር ነበር፤ ዘሌ. 2፥4። በግብጽ የንጉሥ እንጀራ አበዛ (ጋጋሪ) ትልቅ ማዕርግ ነበረው፤ ዘፍ. 40፥1:16። መልከ ጼዴቅ ለአብርሃም እንጀራ አቀረበ (ዘፍ. 14፥18)፤ ካህናትም በመቅደስ በየሳምንቱ እንጀራ ያቀርቡ ነበር፤ ዘሌ. 21፥6፤ 24፥5-9። እንጀራ ሲባል ብዙ ጊዜ ጠቅላላውን ምግብ ያመለክታል፤ ዘፍ. 3፥19፤ ማቴ. 6፥11። ክርስቶስ ሕይወትን ስለሚሰጥ «የእግዚአብሔር እንጀራ» እና «የሕይወት እንጀራ» ብሎ ራሱን አመለከተ፤ ዮሐ. 6፥33:35።

**እንጉልቻ፤** ሳይተኙ እንደተቀመጡ የሚታይ አነስተኛ እንቅልፍ። የስንፍና ምሳሌ ነው፤ ምሳ. 6፥4።

**እንግዳ፤** ከሌላ ወገን የመጣ በእስራኤል

መካከል የሚኖር ሰው። ፋሲካን ለመብላት (ዘጸ. 12፥43)፥ ወደ መቅደስ ለመግባት (ሕዝ. 44፥9)፥ ንጉሥ ለመሆን (ዘዳ. 17፥15)፥ ወይም ቢጋብቻ ከእስራኤል ጋር ለመቀላቀል ለእንግዳ አይፈቀድም ነበር፤ ዘጸ. 34፥12-16። ሕግን ቢቀበልና ቢገረዝ ግን እንደ አገር ልጅ ይሆናል፤ ዘጸ. 12፥48። በአ. ኪ. ከእግዚአብሔር ቃል ውጭ የሆነ ሰው እንግዳ ይባላል፤ ኤፌ. 2፥19። እንደዚሁም ክርስቲያን በዚህ ዓለም እንግዳ ነው፤ ዕብ. 11፥13-16፤ 1ጴጥ. 2፥11።

**እንግዳ ተቀባይነት**፤ እንግዶችን መቀበል በብሉይና በአዲስ ኪዳን ታዝዟል፤ ዘሌ. 19፥34፤ ሮም 12፥13፤ 1ጴጥ. 4፥9። አብርሃም እንግዶችን አክብሮ አስፈላጊውን ነገር ሁሉ በፍጥነት በማዘጋጀቱ ከፍ ያለ ምሳሌ አሳይቷል፤ ዘፍ. 18፥1-8፤ ሉቃ. 7፥44-46። እንግዳ እስኪሄድ ድረስ ባለቤት ለእርሱ ኀላፊ ነው፤ ዘፍ. 19፥1-8፤ መሳ. 19፥1-23። ኢየሱስ ሰዎችን በመመገብ ምሳሌ ሰጠን፤ ማቴ. 14፥15-21። በተለይ የወንጌል ሠራተኞችን መቀበል ይገባልና፥ የሚቀበሉአቸው ዋጋቸውን አያጡም፤ 2ነገ. 4፥8-37፤ ማቴ. 10፥40-42፤ ዕብ. 13፥1:2፤ 3ዮሐ. 5-8 እና 2ዮሐ. 10 ያነጻጽሩ። ክርስቶስ በፍርድ ቀን በተናገረው ላይ ተመርኩዞ ከቀረቡት ስድስት ጥያቄዎች አንዱ እንግዳ መቀበልን የሚመለከት ነው፤ ማቴ. 25፥35:38:43።

**እንግጫ**፤ በወንዝ ዳር የሚበቅል ለምለም ሣር፤ ኢሳ. 19፥15፤ 58፥5።

**እንጎቻ**፤ ትንሽ ቂጣ ወይም ትንሽ እንጀራ፤ ዘጸ. 29፥2፤ 1ነገ. 17፥13።

**እንጥሽታ**፤ ከትንፋንና ከአንድ ዓይነት ብናኝ ነገር የተነሣ ማነጠስ። የኃይል ጩኸትን ያመለክታል፤ ኢዮብ 41፥10።

**እከክ**፤ የሚያሳክክ የቆዳ በሽታ፤ ዘሌ. 21፥20። «በሽታ» ይመ.

**እከት**፤ የስደተኛ ወይም የመንገደኛ ጓዝ ሸክም። ሕዝቅኤል እከት በመሸከም የእስራኤልን ስደት ተነበየ፤ ሕዝ. 12፥3-16።

**እውነት**፤ ትክክለኛና ስሕተት የሌለበት ቃል፥ የውሸት ተቃራኒ። የእግዚአብሔር ቃል እውነት ነው፤ ቲቶ 1፥1:2፤ ዮሐ. 17፥17። እግዚአብሔር እውነትን ለሰው ገልጧል (ሮም 1፥19:20)፥ በተለይ ክርስቶስ የእውነት መግለጫ ነው፥ እርሱ ራሱ እውነት ነውና፤ ዮሐ. 1፥14:17፤ 14፥6። በክርስቶስ የተገለጠውን እውነት፥ ማለት የወንጌልን ቃል የሚቀበል ሕይወትን ያገኛል፤ ዮሐ. 8፥31:32። የማያምኑት ግን በሐሰት ይኖራሉ፤ ይፈረድባቸውማል፤ 2ተሰ. 2፥9-13።

**እዝናት**፤ የተግሣጽ ምክር፤ መሳ. 20፥7።

**እዝን እንጀራ (የ)**፤ በእስራኤልና በኢትዮጵያ ልማድ ሰው በሞተ ጊዜ ኀዘንቤት ወደ ሟቹ ቤት የሚወሰደው ምግብ የእዝን እንጀራ ይባላል፤ ኤር. 16፥7፤ ሕዝ. 24፥17።

**እድሜ**፤ ሰው በሕይወት የሚቆይበት ጊዜ። ረጅም እድሜ የእግዚአብሔር በረከት ነው፤ መዝ. 91፥16። እንደሚገባ የሚታዘዙ የረጅም እድሜ ተስፋ አላቸው፤ ዘጸ. 20፥12። በአባቶች ዘመን ሰዎች ብዙ ዓመታት በሕይወት ይኖሩ ነበር፤ ዘፍ. 5፤ ዘዳ. 34፥7። «የብሉይ ኪዳን ስፍረ ዘመን» ይመ.። በኋላ ግን የሰው እድሜ ከ70 እስከ 80 ዓመታት ገደማ ተወሰነ፤ መዝ. 90፥9:10። ሰው በእድሜ የሸመገሉትን እንዲያከብር ታዝዟል፤ ዘሌ. 19፥32።

**እድሞ**፤ በቤት ወይም በቤ.ክ. ዙሪያ የሚሠራ አጥር፥ ቅጥር፤ አብዛኛውን ጊዜ በዐፈርና በድንጋይ ይሠራል፤ ራእ. 11፥2።

**እድሳት**፤ ያረጀ ሕንፃ ማደስ፥ መጠገን፤ ነህ. 3፥9-32። ኃጢአት፥ ድካምና እርጅና ወደ ዓለም ስለገቡ እግዚአብሔር ሁሉን ያድሳል፤ ኢሳ. 42፥9፤ ራእ. 21፥5። ይህ በተለይ የሚታየው በጠቅላላው ፍጥረት (ኢሳ. 65፥17፤ ዕብ. 1፥10-12፤ ራእ. 21፥1) እና በሰው ዘንድ ነው፤ መዝ. 103፥5፤ ኢሳ. 40፥31፤ ሕዝ. 36፥26፤ 2ቆሮ. 5፥17።

**እድገት (ዕድገት)**፤ ሰው በአካልም ሆነ በመንፈስ ሊያድግ ይችላል፤ ዘፍ. 21፥8፤ ዘጸ. 2፥10፤ ሉቃ. 1፥80፤ 2፥40:52። ማናቸውም ሕያው ነገር ያድጋል፤ መሳ. 16፥22፤ ማቴ. 6፥28፤ 13፥30፤ ማር. 4፥8። ቤተ ክርስቲያን በአንድነት (1ቆሮ. 3፥6፤ ኤፌ. 2፥21)፥ ክርስቲያንም በእምነት፥ በነገር ሁሉ ክርስቶስን ለመምሰል፥ በእግዚአብሔር ዕውቀት፥ ለመዳን ማደግ አለበት፤ 2ቆሮ. 10፥15፤ ኤፌ. 4፥15፤ ቆላ. 1፥10፤ 1ጴጥ. 2፥2፤ 2ጴጥ. 3፥18።

**እጅ**፤ ቃሉ ብዙ ጊዜ ኃይልን (ዘፍ. 9፥2:5፤ ሉቃ. 1፥66)፥ ልግስናን ያመለክታል፤ ዘዳ. 15፥8። ቀኝ እጅ ከግራ እጅ እንደሚበልጥ ይታመናል፤ ዘፍ. 48፥13-19። እጅ እንደ አገደበት የንግግርን ስልት ይገልጣል፤ ሐጌ 1፥1፤ ሐ.ሥ. 26፥1። ክርስቶስ በእጅ ምሳሌነት እንደሚገለጥ ሊቃውንት ተርጕመዋል፤ መዝ. 144፥7።

**እጅ መንሻ**፤ ተቀባይነትን ለማግኘት አንዱ ለሌላው የሚሰጠው ገጸ በረከት፥ መተያያ፤ ዘፍ. 34፥12፤ መዝ. 45፥12፤ 68፥29፤ 72፥10።

**እጅ መጫን**፤ ይህ ሥርዐት ብዙ ነገርን ሊያመለክት ይችላል፤ ዕብ. 6፥1-2። ዋና ዋናዎቹ፥ በረከትን መስጠት (ዘፍ. 48፥13-19)፥ በደልን ማስተላለፍ (ዘጸ. 29፥10:15:19፤ ዘሌ. 16፥21)፥ ሥልጣንን መስጠት (ዘዳ. 34፥9)፥ ለልዩ ሥራ ሰውን መለየት ናቸው፤ ሐ.ሥ. 6፥6፤ 13፥3። እጅ በመጫን ሰዎች ይፈወሳሉ (ማር. 6፥5፤ 16፥18፤ ሐ.ሥ. 28፥8)፥ መንፈሳዊ ስጦታዎች ይተላለፋሉ፤ 1ጢሞ. 4፥14።

**እግረኛ ወታደር**፤ ወይም መልእክተኛ፤ መሳ. 20፥2፤ 2ሳሙ. 8፥4፤ 1ሳሙ. 22፥17።

**እግር**፤ ለመሄጃ፥ ለመረማመጃ የሚያገለግል የሰውነት ክፍል። ቃሉ ለምሳሌነት በብዙ ዓይነት ይጠቀሳል። እግዚአብሔር የቅዱሳንን እግር ይጠብቃል

ሲል፥ ሕይወታቸውን ያድናል ማለት ነው፤ 1ሳሙ. 2፥9። የጠላትን አንገት በእግር መርገጥ ፍጹም ድልን ያሳያል፤ ኢያሱ 10፥24:25፤ 1ቆር. 15፥25። በእግር ላይ መውደቅ ልመናን (1ሳሙ. 25፥24፤ 2ነገ. 4፥27)፥ በእግር አጠገብ መቀመጥ መማርን ያሳያል፤ ሉቃ. 10፥39፤ ሐ.ሥ. 22፥3። እግርን ማጠብ በአነስተኛ አገልጋይ የሚፈጸም የአክብሮትና የትሕትና ሥራ ነው፤ ሉቃ. 7፥44፤ ዮሐ. 13፥5። ከእግር ትቢያን ማራገፍ፥ ከዚያ ቦታ የሰዎች ፍጹም መለየት ማለት ነው፤ ማር. 6፥11።

**የእግር መረገጫ፤** እግር የሚያርፍበት (እግርጌ)፤ ያዕ. 2፥3። ዝቅተኛነትን ሊያመለክት ይችላል፤ መዝ. 110፥1፤ ኢሳ. 66፥1፤ ማቴ. 5፥35።

**እግዚአብሔር፤** ቃሉ ከግእዝ የተገኘ ነው። እግዚእ ጌታ፥ ብሔር ደግሞ ዓለም ሲሆን፥ እግዚአብሔር ማለት የዓለም ጌታ ማለት ነው። መ.ቅ. ስለ እግዚአብሔር የሚሰጠውን ትምህርት በሚከተሉት ሰባት አርእስት ልናጠቃልለው እንችላለን።

1. የእግዚአብሔር መኖር ህልውና። መ.ቅ. በመጀመሪያ እግዚአብሔር እንዳለ ለማረጋገጥ አይሞክርም። የእግዚአብሔርን ህልውና (መኖር) መሠረት አድርጎ ያስተምራል፤ ዘፍ. 1፥1። የእግዚአብሔር ሰው በእምነት ይኖራል፤ ዕብ. 11፥6። ማንም ሰው እግዚአብሔርን በሙሉ ልብ ሲፈልግ ያገኘዋል (ኤር. 29፥13)፥ ፈቃዱንም ለማድረግ የተዘጋጀ እውነተኛውን ትምህርት ያውቃል፤ ዮሐ. 7፥17። እግዚአብሔር ራሱን በፍጥረቱ ገልጧል (ሮም 1፥19-21)፤ ሰው በሕሊናው የእግዚአብሔርን ሕግ ያውቃል (ሮም 2፥14:15)፤ እግዚአብሔር የለም የሚል ሰነፍ ተብሏል፤ መዝ. 14፥1፤ 53፥1።

አንድ ሰው እግዚአብሔር አለ ብሎ ሲያምን በሕይወቱ ሁሉ ለሚያጋጥመው ጥያቄ መልስ ይኖረዋል። ለምሳሌ ዓለም ከየት መጣ? ይህ መልካም፥ ያ ክፉ ለምን ይባላል? ምን ማድረግ ይገባኛል? ከሞት በኋላ ምን ይሆናል? ክርስቶስ ማን ነው? ወዘተ... ተብሎ ቢጠየቅ በመ.ቅ. አጥጋቢ መልስ ይሰጣል። ይህን ስንል ሁሉን ያውቃል ማለት ሳይሆን፥ በዚህ ዓለም በአግባቡ ለመኖር አስፈላጊውን ሁሉ ያውቃል ማለት ነው፤ 1ቆር. 2፥9፤ 1ዮሐ. 3፥1-3።

2. የእግዚአብሔር ስሞች። በዕብራይስጥ እግዚአብሔር የሚጠራባቸው በተለይ ሦስት ስሞች አሉ።

(ሀ) ኤል። ኃያል (አምላክ) ማለት ነው። በብዛት ኤሊም ነው። በአራማይክም ብዙ ጊዜ በግጥም ኤላህ ተብሎ ይነገራል። ቃሉ በሴማዊ ቋንቋ ሁሉ ይገኛል። በዕብራይስጡ የብ. ኪ. መጻሕፍት «ኤል፥ ኤሎሂም» የሚለው በአማርኛው መጽሐፍ ቅዱስ እግዚአብሔር፥ አምላክ፥ አማልክት ተብሎ ብዙ ጊዜ ተተርጉሟል፤ ዘፍ. 1፥1፤ መዝ. 81፥9። በዕብራይስጥም ሆነ በሌሎች ሴማውያን ቋንቋዎች የሚናገሩ በእስራኤል አገር በአካባቢዋም ይኖሩ የነበሩ ሁሉ ጣዖቶቻቸውን «ኤል፥ ኤሎሂም» እንደ አማርኛው «አምላክ፥ አማልክት» ብለው ይጠሩአቸው ነበር (ዘጸ. 18፥11፤ ዘዳ. 4፥28)፤ ቃሉ ገዥነትን፥ ፈራጅነትንም ስለሚያመለክት፥ ሰዎች ተጠርተውበታል፤ ዘጸ. 7፥1፤ 21፥6፤ መዝ. 82፥6፤ ዮሐ. 10፥34:35። መላእክትም ተጠርተውበታል (መዝ. 8፥5)፥ ይህም በዕብራይስጡ ብቻ ነው። ከዚህም ሌላ «ኤል» እንደ ኢትዮጵያ ስም አጠራር ከሰውና ከቦታ ስም ጋር ይነገራል። ለምሳሌ ኤልሳዕ (እግዚአብሔር ደኅንነት ነው)፥ ኤልሳቤጥ (እግዚአብሔር መሐላዬ ነው)፥ ቤቴል (የእግዚአብሔር ቤት)፥ ኤልሻዳይ (ዘፍ. 17፥1፤ ሁሉን ቻይ አምላክ) ማለት ነው።

(ለ) ያህዌ። አንዳንዶች የሆሻ የሆዋ ይላሉ፥ አጠራራቸው ግን ትክክለኛ አይመስልም። ያህዌ የእግዚአብሔር ስም ነው። ትርጉሙ ያለና የሚኖር፥ እንደ ባሕርዩ የሚሠራ ማለት ነው፤ ዘጸ. 3፥13-15። ያህዌ እግዚአብሔር ተብሎ ተተርጕሞአል፤ ዘፍ. 4፥26። ያህዌ ከሌላ ስም ጋር ተዛርፎ ይገኛል፥ ለምሳሌ ያህዌ ይርኤ (እግዚአብሔር ያያል፤ ዘፍ. 22፥14)፥ ያህዌ ንሲ (እግዚአብሔር ዓላማዬ ነው፤ ዘጸ. 17፥15)፥ ኢዮሳፍጥ (እግዚአብሔር ፈርዷል)፥ ኢዮራም (እግዚአብሔር ከፍ ከፍ አለ)፥ ኢያሱ (እግዚአብሔር አዳኝ)፥ ሃሌሉያ (ሀለሉያህ) እግዚአብሔርን (ያህዌን) አመስግኑ ማለት ነው። ብዙ ጊዜ ኤልና ያህዌ በአንድነት ይገኛሉ፤ «እግዚአብሔር አምላክ» ተብለውም ይተረጐማሉ፤ ዘፍ. 2፥8። ኤልያስ ማለትም «ያህዌ አምላክ ነው» ማለትን ያሳያል።

(ሐ) አዶን። ጌታ ማለት ነው። ቃሉ በአማርኛው መጽሐፍ ቅዱስ ጌታ (መዝ. 35፥23)፥ እግዚአብሔር (መዝ. 37፥13)፥ አቤቱ (መዝ. 38፥9)፥ ተብሎ ተተርጕሞአል። አዶን ከልዩ ልዩ ስም ጋር ተዛርፎ ይገኛል፤ ለምሳሌ አዶንያስ (ያህዌ ጌታዬ ነው፤ 2ሳሙ. 3፥4)፥ አዶኒራም (ጌታዬ ከፍ ያለ ነው፤ 1ነገ. 4፥6)። አ.ኪ. በተጻፈበት በግሪክ ቋንቋ «ቴዎስ» እግዚአብሔር ወይም አምላክ፥ «ኪርዮስ» ደግሞ ጌታ ተብሎ ይተረጐማል። በአማርኛው እግዚአብሔር በሚለው ላይ ሁሉ በግእዙ የሕዝቅኤል ትንቢት አዶናይ ይላል።

3. የእግዚአብሔር የባሕርዩ መገለጫ። እግዚአብሔር መንፈስ ነው (ዮሐ. 4፥24)፥ ብርሃን ነው (1ዮሐ. 1፥5)፥ ፍቅር ነው (1ዮሐ. 4፥8)። እግዚአብሔር አካላዊ ወይም እኔነት ያለው ነውና ራሱን በሚገልጥበት መጠን ልናውቀው እንችላለን፤ ዮሐ. 17፥3። ሆኖም የሚሰጠው መገለጥ በከፊል እንጂ ሙሉ በሙሉ እንድናውቀውና እንድናየው አይደለም፤

ዘጸ. 33፥20፤ ኢሳ. 55፥8:9፤ 1ጢሞ. 6፥16። እግዚአብሔር ስለ ራሱ ብዙ ነገሮችን ገልጧል። እነዚህም ነገሮች የእግዚአብሔር የባሕርይ መገለጫዎች ይባላሉ። ከእነዚህም አራቱ በፍጥረት (በፍጡር) ዘንድ አይገኙም።

(ሀ) ሁሉን ቻይነቱ። እግዚአብሔር ለባሕርዩ መነሻ ምክንያት የለውም፤ ከዚህ ተገኘ አይባልም። ራሱ በራሱ የነበረ፥ ያለና የሚኖር ነው። «ያህዌ» የሚለው ስሙም ይህን ይገልጣል፤ ዳን. 4፥35፤ ዮሐ. 5፥26፤ ራእ. 4፥10:11።

(ለ) አለመለወጡ። እግዚአብሔር ከዘለዓለም እስከ ዘለዓለም ያው ነው። በህላዌ (በአንዋንዋር) በአሳቡም አይለወጥም፤ መዝ. 33፥11፤ ሚል. 3፥6፤ ዕብ. 6፥17።

(ሐ) አለመወሰኑ፤ መዝ. 145፥3። እግዚአብሔር በሁሉ ይገኛል (መዝ. 139፥7-10፤ ሐ.ሥ. 17፥27:28)፥ መጀመሪያና መጨረሻ የለውም፤ መዝ. 90፥2።

(መ) አለመከፋፈሉ። ይህ ማለት ሰው ሥጋና ነፍስ እንዳለው ሁሉ፥ ለእግዚአብሔር ግን ሁለት ወይም ከሁለት በላይ የሆኑ ቀዋሚያን ነገሮች አሉት አንልም። ስለዚህ መ.ቅ. እግዚአብሔር መንፈስ ነው፤ ብርሃን ነው ይላል። ይህን ስንል፥ በዓለም ያለው መንፈስና ብርሃን ሁሉ እግዚአብሔር ነው ማለታችን አይደለም። እግዚአብሔር ከፍጥረቱ የተለየ ነው። ሆኖም በፍጥረትም የሚገኘው ሁሉ የእርሱ ሥራ ነው። እግዚአብሔር በራሱ መንፈስ፥ ፍቅር ነው (ዮሐ. 4፥24)፥ ስለዚህ ሰው ወደ እግዚአብሔር ሲቀርብ የባሕርዩ መገለጫ ወደ ሆኑት ወደ ፍቅሩና ወደ መንፈሱ ወደ ጽድቁም ይቀርባል።

ከዚህ በታች የተጠቀሱት ስምንት ነገሮች በመጠኑ በፍጥረት (በፍጡር) ዘንድም ይገኛሉ፥ በእግዚአብሔር ዘንድ ግን በምልአት ይገኛሉ፤ በክርስቶስም ተገልጠዋል፤ ዮሐ. 1፥14፤ ቆላ. 2፥9።

(ሠ) የእግዚአብሔር ዕውቀት። እግዚአብሔር ራሱን (1ቆሮ. 2፥10)፥ በሰው ልብ ያለውን (ሕዝ. 11፥5)፥ የሚመጣውንም (ኢሳ. 46፥10) ያውቃል።

(ረ) የእግዚአብሔር ጥበብ። እግዚአብሔር ለራሱ ክብር እንዲሆን ሁሉን ያደርጋል፤ ዳን. 2፥20:21፤ ሮም 11፥33፤ 1ቆሮ. 2፥7።

(ሰ) የእግዚአብሔር ቸርነት። እግዚአብሔር ለፍጥረት ሁሉ መልካም ነገርን ያደርጋል፤ መዝ. 146፥8:9፤ ማቴ. 5፥44:45።

(ሸ) የእግዚአብሔር ፍቅር። አብ ወልድን ይወዳል (ዮሐ. 10፥17)፥ ዓለምንም ወድዶ ልጁን ሰጠ፤ ዮሐ. 3፥16። የእግዚአብሔር ፍቅር በ3 ቃላት ይገለጣል። 1. ጸጋ። በሰው ምክንያት ሳይሆን እንዲሁ በጸጋው እንደሚወድ ያሳያል፤ ኤፌ. 1፥6:7። 2. ምሕረት። በኃጢአት ሙታን ስንሆን በምሕረቱ በክርስቶስ ሕይወትን ስለሰጠን ፍቅሩን ያሳያል፤ ኤፌ. 2፥4-5። 3. ትዕግሥት። ሰዎች እንዲመለሱ በትዕግሥቱ ለንስሐ ጊዜ በመስጠቱ ፍቅሩን ይገልጣል፤ ሮም 2፥4፤ 2ጴጥ. 3፥9።

(ቀ) የእግዚአብሔር ቅድስና። እግዚአብሔር ከፍጥረቱ የተለየ (ኢሳ. 6፥3)፥ በራሱም ንጹህ ነው፤ ዕን. 1፥13።

(በ) የእግዚአብሔር ጽድቅ። እግዚአብሔር ለሰው እንደ ሥራው ይሰጣል፤ 1ጴጥ. 1፥17።

ሰውንም ለማዳን የኃጢአትን ዕዳ በክርስቶስ በመክፈሉ ጽድቁን አሳየ፤ ሮም 3፥26።

(ተ) የእግዚአብሔር ታማኝነት። እግዚአብሔር እውነት ነውና (ዮሐ. 14፥6)፥ ሐሰትን አይናገርም (ዘኁ. 23፥19)፥ ቃሉንም ይፈጽማል፤ 2ጢሞ. 2፥13፤ ዕብ. 10፥23።

(ቸ) የእግዚአብሔር ሥልጣን። እግዚአብሔር እንደ ባሕርዩ የፈለገውን ለማድረግ ይችላል (ማቴ. 19፥26)፥ እንደ ፈቃዱም ያደርጋል፤ ሮም 9፥14:15፤ ኤፌ. 1፥11።

4. የእግዚአብሔር አካላት። እግዚአብሔር አንድ ነው፥ ግን በአንድነቱ ሦስትነት አለ። «ሥላሴ» ይመ.

5. የእግዚአብሔር ውሳኔ። እግዚአብሔር በፍጥረትም በደኅንነትም ሁሉን ወቅዷል፤ ወስኗልም። ያለ እርሱ ፈቃድ ምንም አልሆነም፤ አይሆንምም። ውሳኔው ከዘለዓለም በጥበቡ ተመሠረተ (ኤፌ. 3፥8-11)፥ እንደ ቻይነቱ ይፈጸማል (ኢሳ. 46፥8-10)፥ እንደ ታማኝነቱ አይለወጥም፤ ኢዮብ 23፥13:14። ውሳኔውም በሰው ድርጊት ይፈጸማል እንጂ አይመሠረትበትም፤ ሐ.ሥ. 2፥23። ውሳኔው የሰውን ሥራ ክፉም ቢሆን ወይም መልካም (ሐ.ሥ. 2፥23፤ ኤፌ. 2፥10)፥ የሰውን ሕይወት (ኢዮብ 14፥5)፥ መኖሪያውንም ያጠቃልላል፤ ሐ.ሥ. 17፥26።

ሰው ኃጢአት የሚሠራው እግዚአብሔር ፈቅዶ አይደለም። ሆኖም ከእግዚአብሔር ሥልጣን ውጭ አይደለም። ሰው ለሚሠራው ሁሉ ኀላፊ ነው፥ እንደ ሥራውም ዋጋውን ይቀበላል፤ ገላ. 6፥7-9። ሰው ምን ማድረግ እንደሚገባው እግዚአብሔር ገልጧል፥ ነገር ግን ጠቅላላው የእግዚአብሔር ዕቅድ አልተገለጠም፤ ዘዳ. 29፥29፤ ሐ.ሥ. 17፥30:31።

6. የእግዚአብሔር ምርጫ። እግዚአብሔር ከዓለም ሕዝብ ሁሉ እስራኤልን መረጠ፤ ዘዳ. 7፥6-8። ሰዎችን ለልዩ ልዩ አገልግሎት መረጠ፤ ዘዳ. 18፥5። ሰዎችንም ለደኅንነት መረጠ፤ ማቴ. 22፥14፤ ሮም 11፥5፤ ኤፌ. 1፥4:5። አንዳንዶችን በመምረጥ ሌሎችን በኃጢአታቸው እንደተዋቸው ማለት ነው። ሰው ኃጢአተኛ በመሆኑ እግዚአብሔር አንድን ሰው እንኳን ባያድን ጻድቅ ነው፥ ሰዎችን ለማዳን ወይም ለመተው የእርሱ መብት ነው፤ ማቴ. 20፥14:15፤ ሮም 9፥14-24። ምርጫው ከሰው ደግነት አይደለም። እምነትም የእግዚአብሔር ስጦታ ነውና በሰው እምነት እንኳን አልተመሠረተም፤ ኤፌ. 2፥8:9፤ 2ተሰ. 2፥13:14፤ 2ጢሞ. 1፥9። ምርጫው ከእግዚአብሔር ነው፤ ዮሐ. 6፥44፤ ሮም

9፥11። እግዚአብሔር የመረጣቸውን እስከ መጨረሻው ያድናቸዋል፥ እነርሱም አይጠፉም፤ ዮሐ. 6፥37-39፤ 10፥28፤ 17፥6-11፤ ሮም 8፥28-39፤ 1ጴጥ. 1፥3-5።

7. የእግዚአብሔር ልጆች። የእግዚአብሔር ልጆች ተብለው የሚጠሩ ሁሉ ከእግዚአብሔር ሥልጣን የተቀበሉ ናቸው። ስለዚህ 1) መላእክት፤ ኢዮብ 1፥6፤ 2፥1፤ 38፥7። 2) ሰዎች ሁሉ፤ ሉቃ. 3፥38፤ ኢሳ. 64፥8። 3) የእስራኤል ሕዝብ፤ ዘጸ. 4፥22፤ ሆሴዕ 11፥1። 4) ኢየሱስ በሰውነቱ፤ ማቴ. 3፥17፤ ሉቃ. 1፥35። 5) በክርስቶስ ያመኑ (ዮሐ. 1፥12)፥ የእግዚአብሔር ልጆች ይባላሉ። ሰዎች የእግዚአብሔር ልጆች መሆናቸውን በአካሄዳቸው ይገልጣሉ፤ ሮም 8፥14፤ 1ዮሐ. 3፥1-10። በዘፍ. 6፥2 «የእግዚአብሔር ልጆች» የሚለውን ከሊቃውንት ብዙዎች የአዳምን ልጅ የሴት ትውልድ፥ አንዳንዶች ደግሞ የወደቁትን መላእክት ያመለክታል ይላሉ። «ልጅነት» ይመ.

**የእግዚአብሔር መንግሥት፤** ይህ መንግሥት እግዚአብሔር የሚነግሥበት ነው። ክርስቶስ ባለበት የእግዚአብሔር መንግሥት አለ፤ ሉቃ. 17፥20:21። የእግዚአብሔርን መንግሥት በንጉሥነት የሚገዛ ጌታ ኢየሱስ ስለሆነ፥ በእርሱ ወደዚህ ዓለም መምጣት የእግዚአብሔር መንግሥት ተመሠረተ (ማቴዎስ «መንግሥተ ሰማያት» ይላል። አሳቡ ግን ያው ነው፥ ማቴ. 5፥3ና ሉቃ. 6፥20 ያነጻጽሩ)። መጥምቁ ዮሐንስ ሰዎችን ለመንግሥቱ አዘጋጀ፤ ማር. 1፥14:15። ኢየሱስ ሰዎችን ወደ እግዚአብሔር መንግሥት አስገባ። ሰዎች ወደ እግዚአብሔር መንግሥት እንዲገቡ ዳግመኛ መወለድ ያስፈልጋቸዋል፤ ዮሐ. 3፥3-5። መግባታቸው በብዙ ችግር ይሆናል፤ ማቴ. 11፥12፤ ሐ.ሥ. 14፥22። የእግዚአብሔር መንግሥት እንደ ምድራዊ መንግሥት አይደለም። አስተዋይ አእምሮ ያለው ያስተውለዋል እንጂ በሰው ዐይን አይታይም፤ ሉቃ. 17፥20፤ ዮሐ. 18፥36። ኢየሱስ አጋንንትን በማውጣቱ መንግሥቱ እንደመጣ አረጋገጠ፤ ማቴ. 12፥28። ወደ እግዚአብሔር መንግሥት የሚገቡ ቃሉን ለመቀበል የተዘጋጁ፥ ጥሩና መልካም ልብ ያላቸው እንጂ ሰዎች ሁሉ አይደሉም፤ ሉቃ. 8፥4-15።

የእግዚአብሔር መንግሥት በትንሽ ነገር ይጀመራል፥ በኋላ ትልቅ ይሆናል፤ ማቴ. 13፥31:32። ትንሽ ነገር ቢመስልም ሁሉን ይለውጣል፤ ማቴ. 13፥33። ሰው ሳያስተውል ይሠራል፥ ጊዜው ሲደርስ ግን ቋሚ ይሆናል፤ ማር. 4፥26-29። ወደዚህ መንግሥት ለመግባት ሰው ያለውን ሁሉ ይሰጣል፤ ማቴ. 13፥44-46። በመንግሥቱ እውነተኞችና ሐሰተኞች ለጊዜው አንድ ላይ ይኖራሉ፥ በዓለም መጨረሻ ግን ይለያሉ፤ ማቴ. 13፥24-30:36-43። «ምሳሌ»፥ «የኢየሱስ ምሳሌዎች» ይመ.

ኢየሱስ በምድር ሳለ መንግሥቱ ነበረ፥ አሁንም አለ፥ በዓለም መጨረሻም ይገለጣል። ኢየሱስ ዳግመኛ ሲመጣ ይፈርዳል፥ ሐሰተኞችን ያወጣል፥ ለሰዎች እንደ ሥራቸው ዋጋ ይከፍላቸዋል። ስለዚህ የእርሱን ሥራ በመሥራት መምጣቱን መጠባበቅ ያስፈልጋል፤ ማቴ. 13፥47-50፤ ም. 25፤ ሉቃ. 12፥35-48። ለኢየሱስ በሰማይና በምድር ሥልጣን ሁሉ አለው፤ ማቴ. 28፥18። መንግሥቱ በተለይ በቤ. ክ. ይታያል። ሆኖም ሰዎች ቢያስተውሉም ባያስተውሉም መንግሥቱ በዓለም ሁሉ ይጸናል፥ ባለ ሥልጣናት በእርሱ ይሾማሉ፤ ሮም 13፥1።

**የእግዚአብሔር መጋቢነት፤**

የእግዚአብሔር ሥልጣንና ገዥነት፥ የባሕርዩ አገዛዝና ጥበቃ። እግዚአብሔር የዓለም ፈጣሪና ንጉሥ በመሆኑ የፈለገውን ያደርጋል፤ መዝ. 103፥19፤ 135፥6፤ ዳን. 4፥35፤ ኤፌ. 1፥11። ስለ መጋቢነቱ በተለይ አራት ነገሮችን መገንዘብ ይገባናል።

1. መጋቢነቱና ፍጥረት። ያለ እርሱ ምንም አይሆንም። እግዚአብሔር ተክልን ያበቅላል (መዝ. 147፥8:9)፥ አውሬዎችን ያስተዳድራል፤ ኢዮብ 39። የነጐድጓድ ወይም የድንቢጥ ውድቀት በእርሱ ፈቃድ ነው፤ መዝ. 29፤ ማቴ. 10፥29። ለሰውና ለእንስሳት ሕይወትን ይሰጣል፤ ይወስዳልም (1ሳሙ. 1፥27፤ ኢዮብ 1፥21)፤ ጤና ይሰጣል፥ ሕማምን ያመጣል (ዘጸ. 7፥15፤ 28፥27:60)፤ መከራንና ጥጋብን ያመጣል፤ አሞጽ 3፥6፤ ኢሳ. 45፥7። በመጋቢነቱ ጥበቡ፥ ኃይሉ፥ ክብሩ፥ ደግነቱም ይገለጣሉ፤ መዝ. 20፥1-5፤ ሐ.ሥ. 14፥17፤ ሮም 1፥19-21።

2. መጋቢነቱና የዓለም ታሪክ። የእግዚአብሔር ዓላማ ከነገድና ከሕዝብ ሁሉ አንዲት ቤተ ክርስቲያንን ለመፍጠር ነው፤ ኤፌ. 3፥1-11። ከእነርሱም መቤዠት የተነሣ ዓለም ሁሉ ወደ ክብር ይደርሳል፤ ሮም 8፥19-21። ይህንም ሲያደርግ በሚቃወሙት ላይ ይስቃል፤ ለዓላማውም ይጠቀምባቸዋል፤ ሐ.ሥ. 4፥25-28፤ መዝ. 2፥4።

3. መጋቢነቱና የሰው ሕይወት። እግዚአብሔር የሚታዘዙለትን እንደሚባርክና የሚቃወሙትንም እንደሚቀጣ ተናግሯል፤ ዘሌ. 26። እንግዲህ ኃጥአን ለምን በምቾት ይኖራሉ? የእግዚአብሔር ሰዎች ግን ለምን መከራን ይቀበላሉ? የኃጥአን ምቾት ጊዜያዊ ብቻ ነው፤ መዝ. 50፥16-21፤ 73፥3-5:17-19። እንደዚሁም የእግዚአብሔር ሰዎች መከራ ጊዜያዊ ብቻ ነው፤ ሚል. 3፥13-4፥3፤ 1ጴጥ. 5፥10። ደግሞም ምእመናን መከራ ለጥቅማቸው እንደሚሆን (ዕብ. 12፥7-11)፥ መከራን በመቀበል እግዚአብሔርን እንደሚያከብሩ ሥራውም እንደሚፈጽምበት (ኢዮብ ም. 1-2፤ መዝ. 73፥14:23-28)፥ ከክርስቶስም ጋር በመከራው እንደሚተባበሩ ያውቃሉ፤ ማቴ. 10፥24፤ ዮሐ. 16፥33፤ ፊል. 3፥10፤ 1ጴጥ. 4፥13።



የእግዚአብሔር ማደሪያ በሕዝቡ መካከል

4. መጋቢነቱና ነፃ ፈቃድ። ምንም እንኳ እግዚአብሔር ያሰበውን ቢያደርግ፥ ሰው ለሚሠራው ሁሉ ኃላፊ ነው። የእግዚአብሔርና የሰው አድራጎት ጐን ለጐን ይሄዳሉ። እንዴት እንደሚገናኙ ግን ምሥጢር ነው፤ ዘፍ. 50፥20፤ ሐ.ሥ. 2፥23፤ ፊል. 2፥12:13፤ ቆላ. 1፥29። «ነፃ ፈቃድ»፥ «እግዚአብሔር» «5:6» ይመ.

**የእግዚአብሔር ማደሪያ፤** የሚተከልና የሚነሣ ድንኳን። ለእግዚአብሔር የሚሰገድበትና እግዚአብሔር የሚገለጥበት ቦታ፤ ዘሌ. 26፥11:12። ማደሪያው ደግሞ የመገናኛው ድንኳን (ዘጸ. 29፥42)፥ የእግዚአብሔር ድንኳን (ራእ. 21፥3)፥ የምስክሩ ድንኳን፤ ዘኁ. 17፥7:8 ይባላል። እግዚአብሔር ለሙሴ የአሠራሩን ዝርዝር ሁሉ ሰጠው፤ ዘጸ. 25-28። ማደሪያው እንዲሠራ አስፈላጊውን ዕቃ ሁሉ ሕዝቡ እንዲሰጡ በተጠየቁ ጊዜ በልግስና አቀረቡ፤ ዘጸ. 25፥1-9፤ 36፥3-6። ማደሪያው በአደባባይ ተተክሎ በዙሪያው በመጋረጃ ታጥሮ ነበር፤ ዘጸ. 27፥9-19።

<u>የእግዚአብሔር ማደሪያ ንድፍ</u>። በስተምሥራቅ በኩል ብቻ በር ነበረ። ሰው በበሩ ሲገባ መጀመሪያ የሚታየው ታላቅ የናስ መሠዊያ ነበር፥ ከእርሱም በኋላ የናስ መታጠቢያ አለ። የማደሪያው ምሰሶችና ሳንቃዎች ከግራር እንጨት የተሠሩ ነበሩ፤ ይህ ከላይ በአራት ዓይነት መጋረጃ ተሸፍኖ ነበር፤ ዘጸ. 26። ውስጡ በሌላ መጋረጃ በሁለት ተከፍሎ፥ መጀመሪያው ክፍል ቅድስት ሲባል ውስጠኛው ቅድስተ ቅዱሳን ተብሏል፤ ዘጸ. 26፥33። በቅድስቱ ውስጥ ሦስት ነገሮች ነበሩ። 1. በስተግራ ከወርቅ የተሠራ መቅረዝ። 2. በስተቀኝ ለመገናኛ ኅብስት (ኅብስተ ገጽ) የሚሆን ገበታ። 3. ፊት ለፊት በመጋረጃው ሥር የዕጣን መሠዊያ (የወርቅ መሠዊያ)። በቅድስተ ቅዱሳኑ ውስጥ ታቦት ብቻ ነበረ፤ ዘጸ. 37። ታቦቱ እንደ ሣጥን ሆኖ የተሠራ ነበር፤ ዐሠርቱ ቃላት (ትእዛዛት) የተጻፉባቸውን ሁለት ጽላት፥ መና ያለበትን የወርቅ መሶብና የአሮንንም በትር በውስጡ ይዟል፤ ዕብ. 9፥2-4።

እስራኤላውያን ከግብጽ አገር በወጡ በ2ኛው ዓመት የእግዚአብሔር ማደሪያ በምድረ በዳ በደብረ ሲና ሥር ተሠርቶ ነበር። ከዚያ በኋላ ለ35 ዓመት በቃዴስ ተቀመጠ። ሕዝቡ ለጕዞ ሲነሡ ማደሪያውንና በውስጥ ያለውን ዕቃ ሁሉ የሚሸከሙ ሌዋውያን ይቀድሙ ነበር፤ ዘኁ. 10፥33-36። በኋላ በጌልገላና በሴሎ (ኢያሱ 4፥19፤ 18፥1) ተቀመጠ። ለአጭር ጊዜ በኖብ፥ የናስ መሠዊያውም በገባዖን ነበረ፤ 1ሳሙ. 21፥1-6፤ 1ዜ.መ. 16፥39-40፤ 21፥29። በመጨረሻ ዳዊት ወደ ኢየሩሳሌም አመጣው።

በእግዚአብሔር ማደሪያ አሠራር ታሪክ ውስጥ የወርቁ ጥጃ አምልኮት ታሪክ ጣልቃ ገብቷል። ከርሱ በፊት እግዚአብሔር ለሙሴ የሰጠው ንድፍ በዝርዝር ይገኛል (ዘጸ. 25-31)፤ ቀጥሎም የሥራው አፈጻጸም ተጽፏል፤ ዘጸ. 35-40። ማደሪያው የተሠራው እግዚአብሔር ከሕዝቡ ጋር እንዲገናኝ፥ ሕዝቡም እግዚአብሔር ከእነርሱ ጋር መሆኑን እንዲያውቁ ነው፤ ዘጸ. 25፥8:22፤ 29፥42። ሥራው ሁሉ ባለቀ ጊዜ የእግዚአብሔር ክብር በደመና ማደሪያውን ሞላ፤ ዘጸ. 40፥34። በአ.ኪ. የእግዚአብሔር ድንኳን ይባላል። በዕብራውያን መልእክት አንዳንድ ጊዜ ጸሓፊው ስለ እርሱ ሲጠቅስ ልዩ ልዩ መንፈሳዊ ትምህርትን ይሰጣል፤ ዕብ. 8፥2-5። በምዕራፍ ዘጠኝና ዐሥር ስለ



የመገናኛ ድንኳን ንድፍ

ጥንታዊው ማደሪያና ስለ ሃይማኖታዊ ሥነ ሥርዓት ሁሉ ሲጽፍ፥ ስለ ክርስቶስ መድኀኒትና ስለ ሊቀ ካህንነቱ ያስተምራል። ቢሆንም በተሰጠው ዋና ዋና ትምህርት ውስጥ ሰው ኃጢአተኛ ሆኖ ሳለ፥ ወደ እግዚአብሔር እንዴት ሊቀርብ እንደሚችል ተገልጧል። ክርስቶስ በሞተ ጊዜ የቤተ መቅደስ መጋረጃ ከላይ እስከ ታች ተቀደደ፥ ይህም የሚያሳየው ወደ እግዚአብሔር የሚያደርሰው መንገድ መከፈቱን ነው፤ ማር. 15፥37:38፤ ዕብ. 10፥19:20።

**እጥበት፤** ከነዓን አቧራማ አገር ነውና ሰው ከጉዞው ወደ ቤት ሲገባ፥ እግርን መታጠብ የተለመደ ነበር፤ ዘፍ. 18፥4፤ መሳ. 19፥21፤ ሉቃ. 7፥44። ካህናት ከአገልግሎት በፊት እንዲታጠቡ ብዙ ሥርዐት ነበረ፤ ዘጸ. 30፥17-21። ሰው ከምግብ በፊት እጅን የመታጠብ ሥርዐት የተለመደ ነበር። ፈሪሳውያንም እጅና ዕቃን አጥርቶ ስለማጠብ ብዙ ወግ ነበራቸው፤ ኢየሱስ ግን ዋናው ቁም ነገር የእጅ ሳይሆን የልብ መታጠብ መሆኑን አስተማረ፤ ማር. 7፥1-8፤ ሉቃ. 11፥38-41፤ ዮሐ. 13፥1-5:8:11። መታጠብ በጥምቀት ከኃጢአት መንጻትን የሚያመለክት ቃል ነው፤ ቲቶ 3፥5።

**እጥፍ፤** ሁለት እጅ፥ ወይም የታጠፈ በመሆኑ የመጀመሪያውን የሚያህል፤ ዘፍ. 43፥12፤ ኢሳ. 40፥2።

**እፉኝት፤** መርዛም እባብ፤ ዘዳ. 32፥33፤ ምሳ. 23፥32፤ ሐዋ. 8፥17።

**እፍረት፤** የጉድለት፥ የነውር፥ ወይም የውርደት ስሜት። ሰዎች የሚገባቸውን ሲያደርጉና በወንጌል ሲያምኑ አያፍሩም፤ ዘፍ. 2፥25፤ ሮም 1፥16፤ 10፥11፤ 2ጢሞ. 1፥8:12፤ 1ጴጥ. 2፥6፤ 4፥16፤ 1ዮሐ. 2፥28። ሰው የማይገባውን ሲያደርግ ግን እፍረት ይሰማዋል፤ ዘፍ. 3፥7፤ ምሳ. 19፥26፤ ዳን. 9፥8፤ 12፥2፤ 1ቆሮ. 1፥27፤ 2ተሰ. 3፥14። እግዚአብሔር ለሕዝቡ ባዘጋጀላቸው አያፍርም (ዕብ. 11፥16)፥ ክርስቶስ በቃሉ በሚያፍሩ ያፍርባቸዋል፤ ማር. 8፥38። ምእመናንን ወንድሞቼ ብሎ ሲጠራቸው አያፍርም፤ ዕብ. 2፥13።

**ኦሖላ፤** ኦሖሊባ፤ በምሳሌ ኦሖላ ለሰማርያ፥ ኦሖሊባ ለኢየሩሳሌም የተሰጡ ስሞች ናቸው። ኦሖላ ማለት ድንኳንዋ፥ ኦሖሊባ ደግሞ ድንኳኔ በእርስዋ ውስጥ ነው ማለት ነው። ስሞቹ የሁለቱን አገሮች ባዕድ አምልኮት ያመለክታሉ፤ ሕዝ. 23።

**ኦሪት፤** (ኦምስቱ ብሔረ ኦሪት)፤ ሕግ፥ ትምህርት ማለት ነው። ቃሉ ኦራይታ ከሚለው የጥንት የሶርያ ቋንቋ የተገኘ ነው። በተለይም ኦሪት የመ.ቅ. መጀመሪያ የሆኑትን አምስቱን መጻሕፍት ያመለክታል። መጻሕፍቱ የሚገልጡትን በአጭሩ ከዚህ ቀጥሎ እናሳያለን።

1. የመጀመሪያ ነገሮች። ፍጥረት፥ የሰው ውድቀት፥ የጥፋት ውሃ፥ የባቢሎን ግንብ፤ ዘፍ. 1-11። 2. የአባቶች ታሪክ። አብርሃም፥ ይስሐቅ፥ ያዕቆብ፥ ዮሴፍ፤ ዘፍ. 12-50። 3. የእስራኤል ሕዝብ ከግብጽ መውጣትና እስከ ደብረ ሲና መድረስ፤ ዘጸ. 1፥1-19፥2። 4. የእስራኤል ሕዝብ ሕግን መቀበል፥ ማደሪያውን (የመገናኛ ድንኳንን) መሥራት፥ ሥነ ሥርዐቱንም ማቆም፤ ዘጸ. 19፥3-ዘሌ. 27። 5. የእስራኤል ሕዝብ ለጉዞ መዘጋጀት፤ ዘኁ. 1፥1-10፥10። 6. ባለማመናቸው ምክንያት አርባ ዓመት በምድረ በዳ የእስራኤል ሕዝብ መቅበዝበዝ፤ ዘኁ. 10፥11-22፥1። 7. ወደ ከነዓን ለመግባት የእስራኤል ሕዝብ መዘጋጀት፤ ዘኁ. 22፥2-36፥13። 8. በእስራኤል ሕዝብ የሙሴ ስንብት (ዘዳግም)።

**የኦሪት ጸሐፊ፤** ኦሪት ከጥንት ጀምሮ አምስቱ የሙሴ መጻሕፍት በመባል ይታወቃል። በ10ኛው ክፍለ ዘመን ገደማ ጀምሮ ግን አንዳንድ መምህራን ኀለኞች ነቢያትና ጸሐፊዎች በእስራኤልና በይሁዳ መንግሥት ዘመን ከምርኮም በኋላ ባለው ዘመን ጽሑፎችንና የቀደሙ የባህል ሕጎችን ሰብስበው አቀነባበሩአቸው፤ በእነርሱም ዘመን ኦሪት መልክ ሊይዝ ችሏል የሚል ግምት አላቸው። ይሁን እንጂ ጉዳዩ በአንዳንድ አብያተ ክርስቲያናት ዘንድ እጅግ አጨቃጫቂ ሆኖ ተገኝቷል።

እርግጥ፥ ሙሴ የሕግ (የትእዛዛት) ክፍሎችን እንደ ጻፈ በኦሪት ውስጥ ተነግሯል፤ ዘጸ. 24፥4፤ 34፥27፤ ዘዳ. 31፥9:24። ከዚህም ጋር የእስራኤልን የጉዞ ታሪክ (ዘጸ. 17፥14፤ ዘኍ. 33፥2-49)፥ መዝሙሩንም እንደጻፈ ተገልጧል፤ ዘዳ. 31፥22፤ 32፥1-44። ከእነዚህም ክፍሎች ሌላ ሙሴ ብዙዎችን ሳይጽፍ አልቀረም። ከሙሴ በፊት ስለነበሩ አባቶች ታሪክ አስቀድመው ሌሎች ጽፈው ይሆናል። እንዲህም ከሆነ ሙሴ ታሪካቸውን አንድ ላይ ሰብስቦ ሊጽፈው ይችላል። ሙሴ ስለ ራሱ ሞት (ዘዳ. 34፥1-12)፥ ከሞተ በኋላ ስለሆኑት ድርጊቶች የጻፈ አይመስልም (ለምሳሌ ዘኍ. 32፥34-42)። ከሙሴ በኋላ የነበሩ ጸሐፊዎች አልፎ አልፎ ማብራሪያ የሰጡ ይመስላል (ለምሳሌ ዘፍ. 36፥31)። ምንም እንኳ ረቂቁን የገለበጡት አንዳንድ ማብራሪያ ቢጨምሩም፥ አንዳንድ ቃላትንም በዘመናቸው ወደሚነገረው ዕብራይስጥ ቢለውጡ ጠቅላላው ሕግ ከሙሴ እንደተገኘ ይታመናል፤ ዮሐ. 1፥17። ጌታችን ኢየሱስና ሐዋርያት እንደ አይሁድ መምህራን ሁሉ ኦሪት በሙሴ መጻፉን እንዳረጋገጡ ግልጽ ነው፤ ማቴ. 8፥4፤ ማር. 12፥26፤ ሉቃ. 24፥44፤ ዮሐ. 7፥19፤ ሐ.ሥ. 28፥23፤ 1ቆሮ. 9፥9፤ ዕብ. 9፥19:20።

**ኦሪዮን፤** የአውሬ አዳኝ ቅርጽ ያለው የሚመስል አንድ የከዋክብት ክምችት፤ ኢዮብ 9፥9፤ 38፥31፤ አሞጽ 5፥8። በክምችቱ ውስጥ ያሉት ኮከቦች ሲበላለጡ፥ በመልካቸውም አንዱ ቀይ፥ ሌሎችም ነጭ ወይም ሰማያዊ ሲሆኑ፥ በ1ኛ ቆሮ. 15፥41 የተጻፈውን ያሳስባሉ።

**ኦፊር፤** 1. የዮቅጣን ልጅ፤ ዘፍ. 10፥29። 2. ወርቅ፥ የሰንደል ዕንጨት፥ የከበረ ዕንቍና የመሳሰሉትም የሚገኙበት አገር፤ 1ነገ. 9፥28፤ 10፥11:12። አንዳንዶች ኦፊር ሕንድ፥ ሌሎች ደቡብ አፍሪቃ፥ የቀሩት ደግሞ ዛሬ አፋር የሚባለው ነው ይላሉ።

**ከሊታውያን፤** (ከሌቲ)፤ በደቡብ ከነዓን ይኖር የነበረ የፍልስጥኤማውያን ነገድ። ዳዊት ከእነዚህና ከፈሊታውያን የክብር ዘበኞቹን ይመርጥ ነበር፤ 1ሳሙ. 30፥14፤ 2ሳሙ. 8፥18፤ 15፥18።

**ከላውዴዎን፤** ከለዳውያን፤ ከባቢሎን በስተደቡብ በኩል የነበረ አገር፥ በዚያም የነበሩት ሕዝብ ከለዳውያን ተባሉ። ዋና ከተማቸው አብርሃም ይኖርበት የነበረው ዑር ነበረ፤ ዘፍ. 11፥31። ከለዳውያን ከባቢሎን መንግሥት ጋር ተባብረው አሦርን አሸነፉ። እነናቡከደነፆር የከለዳውያን ዘር ሲሆኑ፥ የባቢሎን ነገሥታት ሆኑ። አንዳንድ ጊዜ «ከለዳውያን» የሚለው ቃል የባቢሎንን መንግሥት በጠቅላላው ያመለክታል፤ ኢሳ. 48፥20። ከለዳውያን ፍልስፍናቸውን በተለይም የከዋክብትን ጥናትና አምልኮት ወደ ባቢሎን አመጡ፤ ዳን. 1፥3-4፤ 2፥10፤ 8፥10።

**ከሙን፤** ጥሩ ሽታ ያለው፥ ፍሬው ትንንሽ የሆነ የሚፋጅ የቅመም ዓይነት፤ ኢሳ. 28፥25:27፤ ማቴ. 23፥23።

**ከሞስ፤** «ካሞሽ» ይመ.

**ከርቤ፤** በበረሀ የሚበቅል እንጨት። ከዚያም የሚገኝ መራራ ሙጫ ሽቱነት ያለው ለዕጣን ወይም ለመድኃኒት የሚያገለግል። በመድኃኒትነቱ የሕመም ማደንዘዣ ነው፤ ዘጸ. 30፥23፤ ማቴ. 2፥11፤ ማር. 15፥23፤ ዮሐ. 19፥39። የጥንት ሴቶች በከርቤ ይነጹ ነበር፤ አስ. 2፥12።



የከርቤ ዕጣን ከዛፍ ሲለቀም

**ከርከሚሽ፤** በሶርያ አገር በስተሰሜን በኤፍራጥስ ወንዝ አጠገብ የሚገኝ ጥንታዊ ከተማ። በ605 ከክ. በ. ናቡከደነፆር የግብጽን ንጉሥ በከርከሚሽ ድል አደረገ፤ ኤር. 46፥2። ካ. 1ለ።

**ከበሮ፤** በቁርበት ተለጉሞ ከእንጨት የሚሠራ የዜማ ዕቃ። ለድል ቀን መታሰቢያ ይመታል፤ ዘጸ. 15፥20፤ 1ሳሙ. 18፥6። ለእግዚአብሔር ክብር ይዘመርበታል፤ መዝ. 149፥3፤ 150፥4። ለታቦተ ኪዳኑ ታቦት ክብር ይዘመርበት ነበር፤ 2ሳሙ. 6፥5።



**ከበባ፤** በጥንት ዘመን ከባድ መሣሪያ ስላልነበረ የተቀጠረች ከተማ በከበባ ትያዝ ነበር፤ ዘዳ. 20፥12:19፤ 2ሳሙ. 11፥16፤ ዳን. 1፥1። «ጦርነት» ይመ.

**ከባድ፤** ቃሉ የጭንትን፥ የአሳብን፥ የሕግን፥ የአገልግሎትን ሸክም ሊያብራራ ይችላል፤ ዘጸ. 18፥26፤ ዘኍ. 11፥14፤ 1ነገ. 12፥11፤ ማቴ. 11፥28፤ 23፥4፤ 26፥43።

**ከብት፤** የቀንድ ከብት ሁሉ፥ ሰኰናው ስንጥቅ፥ ምግቡን የሚያመሰኳ ስለሆነ፥ ሥጋውን መብላት ለእስራኤላውያን ተፈቅዷል። ንጹሕም ስለሆነ የቀንድ ከብት ለመሥዋዕት ይሆን ነበር፤ ዘሌ. 1፥3፤ 11፥3። ደግሞም እስራኤላውያን ለእርሻና ለሠረገላ መጐተቻ በበሬ ይጠቀሙ ነበር፤ ሉቃ. 14፥19፤ ዘዳ. 25፥4፤ ዘኍ. 7፥3። በግብጽና በከነዓን አገሮች የነበሩ አረማውያን በከብት ምሳሌ የተሠራውን ጣዖት ያመልኩ ነበር። ስለዚህም በእግዚአብሔር እምነት ያልጸኑ እስራኤላውያን ጥጃ የሚመስል ጣዖት በየጊዜው እየሠሩ ስለሰገዱ እግዚአብሔርን አስቈጡ፤ ዘጸ. 32፥4፤ 1ነገ. 12፥28።

**ከተማ፤** ሰዎች በአንድነት ለመኖር ሲፈልጉ ውሃ በሚገኝበትና ለምሽግ በሚመችበት አምባ ወይም ተራራ ላይ ቤቶቻቸውን ይሠሩ ነበር። ብዙ ጊዜ በከተማ ዙሪያ ልዩ ልዩ መከላከያ ያደርጉ ነበር። በዚያን ጊዜ ቀላሉ ምሽግ ጕድጓድና የዐፈር ክምር ነበረ። ከተማው ከፍ ባለ ቅጥር ይመሸጋል። በእስራኤል የግንብ ስፋት 3 ሜትር፥ ቁመቱ እስከ 10 ሜትር ይደርስ ነበር። በታላላቅ ከተማዎች ግን ስፋቱ እስከ 10 ሜትር ቁመቱ እስከ 20 ሜትር ይደርሳል። በቅጥሩ ውስጥ የከተማው ስፋት ሁለት ሄክታር የሚያህል ነበር። በከተማው ቅጥር ላይ ግንቦች ይሠራሉ። የምሽጉ በር ደግሞ አንድ ወይም ከአንድ በላይ ነበረ። በቅጥሩ ውስጥ በዋናው ግንብ ወይም ምሽግ ላይ የመስገጃ ቦታ ይሠራል። በበሩም አጠገብ የሕዝብ መገናኛ አደባባይ ይገኛል። በከተማ የነበሩ መንገዶች ጠባብ፥ ጠምዛዛ፥ መብራት የሌለባቸውና ያልተጠረጉ ነበሩ። በተመሸገው ከተማ ዙሪያ ብዙ ያልተመሸጉ መንደሮች ይገኙ ነበርና ጠላት ሲመጣ በመንደሮች የሚኖሩት ወደ ከተማ ይገባሉ።

የከተማ አስተዳደር ደግሞ የተለያየ ነበር። ከነገሥታት ዘመን በፊት የከተማ አለቃ ንጉሥ ይባል ነበር። በጦርነት ጊዜ ከሌሎች ነገሥታት ጋር ይተባበር ነበር። እንደ ባቢሎንና እንደ ሮም ከፍ ያሉና የሠለጠኑ አንዳንድ ከተማዎች ነበሩ። ሁኔታቸውም ከላይ ከተጻፈው የተለየ ነበር።

**ከተፈ!** (ክትፋት)፤ በጣ፤ ቈረጠ፤ ደሙ እንዲወጣ የታመመውን ገላ መብጣት፥ መቍረጥ፤ ኤር. 48፥37።

**ከነዓን፤**

1. በኖኅ የተረገመ የካም ልጅ፤ ዘፍ. 9፥18-27። ከከነዓን ዐሥራ አንድ ወገኖች ተገኙ፤ ዘፍ. 10፥15-20። ከእነርሱ ብዙዎቹ በታላቁ ባሕርና በዮርዳኖስ ወንዝ መካከል ይኖሩ ነበር። አገሩም ከኢያሱ በፊት ከነዓን ይባል ነበር። ከእነዚህ ወገኖች አንዳንዶቹ ከዮርዳኖስ በስተምሥራቅ ይኖሩ ነበር። እነዚህ ወገኖች በአንድነት ሲጠሩ ከነዓናውያን ወይም አሞራውያን ይባላሉ። ከነዓናውያን ብዙ አማልክትን ያመልኩ ነበር፤ ከሁሉም የታወቀው በአል የተባለው ጣዖት ነው። እስራኤል ከነዓናውያንን ጨርሰው ሊያጠፉአቸው አልተቻላቸውም ነበርና የከነዓን ባዕድ አምልኮ ለእስራኤል እንቅፋት ሆነ። እስራኤል ከነዓናውያንን በማስገበራቸው የመርገም ቃል ተፈጸሟል፤ ኢያሱ 17፥13።



በ1150 ዓመታት ገደማ ከክ.በ. የተቀረጸ የከነዓን ንጉሥ ምስል

2. ከነዓን የተባለ የካም የልጅ ልጆች ይኖሩበት የነበረው አገር፤ ዘፍ. 10፥6:18-19። አብርሃም በእግዚአብሔር ተመርቶ ከዑር ወደ ከነዓን ሄደ፤ ዘፍ. 11፥31፤ 12፥5:6። ከነዓንን ለአብርሃምና ለዘሩ እንደሚሰጥ እግዚአብሔር ተናገረ፤ ዘፍ. 12፥7። የእስራኤል ልጆች በሙሴ መሪነት ከግብጽ ወጥተው በኢያሱ መሪነት ወደ ከነዓን ከገቡ በኋላ እዚያ ይኖሩ ከነበሩት ሰዎች መካከል ግማሾቹን አስወገዱ፤ ዘጸ. 3፥8። የቀሩትም በኋላ በመሳፍንትና በነገሥታት ተሸነፉ። በዚያን ጊዜ አገሩ እስራኤል ተብሎ ተሰየመ፤ 1ሳሙ. 13፥19። በ931 ከክ. በ. የእስራኤል መንግሥትና አገር በሁለት ተከፈለ። በስተሰሜን ያለው እስራኤል ተባለ። በ722 ከክ. በ. እስራኤል በአሦር መንግሥት ተሸነፈ፤ 2ነገ. 17፥6። ባቢሎን ይሁዳ የተባለውን የደቡቡን ክፍል በ587 ከክ. በ. አሸነፈ፤ 2ነገ. 25፥21። ከምርኮው በኋላ እስራኤላውያን የተቀመጡበት ክፍለ አገር ይሁዳ ተባለ፤ ዕዝ. 5፥8። ከ587 እስከ 148 ከክ. በ. በባቢሎን፥ በፋርስ፥ በግሪክ፥ በግብጽና በሶርያ ተገዛ። በግሪክ መንግሥት ጊዜ አገሩ ፍልስጥኤም ይባል ነበር። እንደገና በ63 ከክ. በ. የሮም ግዛት ሆነ። በአ.ክ. ዘመን ከነዓን በአምስት ክፍል ተከፍሎ ነበር። ከዮርዳኖስ በስተምዕራብ ገሊላ፥ ሰማርያና ይሁዳ፥ በምሥራቅም ዐሥር ከተማና የዮርዳኖስ ማዶ (ፔሪያ፥ ጲራልያ) የተባሉት ክፍሎች ነበሩ።

የከነዓን ርዝመት 240 ኪ.ሜ. ስፋቱም 112 ኪ.ሜ. ነው። በታላቁ ባሕር ዳር ሰፊ ሜዳ አለ። ከዚያም በስተምሥራቅ ከገሊላ ተራራዎች እስከ ኬብሮን ድረስ አገሩ ተራራማ ነው፥ በሰማርያ ግን ሰፊ ሜዳ አለ። ከተራራዎቹ በስተምሥራቅ ጥልቀት ያላቸው የዮርዳኖስ ሸለቆና የጨው ባሕር ይገኛሉ። ከዮርዳኖስ ሸለቆ በስተምሥራቅ ያለው ቦታ ሜዳማና ተራራማ ነው። በዚህ ምክንያት ብዙ የአየር መለዋወጥ፥ ልዩ ልዩ የተክል ዐይነት በአገሩ ይገኛሉ። አገሩ በሰሜን ከሊባኖስ ተራራ እስከ ቤርሳቤህ ከተማ፥ ከዮርዳኖስ በስተምዕራብና በስተምሥራቅ ተዘርግቷል። ዛሬ ይህ አገር በሶርያ፥ በዮርዳኖስ፥ በእስራኤልና በሊባኖስ ተይዟል። ካ. ፲፩ን።

**ከንቱ፤** ከንቱነት። ባዶ፥ የማይረባ፥ ዋጋ የሌለው፥ ጥቅመ ቢስ፥ ተስፋ የማይጣልበት፥ የማያዛልቅ፥ የማያዋጣ። ይህ ቃል በብዛት በመጽሐፈ መክብብ ይገኛል። የሰው ሥጋዊ ኑሮ ከንቱ ነው (ኢዮብ 7፥3፤ መዝ. 39፥5፡6፤ ኤፌ. 4፥17፤ ሮም 8፥20)፤ ጣዖትን ማምለክ ከንቱ ነው (2ነገ. 17፥15፤ ኢሳ. 41፥29፤ 44፥9)፤ የሐሰተኛ ነቢይ ትንቢትም ከንቱ ነው፤ ሕዝ. 13፥1-23፤ ዘካ. 10፥2፤ 2ጴጥ. 2፥18።

**ከውር፤** የብርና የወርቅ የሌላውም ማዕድን ሁሉ ማቅለጫ። የፈተና ምሳሌ፤ ምሳ. 17፥3፤ 27፥21። የእግዚአብሔርንም ቍጣ ያመለክታል፤ ሕዝ. 22፥20።




**ከፍቶር፤** ቀርጤስ ወይም በግሪክና በእስያ መካከል የሚገኙ ደሴቶች።

**ከፍ ያለ፤** ከሁሉ በላይ መሆንን ያሳያል፤ የእግዚአብሔር ክብር ታላቅነት፥ የኢየሱስም መሲሐዊ ክብር በዚህ ቃል ተገልጧል፤ መዝ. 8፥1፤ ኢሳ. 2፥2፡11፤ 52፥13፤ 55፥9፤ ዳን. 11፥36፤ ፊል. 2፥9። ሰው ግን ራሱን ከፍ ቢያደርግ ይዋረዳል፤ ማቴ. 23፥12፤ 1ጴጥ. 5፥6።

**ኩላብ፤** በግድግዳ ወይም በምሰሶ ላይ የተተከለ የዕቃና የልብስ ማንጠልጠያ መስቀያ፤ ዘጸ. 27፥10፤ ሕዝ. 15፥3።

**ኩራት፤** ነጭ ሽንኩርት የሚመስል አትክልት፤ ዘኁ. 11፥5።

**ኩሲ፤** የአኪጦፌልን ምክር ከንቱ ያደረገ የዳዊት ወዳጅ፤ 2ሳሙ. 15፥32-37፤ 16፥16-19፤ 17፥5-16፤ 1ዜ.መ. 27፥33። አርካዊ ነበረ፤ ኢያሱ 16፥2።

**ኩሽ፤** የካም የመጀመሪያ ልጅ፤ ዘፍ. 10፥6-8፤ 1ዜ.መ. 1፥8-10። ኩሽ የሚለው የዕብራይስጥ ቃል አገርን ሲያመለክት «ኢትዮጵያ» ተብሎ ተተርጕሟል፤ ዘፍ. 2፥13።

**ኩብኩባ፤** «አንበጣ» ይመ.

**ኩፋሌ፤** ኩፋሌ ማለት መከፈል፥ መግመስ ማለት ነው። መጽሐፈ ኩፋሌ በአሪት ዘፍጥረትና በአሪት ዘጸአት ም. 1-12 የተጸፈውን ታሪክ አስፋፍቶ በመተረክ ዓመታትን ሁሉ የሚነግር መጽሐፍ ነው። የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤ.ክ. ሙሴ ጽፎታል በማለት ከብ. ኪ. መጻሕፍት ጋር ቈጥራ ትቀበለዋለች፤ ሌሎች አብ.ክ. ግን አይቀበሉትም።

**ኪልቅያ፤** ከቀጰዶቅያ በስተደቡብ ያለ አገር። ዋና ከተማው ጠርሴስ ነበረ፤ ሐ.ሥ. 21፥39። ጳውሎስ ወንጌልን በዚያ ሰበከ፤ አብ. ክ.ንም አጸና፤ ሐ.ሥ. 9፥30፤ 15፥23፡41፤ ገላ. 1፥21። ካ. ፮ኘ።

**ኪሩብ፤** ኪሩቤል (በዕብራይስጥ ኪሩቤም)፤ ብዙ ጊዜ በመ.ቅ. ውስጥ የተጠቀሱ ሰማያውያን ፍጥረቶች። በኃጢአት የወደቀው የሰው ልጅ ወደነበረበት ወደ ዔድን ገነት ለመመለስ እንዳይችል መንገዱን ይጠብቁ ዘንድ እግዚአብሔር ኪሩቤልን አኖረ፤ ዘፍ. 3፥24።

እግዚአብሔር የእስራኤልን ልጆች በተገናኘበት በመገናኛው ድንኳን ውስጥ በስርየት መክደኛው ላይ ሁለት ኪሩቤል ከወርቅ ተሠርተው ነበር። ክንፎቻቸውን ወደ ላይ ይዘረጋሉ። ፊታቸውም እርስ በእርሱ ይተያያል። ወደ ስርየት መክደኛውም ይመለከታሉ፤ ዘጸ. 25፥18-22።

በድንኳኑ መጋረጃዎችም ላይ የኪሩቤል ምስል ይታይ ነበር፤ ዘጸ. 26፥1። እግዚአብሔር በኪሩቤል መካከል ሆኖ ለእስራኤል ይናገር ነበር፤ ዘኁ. 7፥89። በኪሩቤል ላይ ይቀመጥ ነበር የሚሉም አሉ፤ 1ሳሙ. 4፥4።

ንጉሥ ሰሎሞን ቤተ መቅደሱን በሠራ ጊዜ በቅድስተ ቅዱሳን ውስጥ ከወይራ እንጨት የተሠሩትን ሁለት የኪሩቤል ምስሎች አቆመ፤ 1ነገ. 6፥23።

ለነቢዩ ሕዝቅኤል የታዩት ኪሩቤል የሰው፥ የአንበሳ፥ የላም (የበሬ) የንስርም ፊት ነበራቸው፤ ሕዝ. 1፥5-28። ሐዋርያው ዮሐንስም በእግዚአብሔር ዙፋን ፊት ሲቆሙ የተመለከታቸው አራቱ እንስሶች የተባሉት፥ እነዚህን የሚመስሉ ናቸው። ዓይኖችም ሞልተውባቸዋል ተብሏል። ይህም እግዚአብሔር ሁሉንም ነገር ያያል፤ ከፊቱም የተሰወረ ነገር የለም ማለት ነው፤ ሕዝ. 10፥12። ሕዝቅኤል ያያቸው ኪሩቤል ለእያንዳንዳቸው አራት አራት ፊትና ክንፍ አላቸው፤ ሕዝ. 10፥21። ኪሩቤል የእግዚአብሔርን

ቅድስናና ግርማ የሚገልጡ መናፍስት እንደ መሆናቸው መጠን በዙፋኑ ፊት እየቆሙ ፦ «ቅዱስ፥ ቅዱስ፥ ቅዱስ፥ የነበረውና ያለው የሚመጣውም ሁሉንም የሚገዛ ጌታ አምላክ» በማለት ክብርና ምስጋና ያቀርባሉ፤ ራእ. 4፥6-9።

**ኪራም**፤ 1. የዳዊት ወዳጅ የነበረ የጢሮስ ንጉሥ። ለዳዊት ቤት ሠራለት፤ 2ሳሙ. 5፥11። ሰሎሞንንም ለእግዚአብሔር ቤት ሥራ ከኪራም ክፍለ ግዛት እንጨት አስመጣ፤ 1ነገ. 5፤ 2ዜ.መ. 2፥3-16፤ 1ነገ. 9፥10-14። 2. የጢሮስ ንጉሥ ኪራም ለሰሎሞን የላከው ብልህ ሠራተኛ ኪራም ወይም ሑራም ይባል ነበር፤ 1ነገ. 7፥13-47፤ 2ዜ.መ. 2፥7:13:14፤ 4፥11-18።

**ኪቲም**፤ የያዋን ልጅ፤ ዘፍ. 10፥4። በመርከብ ንግድ የሚተዳደር በቆጵሮስና በሌሎችም ደሴቶች የሚኖር የነበረው ዘር፤ ዘኁ. 24፥24፤ ኢሳ. 23፥12፤ ኤር. 2፥10፤ ሕዝ. 27፥6።

**ኪኔሬት**፤ ከገሊላ ባሕር በሰሜናዊ ምዕራብ በኩል የሚገኝ ሜዳ፤ 1ነገ. 15፥20። በብ. ኪ. ዘመን የገሊላ ባሕር የኪኔሬት ባሕር ይባል ነበር፤ ዘኁ. 34፥11። በአ.ኪ. ዘመን ግን ኪኔሬት ጌንሳሬጥ ተብሏል፤ ሉቃ. 5፥1።

**ኪነ ጥበብ**፤ የልዩ ልዩ ተግባረ እድ ፦ የዜማ፥ የድርሰት፥ የዘፈንም ሙያና ሥራ። እስራኤል ምስሎችን እንዳይቀርጹ ስለ ተከለከሉ ከጥቂቶች በቀር በሥዕልና በቅርጽ ሥራ ልምምድ አልነበራቸውም፤ ዘጸ. 20፥4፤ 35፥30-35። ሰሎሞን ቤተ መቅደስ ለመሥራትና ለማስጌጥ ከፊንቄ ሠራተኞችን ቀጠረ፤ 1ነገ. 5፥6-18፤ 2ዜ.መ. 2፥13:14። ዕብራውያን ብዙ የዘፈንና የዜማ ችሎታ ነበራቸው፥ ግጥማቸውና ድርሰታቸው ከጥንታዊው ዓለም ድርሰት ጋር ይወዳደራል።

**ኪዳን**፤ «መጽሐፈ ኪዳን» ይመ.

**ካህን**፤ ክህነት፤ በእግዚአብሔርና በሰው መካከል ሆኖ ሰውን ከእግዚአብሔር ጋር የሚያገናኝ ካህን ይባላል። አገልግሎቱ መሥዋዕትን በመሠዋትና ጸሎትን በመጸለይ ይፈጸማል። ካህን በማንኛውም ሃይማኖት አለ፤ ዘፍ. 41፥45፤ 1ሳሙ. 6፥2፤ ሐ.ሥ. 14፥13። በመጀመሪያ እንደ ቃየልና እንደ አቤል ሰው ለራሱ የራሱን መሥዋዕት አቅራቢና ሠዊ ነበረ (ዘፍ. 4፥3:4)፥ በኋላም እንደ ኖኅና እንደ አብርሃም አባት ለቤተሰቡ ይሠዋ ነበር፤ ዘፍ. 8፥20፤ 12፥7፤ 13፥18።

ሕግ ሲሰጥ ግን አሮንና ልጆቹ ለእስራኤል ካህናት እንዲሆኑ ተመረጡ፤ ዘጸ. 28፥1። ከአሮን ቤተሰብ ውጭ የሌዊ ዘሮች በመቅደስ ያገለግሉ ነበር እንጂ መሥዋዕትን አልሠውም፤ ዘኁ. 3፥5-10።

ሆኖም ከአሮን ልጆች ያልሆነ ሌላ ሰው ቢሆንም እግዚአብሔር ራሱን ከገለጠለት እንደ እነጌዴዎን መሥዋዕትን ይሠዋ ነበር (መሳ. 6፥18-26፤ 13፥16)፤ እንደዚሁም የእግዚአብሔር ካህናት ሲጠፉ ኤልያስ መሥዋዕትን ሠዋ፤ 1ነገ. 18፥30። ከአሮን ልጆችም ነውር ያለበት ከተገኘ፥ አይሾምም ነበር፤ ዘሌ. 21፥16-24። አሮንና ልጆቹ ሲሾሙ ልዩ ልብስ ለብሰው በዘይት ይቀቡ ነበር፤ ዘጸ. 28፥40፤ ዘሌ. 8። አገልግሎታቸውንም በብዙ ጥንቃቄ እንዲፈጽሙ ታዘዙ፤ ዘጸ. 30፥17-21። በዚያን ጊዜ የካህናት ሥራ፥ በመቅደስ ማገልገል (ዘኁ. 16፥40፤ 18፥5)፥ ሕግን ለሕዝብ ማስተማር (2ዜ.መ. 15፥3፤ ሕዝ. 7፥26)፥ በኡሪምና በቱሚም የእግዚአብሔርን ፈቃድ መጠየቅ (ዘጸ. 28፥30፤ ዕዝ. 2፥63)፥ ተላላፊ በሽታ ያለባቸውንም መለየት ነበር፤ ዘሌ. 13፥1-3።

የቤተ መቅደስን አገልግሎት በ3 ልንከፍለው እንችላለን ፦

1ኛ. ዕለታዊ አገልግሎት፤ ይህ ጧትና ማታ የሚቃጠል መሥዋዕትን የመሠዋት፥ በቅድስት መብራቶችን የማብራት፥ ዕጣን የማጠን፥ ሰው የሚያመጣውን መሥዋዕትም በያይነቱ የማቅረብ አገልግሎት ነበረ፤ ዘጸ. 29፥38:39፤ 30፥1:7:8።



የእስራኤል ካህን

2ኛ. ሳምንታዊ አገልግሎት፤ በየሰንበቱ ዐሥራ ሁለት የመገኘቱን ኅብስት (ኅብስተ ገጽ) በገበታው ላይ የማኖር አገልግሎት ነው፤ ዘሌ. 24፥5-9።

3ኛ. ዓመታዊ አገልግሎት፤ በማስተሥረያ ቀን ልዩ ሥርዓትን የመፈጸም አገልግሎት ነው (ዘሌ. 16)።

ክርስቶስ እንደ መልከ ጼዴቅ ካህን ሆኖ ለኃጢአት ሁሉ የሚበቃውን መሥዋዕት አቅርቧልና

የአሮንን ክህነት አስቀርቷል፤ ዕብ. 7፥11-28። የክህነቱን ሥራ የፈጸመው በምድራዊ መቅደስ ሳይሆን፥ በሰማያዊ መቅደስ፥ በእንስሳት ደም ሳይሆን፥ በራሱ ደም ነው፤ ዕብ. 9፥11:12። አሁን ለኃጢአት ሌላ የደም መሥዋዕት ማቅረብ አያስፈልግም፥ ሆኖም ምእመናን ሁሉ በክርስቶስ ሥራ መሠረት መንፈሳዊ መሥዋዕትን ለእግዚአብሔር ስለሚያቀርቡ፥ በሚሰጡት ምስክርነትም ሰዎችን ወደ እግዚአብሔር ስለሚያደርሱ፥ ካህናት ተብለዋል፤ ሮም 12፥1፤ ዕብ. 10፥19-25፤ 13፥15፤ 1ጴጥ. 2፥5:9፤ ራእ. 1፥5:6። «ሊቀ ካህናት»፥ «መሥዋዕት»፥ «የቤተ ክርስቲያን አስተዳደር» ይመ.

**ካሌብ**፤ ከይሁዳ ወገን የሆነ የዮፎኒ ልጅ። ከነዓንን እንዲሰልሉ ከተላኩት ከዐሥራ ሁለቱ ሰዎች አንዱ ነበረ፤ ዘኍ. 13፥6፤ 14። አገሩን ሰልለው በተመለሱ ጊዜ ዐሥሩ ሰላዮች ፦ የአገሩ ሰዎች ኃያላን ናቸው፥ ልናሸንፋቸው አንችልም በማለት በእስራኤል መካከል ጥርጣሬንና ጕርምርምታን ሲፈጥሩ፥ ካሌብ ከኢያሱ ጋር ሆኖ ፦ «እንችላለን፥ እግዚአብሔር ከእኛ ጋር ይሆናል፥ በርቱ፥ እንውጣ፥ አገሩንም እንውረስ» እያለ ሕዝቡን አደፋፈረ።

እነዚያ አጕረምራሚዎች በሙሉ በምድረ በዳ ከሞቱ በኋላ በእምነታቸው ምክንያት ወደ ከነዓን ሊገቡ የተፈቀደላቸው ካሌብና ኢያሱ ብቻ ናቸው፤ ዘኍ. 14፥22-30። ከገቡም በኋላ ኬብሮንና አካባቢው ለካሌብ ተሰጠ፤ ኢያሱ 14፥6-15።

**ካም**፤ ከኖኅ ልጆች አንዱ፤ ዘፍ. 5፥32፤ 6፥10። ከጥፋት ውሃ ዳነ፤ ዘፍ. 7፥13፤ 9፥18። የአባቱን ራቁትነት አይቶ ለወንድሞቹ ነገረ፥ በእርሱም ምክንያት ልጁ ከነዓን ተረገመ፤ ዘፍ. 9፥20-27። አራት ልጆችን በመውለዱ የብዙ ሕዝብ አባት ሆነ፤ ዘፍ. 10፥6-20። የግብጻውያን አባት ስለሆነ አንዳንዴ «ካም» ማለት «ግብጽ» ማለት ነው፤ መዝ. 105፥23:27።

**ካሞሽ**፤ ከሞስ፤ የሞዓባውያን አምላክ፤ ዘኍ. 21፥29፤ ኤር. 48፥7:13:46። አሞናውያንም ያመልኩት ነበር፤ መሳ. 11፥24። ሰሎሞን ሚስቶቹን ለማስደሰት ይህን የካሞሽ አምልኮት ወደ ኢየሩሳሌም አስገባ፤ 1ነገ. 11፥7:33።

**ካራ**፤ እንደ ቢላዋ ያለ፥ ባለ አንድ አፍ የሆነ ማረጃ። የጽኑ ትዕግሥት ምሳሌ ነው፤ ምሳ. 23፥2።

**ካራን**፤ በነነዌና በኤፍራጥስ ወንዝ መካከል የነበረ ከተማ። የአብርሃም አባት ታራ በካራን ሞተ (ዘፍ. 11፥32)፥ አብርሃም በካራን ሳለ እግዚአብሔር ጠራው። ርብቃ በካራን አደገች፤ ያዕቆብም በዚያ ልያንና ራሔልን አገባ፤ ዘፍ. 11፥32፤ 12፥1-5፤ 24፥4፤ 27፥43፤ 29፥4:5። ካ. 1ለ።

**ካርሲት፥ የካርሲት በር**፤ የሸክላ ሠሪዎች ምሥራቃዊ በር። ቃሉ የዕብራይስጥ ቃል ነው፤ ኤር. 19፥2።

**ካስማ**፤ የድንኳን አውታር መወጠሪያ ቈላፋ ችካል (ዘጸ. 27፥19፤ መሳ. 4፥21)፥ የተስፋ ምሳሌ ነው፤ ኢሳ. 33፥20፤ 54፥2።

**ካሴሉ**፤ «ወር» ይመ.

**ካደ**፤ ሰው የእግዚአብሔርን ጸጋ ከተለማመደ በኋላ እግዚአብሔርን ከመከተል ቢመለስ፥ እግዚአብሔርን ወይም ሃይማኖትን ካደ ይባላል። ሳኦል፥ ሄሜኔዎስና ዴማስ የክህደት (የከሃዲዎች) ምሳሌዎች ናቸው፤ 1ሳሙ. 15፥11፤ 2ጢሞ. 2፥18፤ 4፥10። ብዙ ጊዜ ሰዎች የሚክዱት ሐሰተኞችን ስለሚሰሙ ነው (ገላ. 1፥6-9፤ 2፥4፤ 2ጢሞ. 4፥3:4፤ 2ጴጥ. 2፥1:2፤ ይሁዳ 3:4)፥ በስደት ጊዜ ክህደት ይበዛል፤ በዓለም መጨረሻም ከፍ ያለ ክህደት ይሆናል፤ ማቴ. 24፥10፤ ሉቃ. 8፥13፤ 2ተሰ. 2፥4። ሃይማኖትን እንዳንክድ ብዙ ማስጠንቀቂያ ተሰጥቷል፤ 1ጢሞ. 4፥1-3፤ 2ጴጥ. 3፥17። ይልቁንም ሰው እውነትን ከተረዳ በኋላ ቢክድ፥ በንስሐ መታደስ የሚችል አይመስልም፤ ዕብ. 6፥4-6፤ 10፥26።

**ካፊያ**፤ ሲዘንም የማይሰማ ልዝብ ዝናም። በማስተዋል የመናገር ምሳሌ ነው፤ ዘዳ. 32፥2።

**ኬልቄዶን**፤ አረንጓዴ ቀለም ያለው የከበረ ድንጋይ፤ ዘጸ. 39፥12፤ ራእ. 21፥19።

**ኬልቅያስ**፤ ትርጕሙ «ዕድል ፈንታዬ እግዚአብሔር ነው» ማለት ነው። በኢዮስያስ ዘመነ መንግሥት የካህናት አለቃ ነበረ። የሕጉንም መጽሐፍ አገኘ፤ 2ነገ. 22፥8፤ 2ዜ.መ. 34፥14። በዚህ ስም ሌሎች ሰባት ሰዎች ተጠርተዋል።

**ኬብሮን**፤ ኅብረት ማለት ነው። ከኢየሩሳሌም በስተደቡብ 30 ኪ.ሜ. ርቆ ያለ የከነዓናውያን ከተማ። አስቀድሞ ቂርያት አርባቅ ይባል ነበር፤ ኢያሱ 14፥15። ኬብሮን ከባሕሩ ጠለል 927 ሜትር ከፍ ይላል። ከኢየሩሳሌምና ከሌሎች የከነዓን ከተማዎች ከፍታ አለው። አብርሃም በኬብሮን ሰፈረ (ዘፍ. 13፥18)፥ የመቃብርም ቦታ በኬብሮን ገዛ፤ አብርሃምና ሣራ፥ ይስሐቅና ርብቃ፥ ያዕቆብና ልያ በኬብሮን ተቀበሩ፤ ዘፍ. 23፤ 49፥31፤ 50፥13። ዛሬ በመቃብሮቹ ላይ መስጊድ ተሠርቷል። የእስልምና ተከታዮች ቦታውን ይጠብቃሉ። ኢያሱ ኬብሮንን ለካሌብ ሰጠ፤ ኢያሱ 14፥6-15። ኬብሮን ለ7 ዓመት የዳዊት መናገሻ ከተማ ነበረ፤ 2ሳሙ. 5፥5። አቤሴሎም በኬብሮን ተወለደ፥ በዚያም በዳዊት ላይ ዐመፀ፤ 2ሳሙ. 15፥10። ካ. 2ለ።

**ኬጡራ**፤ ሣራ ከሞተች በኋላ አብርሃም ያገባት ሁለተኛ ሚስቱ። የዓረብ ሕዝቦች አባቶች የሆኑትን ስድስት ልጆች የወለደችለት፤ ዘፍ. 25፥1-6፤ 1ዜ.መ. 1፥32:33።

**ኬጢያውያን**፤ (ኬጢዎን)። ከከነዓን የተገኘ ወገን፤ ዘፍ. 10፥15። ዋና አገራቸው ከከነዓን በስተሰሜን በኩል ሲሆን፥ በከነዓንም ይኖሩ ነበር፤ ዘፍ. 23፥3፤ 26፥34፤ 2ዜ.መ. 8፥7። በ717 ከክ. በ. አሦራውያን የኬጢያውያንን ዋና ከተማ ከርከሚሽን ሲይዙ መንግሥታቸው ጠከመ።

**ክህደት**፤ «ካደ» ይመ.

**ክራር፤** የበገና ዓይነት የዜማ ዕቃ፤ ዳን. 3፥5:7። የአሁኑ ክራር ስድስት የጅማት አውታሮች ይገኙበታል።

**ክርስቲሎቤ፤** ብጫ መልክ ያለው የከበረ ድንጋይ፤ ራእ. 21፥20።

**ክርስቲያን፤** የክርስቶስ ተከታይ፣ የክርስቶስ ደቀ መዝሙር። ምእመናን መጀመሪያ በአንጾኪያ ክርስቲያን ተባሉ፤ ሐሥ. 11፥26፤ 26፥28፤ 1ጴጥ. 4፥16።

**ክርስቶስ፤** «ኢየሱስ»፣ «መሢሕ» ይመ.

**ክርስጵራስስ፤** ብጫና አረንጓዴ ኅብረ ቀለም ያለው የከበረ ድንጋይ እንደሆነ ይታሰባል፤ ራእ. 21፥20።

**ክርታስ፤** ለመጻፊያ የሚያገለግል ወፍራም ወረቀት። ከእንስሳ ቆዳ የሚሠራውም የብራና ጥቅልል ክርታስ ይባላል፤ ኤር. 36፥4-6።



የክርታስ ጥቅልል

**ክርክር፤** በአሳብ ልዩነት ሳቢያ፣ የራስን አሳብ ወይም አስተያየት አጥብቆ ማቅረብ። በክርክር ምክንያት የእርስ በርስ መዋደድና ኅብረት ሊበላሽ ይችላል፤ 1ቆሮ. 1፥10:11። አጉል ክርክር የሥጋ ሥራ ነው፣ ለምእመናንም ተገቢ አይደለም፤ ገላ. 5፥20:26፤ ሮም 1፥29፤ 13፥13፤ 1ቆሮ. 3፥3፤ 2ቆሮ. 12፥20፤ 1ጢሞ. 6፥4፤ ቲቶ 3፥9።

**ክርፋት፤** ከቆሻሻ ነገር የሚነሣ መጥፎ ሽታ፣ ድካምንና መሸነፍን ሊያመለክት ይችላል፤ ኢዩ. 2፥20።

**ክሳት፤** ከምግብ ጕድለት፣ ከሳንባ በሽታና ከመሳሰለውም የሚመጣ ሁኔታ፤ ዘሌ. 26፥16። «በሽታ» ይመ.

**ክሳድ፤** አንገት፣ «የቀሚስ ክሳድ» ሲል የቀሚስ አንገት ማለት ነው፤ ኢዮብ 30፥18።

**ክብረ በዓል፤** ሕዝብ የሚያከብረው ታላቅ በዓል። ክብረ በዓል ሲባል በተለይ በበዓሉ ዕለት የሚደረገውን ወግና ሥርዓት ያመለክታል፤ ሕዝ. 46፥9:11። «በዓላት» ይመ.

**ክብር፤** ቃሉ ጌትነትንና ከፍተኛነትን፣ ብርሃንነትን፣ ዋጋንና ጥቅምንም አጠቃልሎ ይዟል። እግዚአብሔር በሥራው ሲገለጥ፣ ክብሩ ይታያል፤ መዝ. 19፥1፤ ዘጸ. 16፥7:10፤ 1ነገ. 8፥11፤ ኢሳ. 6፥3። ክብሩ ሊገለጥበት በሚፈቅደው ምሳሌ ይታያል እንጂ፣ ሰው በሙላት የእግዚአብሔርን ክብር ሊያይ አይችልም፤ ዘጸ. 33፥17-23። የእግዚአብሔር ፍጥረት ሁሉ ክብር አለው፤ ሉቃ. 2፥9፤ 1ቆሮ. 11፥7፤ 15፥41። በተለይ የእግዚአብሔር ክብር በክርስቶስ ተገልጧል፤ ዮሐ. 1፥14፤ ዕብ. 1፥3። የክርስቶስ ክብር በተአምራቱ (ዮሐ. 2፥11)፣ በደብረ ታቦር (ማቴ. 17፥1-8)፣ በሕማማቱ (ዮሐ. 12፥23-38)፣ በትንሣኤውና በዕርገቱ (1ጴጥ. 1፥20:21) ተገልጧል። በዳግም ምጽአቱም ይታያል፤ ማር. 8፥38። ምእመናን አሁን ከእግዚአብሔር ጋር ሲገናኙ፣ ክብር ይታይባቸዋል (2ቆሮ. 3፥7:18)፤ ለወደፊቱም በፍርድ ቀን እንደ ሥራቸው ከእግዚአብሔር ክብርን ይቀበላሉ፤ የክርስቶስን መከራ በትዕግሥት የሚካፈሉ ሁሉ ክብሩን ይካፈላሉ፤ ዮሐ. 17፥22-24፤ ሮም 8፥17:21፤ 1ቆሮ. 15፥43፤ ቆላ. 3፥4። ሰዎችን ሁሉ ማክበር (1ጴጥ. 2፥17)፣ እንደ ማዕርጋቸውም ክብርን መስጠት ታዟል፤ ሮም 13፥7። ነገር ግን ከሁሉ በላይ ለእግዚአብሔር ክብርን መስጠት ይገባል፤ ይሁዳ 25።

**ክብደት፤** በጥንት ዘመን የክብደት መለኪያዎች ነበሩ። ዳዊት ሚዛን አቆመ፤ 2ሳሙ. 14፥26። እስራኤል በትክክለኛ ሚዛን እንዲሠሩ ታዘዙ፤ ዘሌ. 19፥36፤ ዘዳ. 25፥13፤ ምሳ. 11፥1፤ 20፥23፤ ሚክ. 6፥11። ሆኖም ሚዛኖች በየአገሩ የተለያዩ ስለነበሩ፣ ምን ያህል እንደነበሩ ለመግለጥ ያስቸግራል። በብ. ኪ. መክሊት (30 ኪሎ ግራም ያህል)፣ ምናን (500 ግራም ያህል)፣ ሰቅል (12 ግራም ያህል)፣ አቦሊ (የሰቅል ሃያኛው ክፍል) ተጠቅሷል። በአ. ኪ. ንጥር (327.45 ግራም)፣ ታላንት (40 ኪሎ ግራም ያህል) የተሰኙት የክብደት መለኪያዎች ተጠቅሰዋል።



በአንበሳ መልክ የተቀረጸ «ምናን» ተብሎ የተጻፈበት የአሦር ንጉሥ የስልምናሶር የድንጋይ ሚዛን.

**ክትክታ፤** በወይናደጋና በቆላ የሚበቅል፣ ጨሬታ እንጂ ረጅም ዛፍ ሆኖ ሊያድግ የማይችል፣ ጥንካሬ ያለው እንጨት፤ 1ነገ. 19፥4፤ ኢዮብ 30፥4።

**ክንድ፤** ከጣት ጫፍ እስከ ክንድ ማጠፊያ ያለው መለኪያ ሲሆን፣ አምሳ ሳንቲ ሜትር ያህል ይሆናል፤ ዘዳ. 3፥11። የኃይል (ዘጸ. 6፥6፤ ኢሳ. 51፥9)፣ የደኅንነት ምሳሌ ነው፤ ዘዳ. 33፥27። እግዚአብሔር የሰውን ክንድ ያጸናል፤ መዝ. 18፥34፤ ሕዝ. 30፥25። «ርዝመት» ይመ.

**ክፋት፤** ለሰው ጉዳት የሚሆን ሁሉ ክፋት ይባላል። ክፋት በኃጢአት ምክንያት ወደ ዓለም ገባ፤ ሰው ኃጢአት ስለሠራ፥ እግዚአብሔር በሰው ላይ ፈርዶ ቅጣትን ወሰነ፤ ዮናስ 3፥10። በትንቢተ ኢሳይያስ 45፥7 ላይ እግዚአብሔር «ክፋትን እፈጥራለሁ» ይላል። ሰዎች ኃጢአትን በሠሩ ጊዜ ክፉ ሰዎችን አስነሥቶ የሚቀጣ መሆኑን ያሳያል፤ ዕን. 1፥2-7።

**ክፍል፤** ብዙ ጊዜ የሰውን የአካል ክፍል፥ በምሳሌም የምእመናንን አንድነትና የተለያየ አገልግሎት ያመለክታል፤ ማቴ. 5፥29፤ ሮም 6፥13፤ 7፥5:23፤ 12፥4፤ 1ቆሮ. 6፥15፤ 12፥26፤ ያዕ. 3፥5፤ 4፥1። የአንድ ነገር ምድብ ወይም ድርሻ፤ ኢያሱ 18፥9፤ 19፥9። የቀንና የሌሊትን ክፍለ ጊዜ ያመለክታል። «ቀን»፥ «ሌሊት» ይመ.

**ኮምበል፤** (ኮንበል)፤ በግእዝ ባሉጥ ተብሎ የሚጠራ አንድ ዐይነት ትልቅ ዛፍ፤ ሆሴዕ 4፥13፤ ሕዝ. 27፥6።

**ኮረብታ፤** ከፍ ያለ መሬት፤ ጉብታ። ከነዓናውያን በየኮረብታው መስገጃ ሠርተው ለአማልክታቸው ይሠው ነበር። እስራኤል የኮረብታ መስገጃዎችን እንዲያጠፉ ታዘዙ፤ ዘኁ. 33፥52፤ ዘዳ. 33፥29። እስራኤላውያን ከነዓንን ከያዙ በኋላ በአንዳንድ ኮረብታዎች ላይ ለእግዚአብሔር መሥዋዕት ማቅረብ ጀመሩ፤ 1ሳሙ. 9፥12፤ 1ነገ. 3፥1-4። ከእግዚአብሔር ሲርቁም ለከነዓን አማልክት በኮረብታዎች ላይ ሠው፤ 1ነገ. 12፥32፤ 14፥23። ከዚህ አምልኮት ጋር ብዙ ዓይነት አስጸያፊ ድርጊትም ይፈጸም ነበር፤ 1ነገ. 14፥24፤ ኤር. 3፥2፤ ሆሴዕ 4፥11-14። ቤተ መቅደስ ከተሠራ በኋላ እንኳን እስራኤል በአንዳንድ ኮረብታዎች ላይ ለእግዚአብሔር ይሠው ነበር፤ 1ነገ. 15፥11-14፤ 18፥20:30። ሕዝቅያስና ኢዮስያስ ግን በዚህ ባዕድ አምልኮ ምክንያት የእግዚአብሔር ቍጣ በሕዝቡ ላይ እንደመጣ ተረድተው፥ የኮረብታዎችን መስገጃዎች ሁሉ አፈረሱ፤ 1ነገ. 13፥1-6፤ 2ነገ. 18፥4:22፤ 23፥5-8:15።

**ኮራት፤** ከኢያሪኮ በስተምዕራብ በኩል የሚገኝ ቦታ። ፈፋ ስለሚገኝበት፥ ኤልያስ በእግዚአብሔር ትእዛዝ በኮራት ተሸሸገ፤ 1ነገ. 17፥1-7።

**ኮራዚ፤** (ኮራዚን)፤ ከቅፍርናሆም በስተሰሜን 3 ኪ.ሜ. ርቆ የሚገኝ መንደር። ክርስቶስ በዚህ ቦታ ተአምራት አደረገ። ነገር ግን የኮራዚ ሕዝብ አላመኑበትም፤ ስለዚህም ያን አገር ወቀሰ፤ ማቴ. 11፥21፤ ሉቃ. 10፥13።

**ኮሬብ፤** «ሲና» ይመ.

**ኮር፤** መጠኑ ትልቅ የሆነ የፈሳሽ ነገር መስፈሪያ። ሁለት መቶ ሃያ ሊትር ያህል ነው፤ 1ነገ. 4፥22፤ 5፥11። «መስፈሪያ» ይመ.

**ኮርማ፤** እንስት ከብቶችን የሚሰር፥ የሚያጠቃ ተባት ከብት ኮርማ በሬ ይባላል። ኮርማ የሚባለው ያላረጀና ቀለሙ ያልተቀጠቀጠ፥ ያልተሰነጋ ነው፤ መዝ. 114፥4፤ ኢዮብ 21፥10፤ ዕብ. 10፥4።

**ኮከብ፤ ከዋክብት፤** (በንዳንድ ጥቅስ ላይ የሰማይ ሠራዊት ተብለዋል)። በእግዚአብሔር ስለተፈጠሩና ብዛታቸውና ስማቸውም በእርሱ ስለተወሰኑ፥ የእርሱን ክብርና ታላቅነት ያሳውቃሉ፤ ዘፍ. 1፥16፤ አሞጽ 5፥8፤ 2ነገ. 23፥5፤ ኢዮብ 22፥12፤ መዝ. 8፥3:4፤ 19፥1፤ 146፥4:5። የከዋክብት ብዛት የእግዚአብሔር ልግስና ምልክት ነው። በዚህም ምልክት ዘሩ እንዲበዛ ለአብርሃም ተስፋ ተሰጠ፤ ዘፍ. 15፥5፤ 22፥17፤ ነህ. 9፥23፤ ዕብ. 11፥12። ነቢያትና ኢየሱስ ክርስቶስ ስለ ዓለም መቀጀትና ስለ ፍጻሜው፥ ስለ ፍርድም ትንቢት ሲናገሩ፥ ከዋክብት የሚጨልሙና የሚወድቁ መሆናቸውን ገልጠዋል፤ ኢሳ. 13፥10፤ ዳን. 8፥10፤ ኢዩ. 3፥15፤ ማቴ. 24፥29፤ ራእ. 6፥13፤ 8፥10-12።

ለከዋክብት መስገድ ለጥንታውያን ሰዎች እንቅፋት ነበረ። እግዚአብሔርም ለከዋክብት እንዳይሰገድ ከለከለ፤ ዘዳ. 4፥19፤ 2ነገ. 17፥16፤ አሞጽ 5፥26፤ ሐ.ሥ. 7፥43። በባቢሎንና በከነዓን ኮከብ ቈጣሪዎች የሚባሉ ምዋርተኞች ኮከብን በመመርመር ወደፊት የሚሆነውን ለመግለጽ ይሞክሩ ነበር። ይህ ዐይነቱ ሥራ ለእስራኤል ክልክል ነበረ፤ ኢሳ. 47፥13፤ ዳን. 2፥27። «ከላውዴውን» ይመ.

በስማቸው የተጠቀሱ ከዋክብት ማዛሮት፥ ሰባቱ ከዋክብት፥ ኦሪዮን፥ ድብ፥ የሬፋን ኮከብና የንጋት ኮከብ ናቸው። በየስማቸው ይመልከቱ። የቤተ ልሔም ኮከብ ሰብአ ሰገል (ጠቢባን) በምሥራቅ አገር ያዩት ታላቅ ኮከብ ነው። እንደገናም ከቤተ ልሔም ከተማ በላይ ታያቸው። ኮከቡ ለአይሁድ ንጉሥ መወለድ ምልክት እንደሆነ ተገለጠላቸው። ኮከቡ ምን ዓይነት እንደሆነ አልታወቀም፤ ማቴ. 2፥1-10። ኮከብ የሚል ቃል የክብር ምሳሌ ሆኖ በአንዳንድ ጥቅስ ይገኛል፤ ራእ. 1፥16፤ 12፥1።

**ኰልታፋ፤** በትክክል መናገር የማይችል፤ ዘጸ. 4፥10፤ ማር. 7፥32። «በሽታ» ይመ.

**ኰነነ፤** ለዘለዓለም አጠፋ። በዕብ. 11፥7 ኰነነ ሲል ለሌሎች ፍርድ እንደሚገባቸው መግለጫ ሆነ ማለት ነው። «ኵነኔ» ይመ.

**ኵላሊት፤** በሆድ ውስጥ ያሉ ሁለት ብልቶች። የእንስሳት ኵላሊት በመሠዊያ ይቃጠሉ ነበር፤ ዘጸ. 29፥13:22። ዕብራውያን የሰው ስሜት ከኵላሊት ይመነጫል ብለው ያስቡ ነበር፤ መዝ. 16፥7፤ 73፥21፤ ምሳ. 23፥16፤ ኤር. 11፥20።

**ኵላብ፤** «ኩላብ» ይመ.

**ኵል፤** ዐይንን ለማሳመር ወይም በሽታን ለማቃለል በዐይን ላይ የሚጨመር ቅባትና መድኃኒት። የጥንት ሴቶች ለማጌጥ ሲሞክሩ የዐይን ሽፋሽፍታቸውን በኵል ይኳሉ ነበር፤ 2ነገ. 9፥30። በምሳሌነትም ሰዎች መንፈሳዊ ነገርን ማስተዋል እንደሚችሉ ያሳያል፤ ኤር. 4፥30፤ ራእ. 3፥18።

**ኵራት፤** ትዕቢት። ሰው በእግዚአብሔር ፊት ብዙ ጕድለት ስላለበት ሊያኰራው የሚችል ነገር የለም፤ 1ሳሙ. 2፥3። «ትዕቢት» ይመ.

**ኵሬ፤** የውሃ ማጠራቀሚያ፤ ኢሳ. 7፥3። ሰሎሞን ለቤተ መቅደስ አገልግሎት የሚውል ሰፊ የሆነ ኵሬ ከናስ አሠርቶ ነበር፤ 1ነገ. 7፥23-26፤ 2ነገ. 25፥13።

**ኵርንችት፤** በቆላ ምድር የሚበቅል እንደ ሐረግ ያለ እሾህ ያለው ተክል፤ ኢሳ. 9፥18፤ ሕዝ. 2፥6።

**ኵርፍታ፤** መቀየም፥ አነስተኛ ቍጣ፤ ዘፍ. 49፥7።

**ኵስኵስት፤** ከሸክላ፥ ከናስ፥ ከብርና ከወርቅ የሚሠራ ጀበና የሚመስል ዕቃ። በምሳሌነት የሰውን ሕይወት ሊያመለክት ይችላል፤ መክ. 12፥6።

**ኵነኔ፤** የማይለወጥ፥ ለዘለዓለም በኃጢአተኞች ላይ ያለ የእግዚአብሔር ፍርድ። ሕጉን የተላለፉትን እግዚአብሔር ይኰንናቸዋል። ሰው ሁሉ ሕገ ልቡና፥ ሕገ ኦሪት ወይም ሕግ ወንጌል አለውና በተቀበለው ሕግ መሠረት ይፈረድበታል፤ ሮም 2፥12-16። በክርስቶስ ኢየሱስ በእምነት ያልተገኙ ይኰነናሉ፤ ዮሐ. 3፥18፤ ሮም 8፥1። ወንጌልን ዐውቀው የካዱ የባሰ ፍርድን ይቀበላሉ፤ ሉቃ. 10፥13-15፤ 12፥46-48። የኵነኔ ሁኔታ በጨለማና በእሳት ምሳሌነት ተገልጧል፤ ማቴ. 8፥12፤ ማር. 9፥45-48፤ ራእ. 20፥15። ሰው ከሞተ በኋላ ከኵነኔ ሊድን አይችልም፤ ሉቃ. 16፥26፤ ዕብ. 9፥27። ለዘለዓለም ከኵነኔ በታች ሆኖ ይኖራል፤ ማቴ. 25፥46፤ ማር. 9፥43-48፤ 2ተሰ. 1፥9፤ ራእ. 14፥11፤ 20፥10:15።

**ኵፋር፤** ባለ ቆብ ካባ፤ ኢዮብ 29፥14። በምሥራቅ ቤ.ክ. ሥርዓት መሠረት ካህን በማስተስረያ ጸሎት ጊዜ ይለብሰዋል።

**ወለላ፤** (የማር)። ከማር የሚፈስ የማር ውሃ፥ ወይም ከዱ የሌለው ንጹሕ ማር። የእግዚአብሔር ፍርድ (መዝ. 19፥9:10)፥ የመልካም ቃል (ምሳ. 16፥24)፥ የጥበብ ምሳሌ ነው፤ ምሳ. 24፥13:14።

**ወለድ፤** «ብድር» ይመ.

**ወላጆች፤** የወላጆች ዋና ሥራ ልጆቻቸውን በጥበብ ማሳደግ ነው፤ ምሳ. 1፥8፤ 4፤ 10፥1። ልጆቻቸው በተገቢ ሥርዓት እንዲያድጉ መጠበቅ፥ አስፈላጊም ሲሆን በበትር መቅጣት ይገባቸዋል፤ ምሳ. 13፥24፤ 22፥15፤ 23፥13:14፤ 29፥15። አባት ለልጆች የሃይማኖትን ትምህርት ያስተምራል፤ ዘጸ. 13፥8፤ ዘዳ. 4፥9፤ 6፥7:20-25። በብ.ኪ. ዘመን ወላጆች ለወንድ ልጅ 20 ዓመት እስኪሞላው ድረስ፥ ለሴት ልጅም እስክታገባ ድረስ ኀላፊዎች ነበሩ፤ ዘኍ. 1፥3፤ ዘዳ. 22፥15። በአ.ኪ.ም ወላጆች በማስተዋል ልጆቻቸውን እንዲያሳድጉ ታዝዘዋል፤ ኤፌ. 6፥4። «ልጆች» ይመ.

**ወልደ አዴር፤** (ወይም ቤን ሃዳድ)፤ የአዴር (የሃዳድ) ልጅ ማለት ነው። የሶርያ ነገሥታት የተሰየሙበት ስም። ሃዳድ የተባለው ከሶርያውያን አማልክት አንዱ ነበረ። በመ.ቅ. ወልደ አዴር በሚለው ስም የተጠቀሱት ሦስት ናቸው። በታሪክ መጻሕፍትም ቀዳማዊ፥ ዳግማዊና ሣልሳዊ ወልደ አዴር (ቤን ሃዳድ) እየተባሉ ይጠራሉ።

1. ቀዳማዊ ወልደ አዴር በይሁዳ ንጉሥ በአሳ ዘመነ መንግሥት በሶርያ ይገዛ ነበር። የእስራኤል ንጉሥ ባኦስ ይሁዳን ባስቸገረ ጊዜ፥ ወልደ አዴር እስራኤልን በመውረር ንጉሥ አሳን ረዳው፤ 1ነገ. 15፥18-21።

2. በ1ነገ. ም. 21 መጀመሪያ ላይ የተጠቀሰው ንጉሥ የፊተኛው ልጅ ነው በማለት ዳግማዊ ወልደ አዴር ይባላል። እስራኤልን ለመውጋት ቢነሣ ንጉሥ አክዓብ አሸነፈው፤ 1ነገ. 21፥16-43። በአንዳንድ ሊቃውንት አስተያየት ግን ይህ ንጉሥ ያው ቀዳማዊው ነው እንጂ ልጁ አይደለም ተብሏል።

3. ወልደ አዴር በሚለው ስም የተጠሩት ሦስት ናቸው የሚሉት ደግሞ፥ ሣልሳዊ ብለው የሚጠቅሱት በ2ነገ. 13፥3-13 ታሪኩ የተጻፈለትን የአዛሄልን ልጅ ነው።



የወልደ አዴር ስም የተጻፈበት የሶርያ አምላክ ቅርጽ

**ወልድ፤** ልጅ ማለት ነው። ይህ ስም ከዘለዓለም ከአብ ጋር ለነበረው ለእግዚአብሔር ወልድ የሆነ የህላዌ ስሙ ነው፤ ማቴ. 28፥19። ወልድ (ልጅ) ስለተባለ፥ ከአብ አያንስም፥ በአኗኗር (በህላዌ)፥ በክብርና በሥልጣን እኩል ነው፤ ዮሐ. 5፥19-24። «ኢየሱስ» ይመ.

**ወረቀት፤** 2ዮሐ. 12። «መጽሐፍ»፥ «ጥቅልል» ይመ.

**ወረደ፤** ከላይ ወደ ታች መጣ፤ በሰው አስተያየት እግዚአብሔር በሁሉ ቦታ የሚገኝ ሲሆን ከሰማይ ወደ ምድር ወረደ ይባላል፤ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ሲጠመቅ መንፈስ ቅዱስ በላዩ ወርዷል፤ ዘፍ. 11፥7፤ ዘጸ. 19፥18፤ 34፥5፤ ሉቃ. 3፥22፤ ሐ.ሥ. 10፥44፤ 1ተሰ. 4፥16። መላእክት ከሰማይ ወደ ምድር ወረዱ፤ ዘፍ. 28፥12፤ ማቴ. 28፥2፤ ዮሐ. 1፥52። ክርስቶስ ከሰማይ ወረደ፤ ዮሐ. 3፥13። ሰው ሲሞት ግን ክብሩን ወይም ሀብቱን ወደ መቃብሩ ይዞ አይወርድም፤ መዝ. 49፥17።

**ወራሽ፤** በመጀመሪያ ደረጃ ወራሽ ልጅ ነው። ልጅ ከሌለ ግን ቅርብ ዘምድና ያለው ይወርሳል፤ ዘፍ. 15፥3:4። በኵር ልጅ ሁለት እጅ ይቀበላል። «በኵር»፥ «ዋርሳ» ይመ.

በሙሴ ሕግ ወራሽ ወንድ ልጅ ብቻ ነበረ። ኋላ ግን ወንድ ልጅ ሳይኖር ሴት ልጅ እንድትወርስ ተፈቅዷል፤ ሴት ልጅም ከሌለች በግራና በቀኝ አካባቢ ያለ ዘመድ ይወርሳል፤ ዘኍ. 27፥1-11። ወራሽነት በኑዛዜ ይጸናል፤ ዕብ. 9፥15:16። እግዚአብሔር የዓለም ወራሽ እንዲሆን ለአብርሃምና ለዘሩ ተስፋ ሰጠ፤ ዘፍ. 15፥3:4፤ 21፥10፤ ሮም 4፥13። ይህም የተፈጸመው በክርስቶስ ነው። እርሱ የእስራኤል (ማር. 12፥7)፥ የሁሉም ወራሽ ነው፤ ዕብ. 1፥2። እንደዚሁም በክርስቶስ የሚያምኑ ወራሾች ናቸው፤ ሮም 4፥14፤ 8፥17፤ ገላ. 3፥29። «ርስት» ይመ.

**ወራውሬ፤** የከበረ ድንጋይ፤ ራእ. 21፥20። ምናልባት እንደ ቶጳዝዮን ብጫ ዓይነት መልክ ያለው ሊሆን ይችላል።

**ወር፤** የእስራኤላውያን ወር በጨረቃ ይቈጠር ነበር (መባቻ ይመ.)። በፀሐይ ዑደት ላይ ከተመሠረተው የዓመት አቈጣጠር ጋር እንዲስማማ በዐሥራ ዘጠኝ ዓመታት ውስጥ ሰባት ጊዜ 30 ቀን ያለው ዐሥራ ሦስተኛ ወር ጭማሪ ይገባ ነበር። እንዲ ወር ጭማሪ የሚገባውም በ3ኛው፥ በ6ኛው፥

| ከምርኮ በፊት የወር ስም | ከምርኮ በኋላ የወር ስም | ወሩ የተጠቀሰበት ስፍራ | የኢትዮጵያ ወር | የግብርና ሁኔታ በእስራኤል አገር | በዓላት | በዓሉ የሚከበርበት ቀን |
|---|---|---|---|---|---|---|
| አቢብ | ኒሳን | ዘጸ. 12፥2<br>፤ 13፥4<br>ነህ. 2፥1 | ሚያዝያ | የኋለኛው ዝናብ<br>የገብስ አጨዳ | የፋሲካ በዓል<br>የቂጣ በዓል<br>የበኵራት<br>ነዶ በዓል | 14<br>15-21<br>16 |
| ዚፍ | (ኢያር) | 1 ነገ. 6፥1<br>: 37 | ግንቦት | በጋ | | |
| | (ሲዋን) | | ሰኔ | የገብስ አጨዳ<br>ማስቂያ | በዓለ ኀምሳ | 6 |
| | ተሙዝ | ሕዝ. 8፥14 | ሐምሌ | ወይን ለቀማ | | |
| | (አብ) | | ነሐሴ | ወይራ ለቀማ | | |
| | ኤሉል | ነህ. 6፥15 | መስከረም | የኋለኛው በለስ ለቀማ | | |
| ኤታኒም | (ቶስሪ) | 1 ነገ. 8፥2 | ጥቅምት | የፊተኛው ዝናብ | መለከቶች<br>የማስተሰረያ ቀን<br>የዳስ በዓል<br>የተቀደሰ ጉባኤ | 1<br>10<br>15-21<br>22 |
| ቡል | (ማርኬስዋን) | 1ነገ. 6፥38 | ኅዳር | እርሻ ይታረሳል | | |
| | ካሴሉ | ነህ. 1፥1<br>ዘካ. 7፥1 | ታኅሣሥ | ዘር ይዘራል | የመቅደስ መታደስ | 25 |
| | (ጤቤት) | | ጥር | ዝናብ | | |
| | ሳባጥ | ዘካ. 1፥7 | የካቲት | የለውዝ አበባ | | |
| | አዳር | ዕዝ. 6፥15 | መጋቢት | የብርቱካን ፍሬ | | |

በ8ኛው፥ በ11ኛው፥ በ14ኛው፥ በ17ኛውና በ19ኛው ዓመት ላይ ነበር። እስራኤላውያን ከግብጽ የወጡበት ወር የመጀመሪያው ወር ተብሎ ይጠራ ነበር፤ ዘጸ. 12፥2። ከባቢሎን ምርኮ በፊት ከወሮች ብዙዎቹ በቍጥር ብቻ ይታወቁ ነበር። ከምርኮ በኋላ ግን ለየወሩ ስም ተሰጠ። በሰንጠረዥ በመጽሐፍ ቅዱስ ያልተጠቀሱ ወሮች በቅንፍ ተደርገዋል። እስራኤላውያን በጨረቃ ወር ይቈጥሩ ስለነበር፥ ወሮቻቸው ከእኛ ወሮች ጋር በትክክል አይገናኙም።

**ወርቀ ዘቦ**፤ ወርቅ ያለበት በወርቅ የተዘመዘመ የክብር ልብስ፤ ሕዝ. 16፥10፤ 27፥7።

**ወርቅ**፤ የከበረና ውድ የሆነ ማዕድን፤ ዘፍ. 2፥11፤ 13፥2። ለጌጥና ለገንዘብ ይጠቅማል፤ ዘፍ. 24፥53፤ ማቴ. 10፥9። የእግዚአብሔር የማደሪያ ድንኳን ዕቃ ተሠራበት፤ ዘጸ. 25፥11-39። ሰሎሞን የሠራው ቤተ መቅደስ በብዙ ወርቅ የተለበጠ ነበር፤ 1ነገ. 6፥20-35። የክብርና የመንግሥት ሰማያት ምሳሌ ነው፤ ራእ. 21፥18። ከወርቅ የሚበልጡ ነገሮች፥ የእግዚአብሔር ሕግ (መዝ. 119፥72)፥ ጥበብ (ኢዮብ 28፥12-19)፥ እምነት (1ጴጥ. 1፥6-7)፥ የተዋጀንበት የክርስቶስ ደም (1ጴጥ. 1፥18-19) ናቸው።

**ወሰካ**፤ ከእንጨት የሚሠራ የበሽተኞች መሸከሚያ ቃሬዛ፤ ሐ.ሥ. 5፥15።

**ወስከምት**፤ በመንኩራኵር መካከል የሚገኝ፥ መንኩራኵሮችን የሚያገናኝና የሚያዞር እንዝርት፤ 1ነገ. 7፥30-33።

**ወስፈንጠር**፤ እንጨት በመትከል፥ ወይም የቆመውን እንጨት ጉብብ በማድረግ የሚሠራ የወፍ መያዣ። ወፍም ሆነ ሌላ ነገር ሲነካው ወደላይ ይፈነጠራል፤ ኢዮብ 18፥9፤ አሞጽ 3፥5።

**ወስፌ**፤ ጫፉ ሹል የሆነ የልዩ ልዩ ዕቃ መብሻ። በሙሴ ሕግ ዕብራዊ ባሪያ ከሰባት ዓመት በኋላ ነፃ ለመውጣት ባይፈልግ ጆሮው በወስፌ ተበስቶ ከጌታው ጋር እንዲኖር ተጽፏል፤ ዘጸ. 21፥6፤ ዘዳ. 15፥17።

**ወሽመጥ**፤ ወደ ባሕር የገባ ሾጣጣ መሬት (ልሳነ ምድር) ወሽመጥ ይባላል፤ እንዲሁም ወደ መሬት የገባ የባሕር ጫፍ የባሕር ወሽመጥ (ልሳነ ባሕር) ይባላል፤ ዘኍ. 34፥11።

**ወተት**፤ በከነዓን የላምም ሆነ የሌላ እንስሳ ወተት እንደ ልብ ይገኝ ነበርና ወተትና ማር የምታፈስ አገር ናት ተባለ፤ ዘጸ. 3፥8፤ ዘዳ. 32፥14፤ ኢሳ. 7፥22። ከወተት እርጎና ቅቤ ይገኛል፤ ዘፍ. 18፥8፤ መዝ. 55፥21። የወተት ብዛት የልማት መግለጫ ነው፤ ኢሳ. 60፥16፤ ኢዩ 3፥18። ሕፃን በወተት እንደሚያድግ ሁሉ አማኝም በእግዚአብሔር ቃል ያድጋል፤ 1ጴጥ. 2፥2:3። ደግሞም ወተት የሕፃናት ምግብ ነውና የመጀመሪያ የሃይማኖት ትምህርት ምሳሌ ነው፤ 1ቆሮ. 3፥2፤ ዕብ. 5፥11-14።

**ወታደር**፤ «ጦርነት»፥ «የጦር መሣሪያ»፥ «ጦር ሠራዊት» ይመ.

**ወኅኒ**፤ ወንጀለኛ የሚቀጣበት። ወኅኒ የሚገኘው ብዙ ጊዜ በጕድጓድ ወይም ከቤት በታች በጨለማ ውስጥ ነበር፤ ኢሳ. 42፥6:7፤ ኤር. 38፥6፤ ማቴ. 5፥25። መጥምቁ ዮሐንስ በወኅኒ ታሰረ፤ ማር. 6፥17። ክርስቶስ አስቀድሞ እንደነገራቸው፥ ሐዋርያት ብዙ ጊዜ በወኅኒ ተጣሉ፤ ሉቃ. 21፥12፤ ሐ.ሥ. 4፥3፤ 5፥19። ጴጥሮስ በወኅኒ ቤት በሁለት ወታደሮች መካከል በሰንሰለት ታሰረ፤ ሐ.ሥ. 12፥3-10። ጳውሎስና ሲላስ በእግር ግንድ ተጠርቀው በወኅኒ ተጣሉ (ሐ.ሥ. 16፥24)፥ በኋላም ጳውሎስ በቂሣርያ በአገረ ገዥው ግቢ፥ በሮምም በግል ቤቱ በወታደር ተጠበቀ፤ ሐ.ሥ. 23፥33-35፤ 28፥16:30። «ግዞት ቤት» ይመ.



ወንጀለኞች የሚታሰሩበት ሰንሰለት

**ወና**፤ ሰው የማይኖርበት የተፈታ ሰፈር። ሰው ብዙ ጊዜ ከኖረበት በኋላ የተተወ ቤትም ወና ይባላል፤ ኢሳ. 32፥14፤ ኤር. 3፥2:21።

**ወናፍ**፤ ብረት ቀጥቃጭ የከሰል እሳት የሚያነድበት መሣሪያ። የእግዚአብሔርን ተግሣጽ ያመለክታል፤ ኢሳ. 54፥16፤ ኤር. 6፥29።

**ወንድ**፤ በእግዚአብሔር መልክ አስቀድሞ የተፈጠረ ሰው። ከወንድ ሴት ተፈጠረች፤ ሴት ከወንድ እንደሆነች፥ እንዲሁም ወንድ ደግሞ ከሴት ነው፤ ዘፍ. 1፥27፤ 2፥21-25፤ 1ቆሮ. 11፥12። ወንድና ሴት በእግዚአብሔር መልክ ተፈጥረዋልና፤ ሁለቱም በአንድ መንገድ ይድናሉ፤ ገላ. 3፥28፤ 1ጴጥ. 3፥7። ሐዋርያው ጳውሎስ ስለ ወንዶች ኀላፊነት ልዩ ልዩ መግለጫዎችን ገልጧል፤ 1ቆሮ. 11፥7-9፤ 1ጢሞ. 2፥8-14። «ሴት»፥ «ጋብቻ»፥ «ሰው» ይመ.

**ወንድም**፤ የአባትና የእናት ልጅ፥ ከዚህም ሌላ በሥጋና በመንፈስ ወይም በሥራ፥ የፍቅርና የመረዳዳት አንድነት ያለው ሁሉ ወንድም ይባላል። ቃሉ የወንድምነትን ደረጃ እንደሚከተለው ያሳያል።

1. በአባት ወይም በእናት በኩል (2ሳሙ. 13፥4)፤ 2. በአገር (ዘጸ. 2፥11)፤ 3. በነገድ (2ሳሙ. 19፥12)፤ 4. በቤተሰብ (ዘፍ. 14፥16)፤ 5. በቃል ኪዳን (አሞጽ 1፥9)፤ 6. በቅርብ ዝምድና (ዘኍ. 20፥14)፤ 7. በወዳጅነት (2ሳሙ. 1፥26)፤ 8. ክርስቶስ በሰውነቱ (ዕብ. 2፥17)፤ 9. በሥራ (ዕዝ. 3፥2)፤ 10. በሃይማኖት (ሮም 1፥13)።

**ወንጌላዊ**፤ ወንጌልን የሚሰብክ። ክርስቲያን የእግዚአብሔርን ቃል ሲያስተምር፥ ወንጌልን ይሰብካል። ሆኖም እግዚአብሔር አንዳንድ ምእመናንን ከቤ.ክ. ወደ ውጭ ሄደው ወንጌልን በመስበክ ሰዎችን ወደ እርሱ እንዲያመጡ ይጠራል፤ እነርሱም የወንጌል ሰባክያን ወይም ወንጌላውያን ይባላሉ፤ ሐ.ሥ. 21፥8፤ ኤፌ. 4፥11፤ 2ጢሞ. 4፥5።

**ወንጌል**፤ ቃሉ ዩአንገሊዮን ከሚለው የግሪክ ቃል የመጣ ሲሆን፥ ትርጒሙም የምሥራች ቃል ማለት ነው። ወንጌል ክርስቶስ የእግዚአብሔር ልጅ እንደሆነ በሥጋ እንደተወለደ፥ ስለ ሰዎች ኃጢአትም ከሞተ በኋላ እንደተነሣ ያበሥራል፤ ሮም 1፥3:4። ሰው ይህን ሲያምንና በዚህ መሠረት ሲኖር ይድናል፤ ባያምን ግን ይፈረድበታል፤ ማር. 1፥15፤ 16፥15:16። ወንጌል በብ.ኪ. የተነገረውን፥ በእምነት የሚገኘውን የእግዚአብሔር ጽድቅ ይገልጣል፤ ሮም 1፥1:2፤ ገላ. 3፥8። ይህ ወንጌል ለሰዎች መዳን የእግዚአብሔር ኃይል ነውና ምእመናን ለሌሎች እንዲያስተላልፉት ግዴታ አለባቸው፤ ሮም 1፥16:17፤ 1ቆሮ. 9፥16።

ወንጌል ደግሞ ክርስቶስን የሚመለከት ስለሆነ፥ የክርስቶስ ታሪክ የተጻፈበት ወንጌል ተብሏል። ብዙ ሰዎች የክርስቶስን ታሪክ ለመጻፍ ቢሞክሩም በእጃችን የሚገኙ በቤ.ክ. የታወቁ የማቴዎስ፥ የማርቆስ፥ የሉቃስና የዮሐንስ ወንጌላት ናቸው። ማቴዎስና ዮሐንስ ሐዋርያት ነበሩ። ማርቆስ የእናቱ ቤት በኢየሩሳሌም ነበረና፥ ከሐዋርያት ጋር ሠራ፥ የጴጥሮስም ጓደኛ ነበረ። ሉቃስ ከሰዎች በመጠየቅ፥ ጽሑፎችንም በማንበብ የሆነውን በጥንቃቄ አረጋገጠ፤ የጳውሎስም ጓደኛ ነበረ፤ በየስማቸው ይመ.

ወንጌላውያን ኢየሱስ ያደረገውን ሁሉ ለመጻፍ አልቻሉም፤ ዮሐ. 21፥25። ነገር ግን እያንዳንዱ ወንጌላዊ በመንፈስ ቅዱስ እየተመራ ከኢየሱስ ድርጊቶችና ከትምህርቶች መርጦ ያለ ስሕተት ጻፈ፤ ዮሐ. 14፥26፤ 15፥26:27። አራቱ ወንጌላውያንም የክርስቶስን ጥምቀት፥ አምስት ሺህ ሰዎች መመገቡን፥ መያዙን፥ ስቅለቱንና ትንሣኤውን ይተርካሉ። አንዳንድ ነገሮች ከአራቱ በሦስቱ፥ ወይም በሁለቱ ብቻ ይገኛሉ። ይህንም በየሐዲጉ በተጻፈው ማመሳከሪያ ጥቅስ መመልከት ይቻላል። ብዙ ሰዎች ማቴዎስ ወንጌሉን ሲጽፍ፥ የማርቆስን ወንጌል ከተመለከተ በኋላ ያየውንና የሰማውን ጨምሮ እንደጻፈ ያምናሉ። ሌሎች ግን ማርቆስ የማቴዎስን ተመልክቶ ጻፈ ይላሉ። እንደዚሁም ሉቃስ የማርቆስን አይቶ ጻፈ የሚሉ አሉ። የማቴዎስ፥ የማርቆስና የሉቃስ ወንጌላት በብዙ አንቀጽ አንድ ናቸው፤ ነገር ግን ይህን በሐዋርያት ትምህርት አቀራረብ አንድነት ወይም የሌላውን ጽሑፍ በመመልከት ለማረጋገጥ አይቻልም። ዋናው ቁም ነገር አጻጻፋቸው ሳይሆን የክርስቶስ ታሪክ ነው።

ማቴዎስ፥ ማርቆስና ሉቃስ በብዙ አንቀጽ ቢመሳሰሉም፥ ማቴዎስ በተለይ የክርስቶስን ትምህርትና መሢሕነት፥ ማርቆስ ድርጊቱንና የፈሪሳውያንን ተቃውሞ፥ ሉቃስ ደግሞ ስለ ሴቶችና ስለ ችግረኞች ክርስቶስ የነበረውን ሰብአዊ ርኅራኄ አጒልተው ያሳያሉ። ዮሐንስ በተለይ ኢየሱስ ወደ ኢየሩሳሌም ለዓመት በዓል ሲመጣ የተናገረውንና ያደረገውን ይገልጣል። የአራቱም ወንጌላት ስለ አንድ ኢየሱስ ክርስቶስ ታሪክ ይናገራሉ። «ኢየሱስ ክርስቶስ» የሚለውን ርእስ ይመ.

**ወንዝ**፤ 1. እንደ ዐባይ ያለ የማይደርቅ የውሃ ፈሳሽ፤ ዘፍ. 2፥10-14። 2. እንደ ቂሶን ያለ በዝናም ጊዜ ብቻ የውሃ ፈሳሽ የሚገኝበት፥ በሌላ ጊዜ ግን የሚደርቅ፤ መሳ. 5፥21። የብዛት ምሳሌ ሊሆን ይችላል፤ ኢዮብ 20፥17፤ ኢሳ. 43፥2።

**ወንጭፍ**፤ የእረኛና የጥንት ወታደር የድንጋይ መወርወሪያ፤ 1ሳሙ. 17፥40፤ መሳ. 20፥16፤ 1ዜ.መ. 12፥2፤ ኤር. 10፥18። «የጦር መሣሪያ» ይመ.



በስተግራ የአሦር፥ በስተቀኝ የግብጽ ባለወንጭፎች

**ወንፊት**፤ ከሸንበቆ፥ ከፈረስ ጭራ፥ ከሣር፥ ከሽቦና ከመሳሰለው ሁሉ የሚሠራ የእህልና የሌላም ማጣሪያ። የእግዚአብሔር ተግሣጽ ምሳሌ ነው፤ ኢሳ. 30፥28፤ አሞጽ 9፥9።

**ወይራ**፤ በኢትዮጵያና በእስራኤል ዱር ውስጥ የሚገኝ ዛፍ። እንጨቱ ጥሩ የሆነ ወይራ በመ.ቅ. የበረሀ



ወይራ ተብሎ ይጠራል፤ ነህ. 8፥14:15። ከዚህ ሌላ በእስራኤልና ደቡብ አውሮፓ ቁመቱ ልከኛ፣ ፍሬው ወፍራም ቅባት የሞላው ሌላ ዓይነት ወይራ አለ። ከዚህ ወይራ የሚገኝ ዘይት ለምግብ፣ ለመድኃኒትና ለቅባት ይጠቅማል። በምሳሌነት የልማትና የብልጽግና ምልክት ነው፤ ዘዳ. 24፥20፤ መዝ. 128፥3፤ ሮም 11፥17:24።

**ወይን**፤ የወይን ቦታ፣ የወይን ጠጅ፤ ወይን ከጥንት ጀምሮ የታወቀ ተክል ነው (ዘፍ. 14፥18)፣ በእስራኤል አገር በብዛት ይገኛል፤ ዘኍ. 13፥23። የወይን ቦታ ዙሪያው ይቀጠርና ለጠባቂው ዳስ ወይም ግንብ ይሠራል፤ ኢሳ. 1፥8፤ 5፥1:2፤ ማር. 12፥1። ሐረጉ በመደገፊያ ይዘረጋል (ሕዝ. 17፥6)፣ በየዓመቱ ይገረዛል (ይከረከማል)፤ ዘሌ. 25፥3፤ ዮሐ. 15፥2። የወይን ጠጅ ለማውጣት ፍሬው በመጥመቂያው ውስጥ ይረገጣል፤ ኢሳ. 16፥10፤ አሞጽ 9፥13። እስራኤላውያን የወይን ጠጅ በአቁማዳና በሸክላ ዕቃ ያኖሩ ነበር፤ ማቴ. 9፥17፤ ዮሐ. 2፥6። የደረቀ የወይን ፍሬም (ዘቢብ) ለምግብ ይሆናል፤ 1ሳሙ. 25፥18።



የወይን ዘለላ በቅርንጫፉ ላይ

የወይን ብዛት የእግዚአብሔር በረከት ምልክት ነው (ዘፍ. 27፥28)፤ ወይን መሥዋዕት ይሆናል፤ ዘጸ. 29፥40። ሰውን ደስ ያሰኛል፤ መዝ. 104፥15፤ ምሳ. 31፥6፤ መክ. 10፥19፤ ሐ.ሥ. 2፥13። ጌታችን ወይን ጠጣ፤ ውሃንም ወደ ወይን ለወጠ፤ ለአዲስ ኪዳን ሥርዓትም ወይንን ሰጠ፤ ማቴ. 11፥19፤ 26፥27-29፤ ዮሐ. 2፥1-11። ወይን መድኃኒት ይሆናል፤ ሉቃ. 10፥34፤ 1ጢሞ. 5፥23።

ነገር ግን የወይን መጠጥ ከበዛ፣ አደገኛና የሚያስነውር ነገርን ሊያመጣ ይችላል፤ ዘፍ. 9፥20-23፤ 19፥30-38፤ ምሳ. 4፥17፤ 20፥1፤ 23፥29-35፤ 31፥4፤ ኢሳ. 5፥11፤ 28፥7። ስለዚህም ካህናት ከአገልግሎት በፊት፣ ናዝራውያንም የስእለታቸው ወራት እስኪፈጸም ድረስ ወይን እንዳይጠጡ ተከለከሉ፤ ዘሌ. 10፥9፤ ዘኍ. 6፥3:20። ማንም ሰው ወይን ለራሱ ወይም ለጓደኛው ማሰናከያ የሚሆን ከሆነ ባይጠጣ መልካም ነው (ሮም 14፥17-21)፤ በወይን ጠጅም ፈንታ በመንፈስ ቅዱስ መሞላት ይገባዋል፤ ኤፌ. 5፥18።

ወይን የእስራኤልና የቤ.ክ. ምሳሌ ነው (መዝ. 80፥8-14፤ ኢሳ. 5፥1-5፤ ሉቃ. 20፥9-18)፤ ክርስቶስ ራሱን በእውነተኛ የወይን ግንድ መስሎ ተናገረ፤ ዮሐ. 15፥1-8። ወይን መርገጥ የፍርድ ምሳሌ ነው፤ ኢሳ. 63፥3፤ ራእ. 19፥15። «ስካር»፣ «መጥመቂያ» ይመ.



የወይን መጠበቂያ ግንብ

**ወዮ**፤ ኀዘን የሚገለጥበት ጩኸት። 2ነገ. 6፥5፤ ኢሳ. 6፥5፤ ማቴ. 11፥21፤ 23፥15:16፤ 1ቆሮ. 9፥16፤ ራእ. 8፥13። ነቢያት ብዙ ጊዜ በዚህ ቃል ሕዝቡን ያስጠነቅቁ ነበር፤ ዕን. 2፥6-19።

**ወደብ**፤ የመርከብ መነሻና መድረሻ፣ በባሕር ዳርቻ የሚገኝ ቦታ፤ ዘፍ. 49፥13። ከመከራ በኋላ የሚገኝ ዕረፍትን ይገልጣል፤ መዝ. 107፥30።

**ወጀብ**፤ በነፋስ ጊዜ የሚዘንም ዝናም ወይም ውሽንፍር፤ ምሳ. 25፥23። ወጀብ የእግዚአብሔር የኃይሉ መገለጫ ነው፤ ናሆም 1፥3።

**ወገብ**፤ ወገብን ማሸንፈጥ ማለት በፍጥነት ለመሮጥ ልብስን መታጠቅ ማለት ነው፤ 1ነገ. 18፥46። ወገብን መታጠቅ በትጋት ማገልገልን ያመለክታል፤ ሉቃ. 12፥35፤ 1ጴጥ. 1፥13። ዘር ከወገብ ይከፈላል፤ ዕብ. 7፥5።

**ወግ**፤

1. ሥርዓት፣ ደንብ፣ ከሕግ የተነሣ የሚደረግ ልማድ። አይሁድ ከአባቶቻቸው ብዙ ወግ ተቀብለው ነበርና ከእግዚአብሔር ሕግ ይልቅ ወጋቸውን ይጠብቁ ነበር፤ ገላ. 1፥14። ኢየሱስ ከእግዚአብሔር ሕግ መሸሻቸውን እየገለጠ ወጋቸውን በማፍረስ ሕጉን በትክክል ይተረጉም ነበር፤ ማቴ. 15፥1-20።



እንስሳት በወጥመድ ውስጥ፤ በ650 ገደማ ከክ.በ. ተቀርጾ በነነዌ የተገኘ

በአ.ኪ. ሐዋርያት ስለ ቤ.ክ. አስተዳደር ልዩ ልዩ ትእዛዛትን ሰጡ። ይህንም ወግ እንዲጠብቁ ምእመናንን አስጠነቀቁ፤ 1ቆሮ. 11፥2፤ 2ተሰ. 2፥15፤ 3፥6።

2. በብ.ኪ. በመሥዋዕት አከፋፈል ጊዜ የካህናት ልዩ ድርሻ ወግ ተብሏል፤ ዘጸ. 29፥26-28።

**ወጥመድ፤** ወፍ ወይም አውሬ የሚያዝበት ጉድጓድ፥ ሣጥን፥ መረብ ወይም ገመድ። መ.ቅ. ብዙ ጊዜ ወጥመድን ምሳሌ ያደርጋል፤ መዝ. 64፥5፤ 91፥3፤ 124፥7፤ ሮም 11፥9፤ 1ጢሞ. 3፥7፤ 2ጢሞ. 2፥26።

**ወጨፎ፤** ነፋስ የተቀላቀለበት ዝናም። የእግዚአብሔር ፍርድ ምሳሌ ነው፤ ኢሳ. 29፥6። «ውሽንፍር» ይመ.

**ወጭት፤** ከሸክላ፥ ከነሐስ፥ ከሌላም የሚሠራ ትልቅና ሰፊ የወጥ ማቅረቢያ፤ ማቴ. 23፥25-26፤ 26፥23።

**ወፍጮ፤** ሰዎች በጥንት ዘመን ሁለት ተስተካክለው በተሠሩት ድንጋዮች መካከል እህል ይፈጩ ነበር። ክብ በሆነው በላይኛው መጅ ሴቶች እያዞሩ ይፈጩበታል። ዱቄቱም ከድንጋዮች መካከል እየወጣ ይደቃል። ወፍጮው ትልቅ ከሆነ፥ በብዙ ሰዎች ወይም በከብት ኃይል ድንጋዩን በማዞር ይፈጩ ነበር፤ ዘጸ. 11፥5፤ መሳ. 16፥21፤ ማቴ. 24፥41።

**ወፎች፤** እግዚአብሔር ወፎችን በአምስተኛው ቀን ፈጠረ፤ ዘፍ. 1፥20-23። በሚከተለው ዝርዝር በዘሌ. 11፥13-19 የተጠቀሱት የማይበሉት ተጨምረው ተገልጠዋል። በልዩ ልዩ ጥቅስ የወፎች ስም ትክክለኛ ትርጉም ባይታወቅም እንኳ የሚከተሉት በአማርኛ የተጠቀሱት አዕዋፍ ናቸው ፡-

ርግብ (ዘፍ. 8፥8)፥ ሰጐን (ኢዮብ 39፥13)፥ ሳቢሳ (ዘሌ. 11፥19)፥ ሽመላ (ኤር. 8፥7)፥ ቍራ (ዘፍ. 8፥7)፥ ቆቅ (ኤር. 17፥11)፥ ቍርዬ (መ.መ. 2፥12)፥ በቋል (ዘሌ. 11፥16)፥ ንስር (ምሳ. 23፥5)፥ አሞራ (ኢሳ. 34፥15)፥ እርኩም (ዘሌ. 11፥17)፥ ዋሊያ (ኢሳ. 34፥15)፥ ዋኖስ (ዘፍ. 15፥9)፥ ዓሣ አውጭ (ዘሌ. 11፥14)፥ ዝንጉርጉር አሞራ (ኤር. 12፥9)፥ ዝንጉርጉር ወፍ ወይም ጣዎስ (1ነገ. 10፥22)፥ ዝዬ (ዘሌ. 11፥16)፥ የውሃ ዶሮ (ዘሌ. 11፥18)፥ ይብራ (ዘሌ. 11፥19)፥ ዶሮ (ማቴ. 23፥37)፥ ድርጭት (ዘጸ. 16፥13)፥ ድንቢጥ (ማቴ. 10፥29)፥ ጃን (ኢሳ. 34፥14)፥ ጅንጁላቴ ወፍ (ዘሌ. 11፥19)፥ ገዴ (ዘሌ. 11፥14)፥ ጋጋኖ (ዘሌ. 11፥18)፥ ጉጉት (ኢሳ. 34፥11)፥ ጠላቋ (ዘሌ. 11፥16)፥ ጥንብ አንሣ አሞራ (ዘሌ. 11፥19)፥ ጨረባ (ኢሳ. 38፥14)፥ ጭላት (ዘሌ. 11፥14)፥ ጭልፊት (ኢዮብ 39፥26)።

**ዋሄብ፤** የቦታ ስም (ዘኁ. 21፥14)፤ ዛሬ የት እንደነበረ ተረስቷል የግእዙ ትርጉሜ ዛሕም ይለዋል።

**ዋላ (ዋልያ)፤** ከፍየል ወገን የሆነ፥ ረጅም ቀንድ ያለው የዱርና የተራራ እንስሳ፤ ኢዮብ 39፥1፤ መዝ. 42፥1።



**ዋልያ**፤ (ዋኒያ፣ ዋኒ)፤ እንደ ዋኖስ ያለ ወፍ፤ ሉቃ. 2፥24። ነገር ግን በኢሳ. 34፥15 ዋሊያ ተብሎ የተጠቀሰው ጉጉት መባል ነበረበት፤ በኤር. 8፥7 ዋሊያ የሚለው ጥርኙ ተብሎ ቢተረጎም ይሻላል። «ወፎች» ይመ.

**ዋርሳ**፤ ዋርሳዬት፤ የወንድሙን ሚስት የሚወርስ ወይም የባልዋን ወንድም የምትወርስ። በእስራኤል ኅብረተ ሰብ መካከል ሰው ሳይወልድ ቢሞት፣ የሟቹ ስም እንዳይጠፋ ወንድሙ ወይም የቅርብ ዘመዱ የሟቹን ሚስት ወርሶ (አግብቶ) ዘር ይተካ ነበር፤ ዘዳ. 25፥4-10፤ ሩት 3፥12-4፥12።

**ዋስ**፤ ተያዥ። በእስራኤል ዘንድ ሰው ዋስ እንዲሆን ይፈቀድ ነበር። ግን እየቆየ በዋሱ ላይ ውድቀት የሚያመጣ መሆኑ ተገልጧል፤ ምሳ. 6፥1-5፤ 11፥15፤ 17፥18፤ 20፥16።

**ዋሽንት**፤ ባለ አንጓ የሆነ ከሸንበቆ ወይም ከብረትና ከቆርቆር የሚሠራ የዜማ ዕቃ፤ ዳን. 3፥5:10።

**ዋኖስ**፤ ከርግብ የምታንስ፣ እህልን የምትበላ ዋኖስ ወይም ዋሊያ የምትባል ወፍ። የድሀ መሥዋዕት ነበረች፤ ዘሌ. 14፥21-22። «ወፎች» ይመ.

**ዋጋ**፤ አንድ ነገር የሚነገድበትን (ኢሳ. 55፥1፤ ማቴ. 13፥46፤ 27፥9) ወይም የሚገኝበትን (1ቆሮ. 6፥20፤ 7፥23)፣ የድርጊትን ትክክለኛ ውጤት (ማቴ. 5፥46፤ ሮም 6፥23)፣ በሰው ዓይን ክብርን (ማቴ. 6፥1:2:16)፣ ከእግዚአብሔር በረከትን (ዘፍ. 15፥1፤ ምሳ. 25፥22፤ ማቴ. 5፥12፤ 10፥41-42፤ ዕብ. 11፥6) ሊያመለክት ይችላል። «ደመወዝ» ይመ.

**ዋጀ**፤ ዋጋ በመክፈል ወይም ራስን በመተካት የተወሰደን ማስመለስ፣ ገና ሊወሰድ የተዘጋጀ ማናቸውንም ነገር ማስቀረት። የእስራኤል ሕዝብ በኩር ልጆቻቸውን የከብት በኩራታቸውንም ሊዋጁ ተፈቅዶላቸው ነበር፤ ዘጸ. 13፥11-16። ኢየሱስ በሞቱ እኛን ዋጀን፤ ገላ. 3፥13፤ 4፥4-5፤ 1ጴጥ. 1፥18:19፤ ራእ. 5፥9። «ቤዛ» ይመ.

**ዋግ**፤ የእህል በሽታ፤ ዘዳ. 28፥22፤ 2ዜ.መ. 6፥28፤ አሞጽ 4፥9።

**ዋጠ**፤ ወደ ሆድ አስገባ፣ አስቀረ፤ ዘፍ. 41፥4:7፤ ዘጸ. 7፥12፤ 15፥12፤ ኢሳ. 25፥8፤ ዮናስ 2፥1፤ 1ቆሮ. 15፥54፤ 1ጴጥ. 5፥8።

**ውሃ**፤ ለሕያው ፍጥረት ሁሉ ከሚያስፈልጉ ነገሮች አንደኛው ውሃ ነው፤ ውሃ በጥንተ ፍጥረት በምድር ላይ ተገኘ፤ ዘፍ. 1፥2:6። በእስራኤል አገር ውሃ ውድ ነበረ፤ ወንዞች ትልልቆች አልነበሩምና በድርቅ ዘመን ውሃ አይገኝባቸውም ነበር፤ ኤር. 14፥3-6። እስራኤላውያን በግብጽ በእግር የሚዞር የውሃ ማውጫ መርተው ከወንዝ ውሃውን እያወጡ መሬቱን ያጠጡ ነበር። ነገር ግን በአገራቸው ዝናም ሲዘንም ውሃን ማጠራቀም ለመዱ፤ ዘዳ. 11፥10:11፤ መክ. 2፥5:6። «ጉድጓድ» ይመ.

ውሃ የልብ ከኃጢአት የመንጻት ምሳሌ ነው፤ ሕዝ. 16፥4:9፤ 36፥25፤ ዮሐ. 3፥5። ደግሞም የእግዚአብሔርን በረከት (መዝ. 23:2፤ ኢሳ. 35፥6:7፤ ሕዝ. 47፥1-12፤ ዮሐ. 4፥14፤ 7፥38፤ ራእ. 22፥1)፣ ፍርድንና አደጋን ሊያመለክት ይችላል፤ መዝ. 18፥16፤ 32፥6፤ 69፥1።

የውሃ ምረት (መራራ ውሃ)፤ 1. በአንዳንድ ቦታ ከመሬቱ ማዕድናማነት የተነሣ ውሃው ይመራል፤ ይጎመዝዛል። የማራ ውሃ መራራ ነበረ፤ ሙሴ እግዚአብሔር ያሳየውን እንጨት ሲጥልበት ግን ውሃው ጣፈጠ፤ ዘጸ. 15፥22-26። የኢያሪኮም ውሃ መራራ ነበረ። ነገር ግን ኤልሳዕ በምንጩ ላይ ጨው በጨመረበት ጊዜ ውሃው ተፈወሰ (2ነገ. 2፥19-22)። 2. የእርግማን ውሃ። በብ.ኪ. ካህኑ በሸክላ ዕቃ ውስጥ የከርቤና የዕጣን ትቢያ የተጨመረበት ውሃ ያስቀምጣል፤ ባል ሚስቱን በሴሰኝነት ሲጠረጥራት፣ ካህኑ ከዚህ መራራ ውሃ ያጠጣት ነበር፤ ዘኍ. 5፥12-31።

**ውላጅ**፤ በቤት ውስጥ ከሚኖሩት ወንድ ወይም ሴት ባሮች የሚወለድ ልጅ፤ ኤር. 2፥14።

## ውላጤ ራእይ (የመልክ መለወጥ)

ኢየሱስ ጴጥሮስን፣ ያዕቆብንና ዮሐንስን አስከትሎ ወደ አንድ ረጅም ተራራ ወጣ። በዚያም መልኩ ተለወጠና በክብር ታያቸው፤ ማቴ. 17፥1-8፤ 2ጴጥ. 1፥17:18። ተራራው ደብረ ታቦር ነው ይባላል። መ.ቅ. ግን የትኛው ተራራ እንደሆነ አይገልጥም። ካ. 5ለ።

**ውርጭ**፤ ደቃቅ የመስታወት ስባሪ መስሎ የሚታይ፤ ዘጸ. 16፥14። በመከር ወራት እንደ ጠል ወይም እንደ ጤዛ ሆኖ ሲወርድ ያስደስታል (ምሳ. 25፥13)፣ በፍርድ ቀን ስለሚሆነው ድርጊት ምሳሌ ሆኖ ተጠቅሷል፤ ዘካ. 14፥6።

**ውሻ**፤ የቤት ጠባቂ እንስሳ፤ ዘጸ. 11፥7፤ ኢሳ. 56፥10። በቤት ውስጥ ይኖራል፤ ማቴ. 15፥26:27። እንደ ርኩስ ስለተቈጠረ በተቀደሰ ቦታና ጉዳይ እድል ፈንታ የለውም፤ ማቴ. 7፥6፤ ራእ. 22፥15። የንቀት (2ሳሙ. 16፥9)፣ ወደ ቀደመ ጠባይ የሚመለስ የጊዜያዊ አማኝ (2ጴጥ. 2፥22)፣ የብ.ኪ.ን ሰላም የሚያውክ ምሳሌ ነው፤ ፊል. 3፥2። የወንድ ጋለሞታ ውሻ ይባላል፤ ዘዳ. 23፥17:18።

**ውሽንፍር**፤ የበረዶ፣ የዝናምና የነፋስ ቅልቅል። ዝናም ከበረዶ ጋር በሚዘንምበት ጊዜ፣ ተጨማሪ ነፋስ ሲነፍስ ውሽንፍር ወይም ተግብ ይባላል፤ ኢዮብ 36፥33፤ 37፥6።

**ውዳሴ**፤ ለእግዚአብሔር ክብር የሚደረግ ምስጋና፣ ውደሳ፤ ራእ. 4፥9። «አምልኮ» ይመ.

**ውድቀት**፤ የሰው ውድቀት በዘፍ. 3 ይተረካል። አስቀድሞ ግን ሰይጣንና ሌሎች መላእክት ወደቁ፤ 2ጴጥ. 2፥4፤ ይሁዳ 6። አዳም በእግዚአብሔር መልክ ተፈጠረ። ሲፈጠር መልካም ነበረና ኃጢአት አልነበረበትም፤ ዘፍ. 1፥26:31። ግን

በራሱ ፈቃድ የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ተላለፈ። አዳም ይህን በማድረጉ ሰዎች ሁሉ ኃጢአተኞች ሆኑ፤ ሞትም ደረሰባቸው። ክርስቶስ ኋለኛው አዳም ሆኖ በእርሱ የሚገኙትን ሰዎች ከኃጢአትና ከሞት አዳናቸው፤ ሮም 5፥12-19፤ 1ቆሮ. 15፥21:22:45-49። «ኃጢአት» ይመ.

**ውግረት**፤ ሰውን ለመግደል ድንጋይ በሰው ላይ መጣል። በሙሴ ሕግ የሞት ፍርድ በውግረት ይፈጸም ነበር፤ ዘሌ. 20፥2፤ ዮሐ. 8፥7፤ ሐ.ሥ. 7፥59። «ቅጣት» ይመ.

**ዎጆ**፤ (ወጆ)፤ ዋጋ። በብ.ኪ. ሰው ከብትን ወይም ባሪያን ቢገዛ፥ የተገዛውም የማይጠቅም ቢሆን በዎጆ ይመልሳል። ይህም ዋጋ ተቀብሎ ነፃ ያወጣዋል ማለት ነው፤ ዘጸ. 21፥8። «ዋጋ» ይመ.

**ዐምድ**፤ አዕማድ፤ 1. የታላላቅ ቤቶች ጣራ በአዕማድ ላይ ይሠራል፤ ዐምድ ከእንጨት፥ ከድንጋይ ወይም ከጡብ ሊሠራ ይችላል። በዐምዱና በጣራው መጋጠሚያ ላይ ልዩ ልዩ ጌጥ ይደረጋል፤ 1ነገ. 7፥11-12። ዐምድ ለድጋፍ ብቻ ሳይሆን፥ ለጌጥም ሊቆም ይችላል። በዚህ ዓይነት በሰሎሞን ቤተ መቅደስ በስተውጭ በኩል ያቆምና በለዝ ተብለው የተሰየሙ ሁለት ታላላቅ አዕማድ ቆመው ነበር፤ 1ነገ. 7፥15-22። መጠናቸውንም ኤር. 52፥21-23 ይገልጣል። 2. እስራኤል በደመናና በእሳት ዐምድ ተመሩ፤ ዘጸ. 13፥21። 3. አዕማድ የሰማይን (ኢዮብ 26፥11)፥ የመልአክን እግሮች (ራእ. 10፥1)፥ የቤተ ክርስቲያንን (1ጢሞ. 3፥15)፥ የመሪዎቿንም (ገላ. 2፥9) ሁኔታ ያብራራል።


የግሪክ ሕንፃ ዐምድ

## ዐሠርቱ (አሠርቱ) ትእዛዛት፤

እግዚአብሔር በሙሴ አማካይነት በደብረ ሲና ለእስራኤል የሰጣቸው የኪዳን ትእዛዛት፤ ዘጸ. 19፥5-20፥17። ትእዛዛቱ በሁለት ጽላት በእግዚአብሔር ጣት ተጻፉ፤ ዘጸ. 31፥18። ጽላቱም በታቦቱ ውስጥ ተቀመጡ፤ 1ነገ. 8፥9። ከአርባ ዓመታት በኋላ ወደ አገራቸው ሊገቡ ሲደርሱ ሙሴ ትእዛዛቱን በድጋሚ አስታወሳቸው። ሆኖም የእስራኤል ሕዝብ ሁኔታ አዲስ ስለሆነ ሰንበትን የማክበር ምክንያት ተለወጠ፤ የባልንጀራንም እርሻ ደግሞ እንዳይመኙ ታዘዙ፤ ዘዳ. 5፥6-21።

በዘጸ. 20፥2 መሠረት ዐሠርቱ ትእዛዛት የተሰጡት ደኅንነትን ተቀብሎ በቃል ኪዳን ውስጥ ለሚገኘው የእስራኤል ሕዝብ ነው። የተሰጡበትም ምክንያት ደኅንነት ባለው ሕይወት እግዚአብሔርን እንዴት መከተል እንዳለባቸው የእግዚአብሔርን ፈቃድ ለቃል ኪዳኑ ሕዝብ ለማስረዳት ነው።

በአ.ኪ. ዘመንም እነዚህ ትእዛዛት አልተሻሩም፤ ምክንያቱም የእግዚአብሔርንና የሕዝቡን ግንኙነት በማናቸውም ዘመን በቋሚነት ያስረዳሉ። በእነዚህ ትእዛዛት ውስጥ የሚታየው የእግዚአብሔር መሠረታዊ ፈቃድ «ታላቂቱና ፊተኛይቱ ... ሁለተኛይቱም» በተባሉት ትእዛዛት ተጠቃለሉ ይገኛል፤ ማቴ. 22፥36-40፤ ሮም 13፥8-10። ትእዛዛቱ በቃልም ሆነ በመንፈስ በአ.ኪ. ይገኛሉ፤ የአራተኛው ትእዛዝ አፈጻጸም ግን ፊደሉን ሳይሆን መንፈሱን ተከትሎ ነው። በብ.ኪ. ዘመን እንደታየው ሁሉ፥ በአ.ኪ.ም የእግዚአብሔርን ትእዛዛት መጠበቅ አለብን፤ ዮሐ. 15፥14። አ.ኪ. እነዚህን ትእዛዛት ያጸናል፤ ማቴ. 5፥21-30። ክርስቶስ ሕግን ፈጸመልን። አሁን እነዚህ ትእዛዛት ሕይወታችንን ለመምራት የሚያገለግሉ ናቸው፤ ገላ. 4፥4-5። «ብሉይ ኪዳን» ይመ.

**ዐሥራት**፤ አንድ ዐሥረኛ ማለት ነው። ከቀድሞ ዘመን ጀምሮ ከማንኛውም ገቢ ዐሥረኛው እጅ ለሃይማኖት መሪዎች ወይም ለመንግሥት ይሰጥ ነበር። ነገር ግን እንዴት እንደተጀመረ አይታወቅም። ከሙሴ ዘመን በፊትና እንዲሁም ከባቢሎን እስከ ሮም ድረስ ይሠራበት ነበር። አብርሃም ለመልከ ጼዴቅ ዐሥራትን ሰጠው፤ ዘፍ. 14፥20። ያዕቆብም ለእግዚአብሔር ዐሥራት ለመክፈል ተሳለ፤ ዘፍ. 28፥22። ሌዋውያን ካህናት እንዲጠቀሙበት (ዘኁ. 18፥21-32)፥ ምድር ከምታፈራውና ከከብትም ወገን ዐሥራት እንዲሰጥ ታዘዘ፤ ዘሌ. 27፥30-33።

የሚከፈልበት ጊዜ ተወሰነ፤ ዘዳ. 12፥5-18፤ 14፥22-29። ዐሥራትንም ሲከፍሉ እግዚአብሔር ሕዝቡን ይባርካል፤ ዘዳ. 26፥13-15፤ ሚል. 3፥10። ፈሪሳውያን ከቅመማ ቅመም ሳይቀር ዐሥራት ይከፍሉ ነበር፤ ማቴ. 23፥23። ሐዋርያት ስለ ዐሥራት አልጻፉም፤ ሆኖም እንደ እግዚአብሔር በረከት መጠን በልግስና በውዴታ ዐሥራት መስጠት ይገባል፤ 1ቆር. 16፥1-4፤ 2ቆር. 9፥6-12።

**ዐሥር ከተማ፤** ከዮርዳኖስ ወንዝ በስተምሥራቅ ከክ.በ. ጥቂት ዓመት ቀደም ብሎ በግሪኮች የተቈረቈሩ ዐሥር ከተሞች የነበሩባት አገር። ሕዝቡም የራሳቸው ገንዘብ፥ ጦር ሠራዊትና ሥርዓት ነበራቸው። ከዐሥር ከተማ ኢየሱስን የተከተሉት ብዙዎች ነበሩ፤ ማቴ. 4፥24:25፤ ማር. 5፥1-20፤ 7፥31-37። ዛሬ በዮርዳኖስ ውስጥ ትገኛለች። ካ. 5ረ።

**ዐረብ፤** የዐረብ አገር፥ ነገድ ወይም ቋንቋ። የዐረብ ቋንቋ (ዐረብኛ) በአማርኛ መ.ቅ. ውስጥ ተጠቅሶ አይገኝም። በግእዝ አዲስ ኪዳን አንዳንድ ረቂቆች ግን በዮሐንስ ራእይ 9፥11 በዕብራይስጥ አብዶን የተባለው የጥልቅ መልአክ በዐረብ ሰናሴር ይባላል ይላል።

**ዐረብ፤** ከእስራኤል አገርና ከሶርያ በስተደቡብ ከኤርትራ ባሕር በስተምሥራቅ ያለው ምድረ በዳ። በዐረባውያን መካከል እንደ እስማኤላውያንና እንደ ምድያማውያን ያሉ ልዩ ልዩ ነገዶች ይገኛሉ፤ 1ነገ. 10፥14፤ ኤር. 25፥24፤ ሕዝ. 27፥21፤ ገላ. 1፥17።

**ዐወጀ፤** አወጀ፤ አዲስ ነገርን በሥልጣን አሳወቀ፤ ዘጸ. 33፥19፤ ዕዝ. 8፥21፤ ኢዩ. 2፥15፤ ዮናስ 3፥5-7።

**ዐይን፤** በምሳሌነት ሲገለጥ የአሳብ መግቢያን ያሳያል፤ ማቴ. 6፥23፤ ኤፌ. 1፥18። ደግሞም የሰውን ጠባይና ስሜት ይገልጣል፤ ዘዳ. 7፥16፤ ኢሳ. 5፥15፤ ሕዝ. 24፥16። ያለፈውንና የሚመጣውን ነገር ሁሉ ማስተዋልን ያመለክታል፤ ሕዝ. 1፥18።

**ዐግ፤** ሙሴ ያሸነፈው አሞራዊው የባሳን ንጉሥ፤ ዘኍ. 21፥33-35። አገሩ ሰፊ ነበረ፤ ዘዳ. 3፥4:5። ለምናሴ ነገድ እኩሌታ ተሰጠ፤ ዘዳ. 3፥13። ዐግም ከራፋይም ወገን የሆነ ቁመታም ሰው ነበረ፤ ዘዳ. 3፥11። በእርሱ ላይ የተገኘው ድል የማይረሳ ታላቅ ድል ነበረ፤ ኢያሱ 9፥10፤ ነህ. 9፥22፤ መዝ. 135፥11፤ 136፥20።

**ዐጸድ፤** «የአትክልት ቦታ»፥ «የማምለኪያ ቦታ» በሚል ስያሜ አስታሮት ለተባለች አምላክ የተሠራው ምስል የተተከለበት ቦታ። ይህም አምልኮት በእስራኤል ዘንድ የተወገዘ አምልኮት ነበር፤ 1ነገ. 15፥13፤ 18፥19፤ ዘዳ. 12፥3፤ 16፥21።

**ዑር፤** በከለዳውያን አገር ተመሥርቶ አብርሃም ይኖርበት የነበረ ከተማ፤ ዘፍ. 11፥28፤ 15፥7። ካ. 1ረ።

**ዓለም፤** ዓለም ያልነበረበት ጊዜ ነበረ። በኋላ ግን እግዚአብሔር አስገኘው፤ ዘፍ. 1፥1፤ ዕብ. 11፥3። ቃሉ ጠቅላላ ፍጥረትን (ዮሐ. 1፥10)፥ ጠቅላላ የዓለምን ሕዝብ (ዮሐ. 16፥21)፥ አይሁድንና አሕዛብን (ዮሐ. 4፥42)፥ ክርስቶስን የማይቀበሉትን ሁሉ (ዮሐ. 17፥9)፥ ወይም እግዚአብሔር የማይከበርበትን ኅብረተ ሰብ (ዮሐ. 3፥19) ሊያመለክት ይችላል።

የዓለም ሰው ኃጢአትን ይወዳል (ዮሐ. 3፥19)፥ በሰይጣን እጅ ነው (ዮሐ. 14፥30)፥ ክርስቶስንና ተከታዮቹን ይጠላል (ዮሐ. 15፥18)። ክርስቶስ ግን የዚህን ዓለም ገዥ በመስቀሉ አሸንፏል፤ 1ዮሐ. 2፥2። ምእመናን ከዓለም መንፈስ የተለየውን



የዑር ቤተ ጣዖት

የእግዚአብሔርን መንፈስ ተቀብለዋል (1ቆሮ. 2፥12)፥ ዳግመኛ ስለተወለዱ በእምነታቸው ዓለምን ያሸንፋሉ፤ 1ዮሐ. 5፥4። ዓለምን መውደድ እግዚአብሔርን መጥላት መሆኑን ያውቃሉ (ያዕ. 4፥4)፥ በዓለም አስተሳሰብ መሠረት አይሄዱም፤ ሮም 12፥2፤ 1ዮሐ. 2፥15-17። ኢየሱስ ለተቀበሉትና ሊቀበሉ ላሉት እንጂ ለዓለም አልጸለየም፤ ራሱንም አልገለጠም፤ ዮሐ. 14፥22፤ 17፥9። ተከታዮቹ ወንጌልን በዓለም ሁሉ እንዲሰብኩ ተልከዋል (ማር. 16፥15)፥ የዚህ ዓለም ብርሃን ናቸው፤ ማቴ. 5፥14። በትንሣኤ ጊዜ ዓለም ከከንቱነቱ ይድናል፤ ሮም 8፥21። እግዚአብሔር ሁሉ በሁሉ ይሆናል፤ 1ቆሮ. 15፥28።

**ዓለት**፤ በመሬት ውስጥ የተነጠፈ ትልቅ ድንጋይ፤ መሳ. 20፥45-47። ከስፍራው አይነቀልም (ኢዮብ 18፥4)፥ ስለዚህ ዓለት የማይለወጥ የእግዚአብሔር ምሳሌ ነው፤ 2ሳሙ. 22፥2። ሙሴ ከዓለት ውሃ አወጣ፤ ዘጸ. 17፥6። ክርስቶስ ለሚያምኑበት መንፈሳዊ መጠጥ የሚገኝበትና መንፈሳዊ መሠረት የሚቆምበት (1ቆሮ. 10፥4)፥ ለማያምኑበት ግን የማሰናከያ ዓለት ተብሏል፤ ኢሳ. 8፥14፤ 1ጴጥ. 2፥8። ጴጥሮስ «አንተ ክርስቶስ ነህ» ካለ በኋላ ኢየሱስ «አንተ ጴጥሮስ ነህ፤ በዚችም ዓለት ላይ ቤተ ክርስቲያኔን እሠራለሁ» አለው። አንዳንድ ሊቃውንት «ዓለት» ክርስቶስን፥ ሌሎች ጴጥሮስ የተናገረውን ቃል፥ የተቀሩት ደግሞ ጴጥሮስን ያመለክታል ይላሉ፤ ማቴ. 16፥16-18።

**ዓላማ**(አላማ)፤ ሰዎች ለዘመቻ፥ ለጦርነት፥ ለንግድ፥ ለሌላም የሚይዙት ወይም የሚያቆሙት ምልክት ነው፤ ዘኍ. 2፥2 መ.መ. 6፥4፤ ሐ.ሥ. 28፥11።



የግብጻውያንና የአሦራውያን የጦር ሠራዊት ሰንደቅ ዓላማዎች

**ዓልሙን**፤ ውድ የሆነ ጣፋጭ ሽታ ያለው እንጨት፤ ምሳ. 7፥17።

**ዓመት**፤ በእስራኤል የዓመት አቆጣጠር እስራኤላውያን ከግብጽ የወጡበት የኒሳን ወር የመጀመሪያ ሆኖ ይቈጠራል፤ ዘጸ. 12፥2። ሆኖም ሕዝቡ በግብርና ስለሚኖሩ አጨዳ ሲጨርሱ የዓመት መለወጫ በዓልን ያከብሩ ነበር፤ ዘጸ. 23፥16፤ 34፥22። ብዙ ጊዜ በወሩ ሳይሆን በግብርና ሥራ ጊዜው ይገለጣል፤ ዘኍ. 13፥20፤ ሩት 1፥22። በጥንት ዘመን እንደ ከተማ መቈርቈር፥ እንደ ምድር መናወጥ ከመሳሰሉ ከታወቁ ሁኔታዎች በመነሣት ዓመታት ይቈጠሩ ነበር፤ አሞጽ 1፥1። በዚህ ምክንያት በየጊዜው የተፈጸሙትን ድርጊቶች ከክርስቶስ ልደት ወዲህ ካለው አቆጣጠር ጋር ማዛመድ ያዳግታል። ከክርስቶስ ልደት ጀምሮ የተፈጸሙትን ነገሮች በዓመት ለመወሰን ለመጀመሪያ ጊዜ የሞከረ በስድስተኛው መቶ ክፍለ ዘመን የነበረ ዲዮናስዮስ ኤክስጉአስ የተባለ መነኩሴ ነው። ሌላውም በ13ኛው መቶ ክፍለ ዘመን የነበረ አቡሻክር እብን አራሂብ (ወልደ መነኮስ) ነው። ከዚያም ወዲህ ብዙ ሰዎች የመንግሥታትን ታሪኮች እየመረመሩ ዘመናትን መቍጠር ሞክረዋል። ይሁን እንጂ በቂ የጥናት መሠረትና ማስረጃ ስላልነበራቸው፥ ዘመኑን በትክክል አልገመቱም። ስለዚህም በሊቃውንት መካከል ብዙ መለያየት ተፈጠረ። ለምሳሌ የዚህ መጽሐፍ ረቂቅ እንደ ኢትዮጵያ አቆጣጠር በ1968 ዓ.ም.፥ እንደ አውሮፓ አቆጣጠር ደግሞ በ1975 ዓ.ም. ተጀመረ። የአሁኑ ሊቃውንት ግን ብዙ የጥንት ረቂቆችን በመመልከት ሕፃናትን የገደለው ሄሮድስ ከ1979 ዓመታት በፊት እንደሞተ ሊወስኑ ችለዋልና ክርስቶስ ከተወለደ ወዲህ 1982 ዓመታት ገደማ እንደሚሆን ይገምታሉ። ሆኖም ሌላው አቆጣጠር ተለምዷልና ይህን መጽሐፍ በእንግሊዝኛ ከተጻፉት ሌሎች መጻሕፍት ጋር ለማነጻጸር እንዲቻል በአውሮፓ አቆጣጠር ተጠቅመናል። በመ.ቅ. ከሚገኙት ታሪኮች አንዳንዶቹ በባቢሎን ወይም በሮም መንግሥታት የሸክላ ቅርጾችና ረቂቆች ተገኝተዋል፥ በእኛ አቆጣጠር በመደመርም ሊቃውንት ሊወስኑአቸው ይችላሉ። ለምሳሌ ናቡከደነፆር ኢየሩሳሌምን በ587 ከክ.ል. እንደያዘ ተረጋግጧል (2ነገ. 24፥10-17)፥ ከዚህም የተነሣ ሌሎች ብዙዎች ድርጊቶች የተፈጸሙባቸውን ዓመታት ልናውቅ እንችላለን። «የብሉይ ኪዳን ስፍረ ዘመን»፥ «የአዲስ ኪዳን ስፍረ ዘመን» ይመ.

**ዓመፃ**፤ ዐመጽ፤ በደል፤ መዝ. 7፥16። ቃሉ ክዳትን፥ ሽንገላንና ሽፍትነትን ያመለክታል። ሰው በዓመፅ ከእግዚአብሔር ከተለየ በኋላ በንስሓ መመለስን ሲጠላ ዓመፀኛ ይባላል፤ ይህም ትዕቢተኛ ማለት ነው፤ መዝ. 45፥7፤ 51፥5፤ 2ተሰ. 2፥3:7-12።

**የዓመፅ ሰው**፤ «ተቃዋሚ» ይመ.

**ዓሚ**፤ ትርጕሙ «ሕዝቤ» ማለት ነው፤ ሆሴዕ 2፥1-3። «ሎዓሚ» ይመ.

**ዓሣ**፤ «እንስሳት» ይመ.

**ዓሣ አውጭ**፤ ዓሣን ከውሃ አውጥቶ የሚበላ፥ እቶ ረዥም የሆነ የባሕር አሞራ፤ ዘሌ. 11፥14። «ወፎች» ይመ.

**ዓሣ አጥማጅ**፤ ከጥንት ጀምሮ ሰዎች በግብጽ ወንዝ (ዘኍ. 11፥5)፥ በታላቁ ባሕር (ነህ. 13፥16)፥ በገሊላ ባሕር ዓሣ ያጠምዱ ነበር። መጣሪያቸውም ጦር (ኢዮብ 40፥31)፥ መቃጥን

(ኢሳ. 19፥8፤ ማቴ. 17፥27)፥ መረብ (ዮሐ. 21፥6:8) ነበረ። በገሊላ ባሕር ታንኳዎችን በመቅዘፊያና በመጋረጃ እያስኬዱ መረባቸውን ይጥሉ ነበር፤ ብዙ ጊዜም በሌሊት ያጠምዱ እንደነበር ታውቋል። ዓሦችን በመረብ ከያዙ በኋላ ወደ ታንኳ ይገለብጡአቸዋል ወይም ወደ ባሕሩ ዳር ጐትተው ያወጡአቸዋል። ከዚያም በኋላ መልካሙን ከመጥፎው ይለያሉ፤ ሉቃ. 5፥2-7፤ ዮሐ. 21፥1-11፤ ማቴ. 13፥48። ከኢየሱስ ደቀ መዛሙርት ጴጥሮስና እንድርያስ፥ ያዕቆብና ዮሐንስ ዓሣ አጥማጆች ነበሩ (ማር. 1፥16-20)፤ ቶማስና ናትናኤል፥ ሌሎችም ዓሣ ሲያጠምዱ ኖረዋል፤ ዮሐ. 21፥2:3። ዓሣን ማጥመድ የፍርድ (ኤር. 16፥16፤ ሕዝ. 32፥3፤ ማቴ. 13፥47-50)፥ የወንጌል ሥራም ምሳሌ ነው፤ ማቴ. 4፥19።



**ዓረባ፤** ከአርሞንዔም ጀምሮ እስከ ዔጽዮን ጋብር ድረስ ያለው የገሊላ ባሕር፥ የዮርዳኖስ ወንዝና የጨው ባሕር የሚገናኙበት ጐድጓዳ መሬት። ብዙ ጊዜ ቃሉ በኢያሪኮ አጠገብ ያለውን መሬት ያመለክታል፤ ዘዳ. 1፥1:7፤ 11፥30፤ ኢያሱ 3፥16፤ 1ሳሙ. 23፥24፤ ኤር. 39፥4።

**የዓረባ ባሕር፤** «የጨው ባሕር» ይመ.

**ዓባይ፤** የግብጽና የአፍሪቃ ዋና ወንዝ። ርዝመቱ 6480 ኪ.ሜ. ነው። ጥቁር ዓባይ ከጐጃም ተነሥቶ በኬንያ ሐይቅ ከሚነሣው ከነጭ ዓባይ ጋር ተገናኝቶ በሱዳንና በግብጽ እየዞረ ወደ ሜዲትራኒያን ባሕር ይገባል። በግብጽ ዓባይ የሚደርስበት ሁሉ ለምለም ነው፤ ሌላው መሬት ግን በረሃ ነው፤ ኢሳ. 19፥7:8፤ 23፥3። ብዙ ጊዜ የግብጽ ወንዝ ተብሎ ይጠራል። ሙሴ ሕፃን ሳለ በሣጥን ተጨምሮ በዓባይ ወንዝ ተጣለ፤ ዘጸ. 2። እግዚአብሔር ግብጻውያንን በቀሠፈ ጊዜ የዓባይ ውሃ በግብጽ ላይ ብቻ ወደ ደም ተለውጦ ነበር፤ ዘጸ. 7፥20:21። ካ. 1መ።

**ዓናቶት፤** ከኢየሩሳሌም በስተሰሜን 5 ኪ. ሜ. ርቆ የሚገኝ መንደር። የካህኑ አብያታር መኖሪያ ነበረ። ሰሎሞን ከሻረው በኋላ ወደዚያ ስፍራ ሰደደው፤ 1ነገ. 2፥26። የኤርምያስም መኖሪያ ነበረ፥ ስለዚህ ኢየሩሳሌም በተከበበ ጊዜ በዓናቶት አንድ የእርሻ መሬት ከዘመዱ ገዛ፤ ኤር. 1፥1፤ 32፥7-9።

**ዓውሎ ነፋስ፤** ኃይለኛ ነፋስ፤ ምሳ. 1፥27፤ ኢሳ. 5፥28። ሰው ሳያስብ ቶሎ ስለሚደርስበት የእግዚአብሔር ፍርድ ምሳሌ ነው፤ ምሳ. 10፥25፤ ኢሳ. 17፥13፤ ናሆም 1፥3። የመንፈስ ቅዱስ መገለጫ ነው፤ ሐ.ሥ. 2፥2።

**ዓውደ ዓመት፤** በየዓመቱ የሚከበር የዓመት በዓል፤ ኢሳ. 30፥29።

**ዓዛርያስ፤** ትርጉሙ «እግዚአብሔር ረድቷል» ማለት ነው። በዚህ ስም ብዙ ሰዎች ተጠርተዋል። ከእነርሱም የታወቁ 1. ዖዝያን በመባል የሚጠራው የይሁዳ ንጉሥ፤ «ዖዝያን» ይመ.። 2. ንጉሥ ዖዝያንን የተቃወመው ሊቀ ካህናት፤ 2ዜ.መ. 26፥17-20።

**ዓይበት፤** ከወይፈን ቆዳ የሚሠራ አቁማዳ ጭልፋ፤ ዘፍ. 42፥25:28።

**ዓይነ ርግብ፤** 1. ከሐር ክር የሚታታ የሴቶች የፊት መሸፈኛ ጌጥ፤ ኢሳ. 3፥23። 2. የተታታ የመስኮት መዝጊያ፤ 2ነገ. 1፥2።

**ዓይን ሮጌል፤** የቄድሮንና የሄኖም ሸለቆዎች በሚጋጠሙበት ቦታ ከኢየሩሳሌም በስተደቡብ የሚገኝ የውሃ ጉድጓድ። የብንያምና የይሁዳ ድንበር እስከ ዓይን ሮጌል ይደርሳል፤ ኢያሱ 18፥16። አኪማአስና ዮናታን ወደ ዳዊት ወሬ ለማምጣት በዚህ ቦታ ተሸሽገው ነበር፤ 2ሳሙ. 17፥17-22። አዶንያስ በዚህ ቦታ በሰሎሞን ላይ ዐመፀ፤ 1ነገ. 1፥9።

**ዓይንዶር፤** በናዝሬትና በታቦር ተራራ መካከል የነበረ ከተማ። ሳኦል መናፍስትን የምትጠራ ሴት በዓይንዶር ጠየቀ፤ 1ሳሙ. 28፥7።

**ዓይንጋዲ፤** ከመሳዳ 18 ኪ.ሜ. ያህል ርቆ በስተሰሜን በኩል የሚገኝ ምንጭ። ከጨው ባሕር ድንበር በስተምዕራብ ሌላ ምንጭ የለም። ዳዊት ከሳኦል ሸሽቶ በዓይንጋዲ ተሸሸገ፤ 1ሳሙ. 23፥29፤ 24፥1-6። በዚህ ቦታ ኢዮሣፍጥ ጠላቶቹን ድል ነሣ፤ 2ዜ.መ. 20፥2።

**ዓዶላም፤** ዋሻ። መማጠኛ ማለት ነው። ከኢየሩሳሌም ወደ ኬብሮን በሚወስደው መንገድ በስተምዕራብ በተራራ ላይ ያለ ዋሻ። ዳዊት ከንጉሥ ሳኦል ፊት በኰበለለ ጊዜ፥ አራት መቶ ሰው ሰብስቦ በዓዶላም ተደበቀ፤ 1ሳሙ. 22፥1:2።

**ዔሊ፤** ከአሮን ቤተሰብ የተገኘ፥ በሊቀ ካህንነትና በፈራጅነት በእስራኤል ያገለገለ ሰው። በዘመኑ የእግዚአብሔር የመቅደሱ ድንኳን በሴሎ ተተክሎ ነበር፤ 1ሳሙ. 1፥9፤ 4፥18፤ 14፥3፤ 1ነገ. 2፥27። አፍኒንና ፊንሐስ የተባሉት የዔሊ ልጆች እግዚአብሔርን ባለመፍራታቸው ከመንገዱ ተለይተው ተገኙ። አባታቸውም ምንም ካህን ቢሆን በሚገባ ልጆቹን አልገሠጻም፤ በደካማነቱም ተነቀፈ፤ 1ሳሙ. 2፥11-26። በመቅደሱ ያገለግለው የነበረው ወጣቱ ሳሙኤል ከእግዚአብሔር የተገለጠለትን በማስታወቅ በዔሊ ቤት ላይ ከባድ ፍርድ

እንደሚደርስበት ነገረው፤ 1ሳሙ. 3፥11-14።

እግዚአብሔርም የተናገረው ነገር ተፈጸመ። ልጆቹ በጦር ሜዳ ላይ በጠላት እጅ ተመትተው ሞቱ። በውጊያውም ላይ የእግዚአብሔር ታቦት ስለተማረከ፥ ዔሊ ከድንጋጤ የተነሣ ወድቆ ሞተ፤ 1ሳሙ. 4፥10-18። ክህነትም ከዔሊ ቤት ተወስዶ ለሌላ በተሰጠ ጊዜ፥ እግዚአብሔር የፈረደበት ፍርድ ተግባራዊ ሆነ፤ 1ነገ. 2፥26-27:35።

**ዔሳው፤** ይስሐቅና ርብቃ ከወለዷቸው መንታ ልጆች አንዱ፤ ዘፍ. 25፥25። ከእናቱ ማኅፀን የመጀመሪያ ሆኖ የወጣው ዔሳው ስለሆነ፥ እንደ ታላቅ ይቈጠር ነበርና የብኵርና መብት የእርሱ ነበረ። ነገር ግን ብኵርናውን በመናቅ ከበረሃ ደክሞ በመጣበት ቀን፥ የተሰማውን ራብ ለማስታገሥ ሲል፥ ወንድሙ ያዕቆብ ያዘጋጀውን ወጥ መርጦ መብቱን ሸጠ፤ ዘፍ. 25፥30-34። ከኬጢያውያን ወገን የሆኑትን ሁለት ሚስቶች አገባ። እነዚህ ሴቶች ግን ለይስሐቅና ለርብቃ የሐዘን ምክንያት ሆኑ፤ ዘፍ. 26፥34-35። ወንድሙ ያዕቆብ ብኵርናውን ስለወሰደበት ሊያጠፋው አሰበ፤ ዘፍ. 27። በኋላ ግን ከያዕቆብ ጋር ታረቀ፤ ዘፍ. 32፥7-33፥15። ለዔሳው «ኤዶም» የተሰኘ ሁለተኛ ስም ወጣለት። ትርጕሙም ቀይ ማለት ነው። ይህን ስም ሊያገኝ የቻለው ያዕቆብ ያዘጋጀውን ቀይ ወጥ በመውደዱ ነው።

ኤዶም ተባለና በሴይር ተራራ ለሚኖሩ ኤዶማውያን አባት ሆነ፤ ዘፍ. 36፥9። አንዳንድ ጊዜ ግን እነዚህ ሕዝቦች «የዔሳው ልጆች» እየተባሉ ይጠራሉ፤ ዘዳ. 2፥4። እንዲሁም የዔሳው ቤት፥ ወይም ዔሳው ተብሎም ይጠቀሳል፤ ኤር. 49፥8። በመ.ቅ. እንደተገለጠልን ሁለቱ ልጆች ሳይወለዱ ከሁለቱ እግዚአብሔር የመረጠውና የባረከው ያዕቆብን ነው። ዔሳው ግን ብኵርናውን የናቀ በመሆኑ እግዚአብሔር እንደጠላው ሆኖ ይቈጠራል፤ ሚል. 1፥2-3፤ ሮም 9፥9-13። በአዲስ ኪዳንም የማያምንና ዓለማዊ የሆነ ሰው ምሳሌ ሆኗል፤ ዕብ. 12፥16-17።

**ዔናቅ፤** የዔናቅ ልጆች አባት። የዔናቅ ልጆች ረጃጅምና ኃያላን በመሆናቸው እስራኤልን አስፈሩ፤ ዘኍ. 13፥32:33። ኢያሱ ብዙዎቹን ገድሏቸዋል። ካሌብም ከኬብሮን አባረራቸው። አንዳንዶች ግን በፍልስጥኤማውያን አገር ቀሩ፤ ኢያሱ 11፥21:22፤ 14፥6-15። ጎልያድ ከእነዚህ ዘር እንደተወለደ በአንዳንድ መተርጕማን ይነገራል።

**ዔድን፤** ቃሉ ደስታ ማለት ነው። ዔድን ከእስራኤል አገር በስተምሥራቅ ነበረ። ቦታው በእርግጥ የት እንደሆነ ዛሬ አይታወቅም። ግን በጤግሮስና በኤፍራጥስ ምንጮች አጠገብ እንደሚገኝ ከጥንት ጀምሮ ይታሰብ ነበር። ከጥፋት ውሃ የተነሣ የወንዞቹ መስመር ተለውጦ ይሆናል። እግዚአብሔር በዔድን ገነት የተባለውን የአትክልት ቦታ አዘጋጀ፤ በዚያም ሰውን አኖረ፤ ዘፍ. 2፥8-15። በአሦር ዘመነ መንግሥት በመስጴጦምያ ዔድን የተባለ አገር ነበር፤ 2ነገ. 19፥12።

**ዔጽዮን ጋብር፤** በኤርትራ ባሕር ዳር በኤሎት (በኤላት) አጠገብ ያለ ከተማ። ንጉሥ ሰሎሞን በዚህ ከተማ መርከቦችን ሠራ፤ 1ነገ. 9፥26። ዛሬም እንደገና ወደብ ሆኗል። ካ.2በ።

**ዕረፍት፤** ከድካም፥ ከሥራ ማረፍ። እግዚአብሔር በሰባተኛው ቀን ከመፍጠር ሥራ ዐረፈ (ዘፍ. 2፥2)፤ ሰባተኛውም ቀን ለሰው የተቀደሰ የዕረፍት ቀን ሆነ፤ ዘጸ. 31፥15። ለምድር በሰባተኛ ዓመት የዕረፍት ሰንበት ሙሉ ዓመት ተሰጠ፤ ዘሌ. 25፥4-7። እስራኤል በከነዓን ዕረፍት እንደሚያገኙ (ዘዳ. 3፥20)፥ ወደዚህም ዕረፍት ከባቢሎን ምርኮ በኋላ እንደሚገቡ ተስፋ ተሰጣቸው፤ ኤር. 46፥27። ጠላቶች ስላልተነሡበት ሰሎሞን የዕረፍት ሰው ተባለ፤ 1ዜ.መ. 22፥9። እስራኤል ባለማመናቸውና ባለመታዘዛቸው ዕረፍትን አላገኙም፤ መዝ. 95፥8-11። ምእመናን ግን በክርስቶስ ዕረፍትን ለነፍሳቸው ያገኛሉ (ማቴ. 11፥28-30)፤ ወደፊትም ወደ እግዚአብሔር ዕረፍት ይገባሉ፤ ዕብ. 4፥3-11።

**ዕራቁት፤** ያለ ልብስ መሆን፤ ዘፍ. 2፥25። በመጀመሪያ ሰዎች ዕራቁታቸውን ነበሩ፤ ግን በኃጢአት ከወደቁ በኋላ ንጹሕ ባልሆነ ዓይን ዕራቁትነታቸውን ሲመለከቱ አፈሩ፤ ዘፍ. 3፥7-11። በምሳሌነት ጕድለትን ያመለክታል፤ ዘፍ. 42፥9፤ ራእ. 3፥17። ኖኅ ሰክሮ ዕራቁቱን ሆነ፤ ዘፍ. 9፥21። ሰው ወደዚህ ዓለም ዕራቁቱን ሆኖ ይመጣል፤ ይመለሳልም፤ ኢዮብ 1፥21።

**ዕርቅ፤** ጥል ባለባቸው በሁለት ሰዎች መካከል ሰላም ሲሆን ዕርቅ ይባላል። በኃጢአት ምክንያት በእግዚአብሔር ዘንድ ጠላትነት ያለው ሰው በክርስቶስ ሞት መሠረት በእምነት ከእግዚአብሔር ጋር ሰላምንና ኅብረትን ማግኘቱም ዕርቅ ይባላል። እግዚአብሔር በጸጋው ሰውን ከራሱ ጋር ያስታርቃል፤ ሮም 5፥10:11፤ 2ቆሮ. 5፥18-20፤ ኤፌ. 2፥16፤ ቈላ. 1፥19:20። ሰዎች ከእግዚአብሔር ጋር ሲታረቁ እርስ በርሳቸውም ይታረቃሉ፤ አይሁድ፥ አሕዛብ በክርስቶስ አንድ ሆነዋል፤ ኤፌ. 2፥14-16። ምእመናን ጥል ቢኖርባቸው እንዲታረቁ ታዝዘዋል፤ ፊል. 4፥2። የሚያስተራርቁ ብፁዓን ናቸው፤ ማቴ. 5፥9።

**ዕርድ፤** ጕድብ፤ በጦርነት ጊዜ የሚሠራ እንደ ምሽግ ያለ፤ 2ነገ. 25፥1።

**ዕርገት፤** ከታች ወደ ላይ መውጣት። ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በዚህ ዓለም የነበረውን ሥራ ጨርሶ ወደ ሰማይ ዐረገ። በአብ ቀኝም ተቀመጠ። በሥጋ እንዳረገ እንዲሁ በዓለም ፍጻሜ ይመጣል፤ ሐ.ሥ. 1፥6-11፤ ሉቃ. 24፥50:51። ከማረጉ የተነሣ የሚከተሉትን ነገሮች እናስተውላለን።

1. ወደ ሰማይ ካረገ በኋላ በመስቀል ላይ የሠራው የመሥዋዕትነት ሥራ ሁሉ ፍጹም ሆነ፤ ዕብ. 9፥11:12።

2. በሥልጣን በአብ ቀኝ ተቀመጠ፤ ዕብ. 10፥12።

3. የመንፈስ ቅዱስን ተስፋ ከአብ ተቀብሎ መንፈስ

ቅዱስን ለምእመናን ሰጠ፤ ሐ.ሥ. 2፥33።

4. የቤተ ክርስቲያን ራስ ሆነ፤ ኤፌ. 1፥19-23።

5. ሕዝቡን ይጠብቃል፤ ሮም 8፥34፤ ዕብ. 7፥25፤ 1ዮሐ. 2፥1።

6. ቦታ ያዘጋጅልናል፤ ዮሐ. 14፥2።

7. ጠላቶቹ ሁሉ እስኪሸነፉ ድረስ ይጠብቃል፤ ዕብ. 10፥13።

**ዕቃ፤** ከማዕድን፥ ከእንጨት፥ ከሌላም የሚሠራ ማናቸውም ዓይነት መሣሪያ፤ በብ.ኪ. ዘመን ብዙ የቤተ እግዚአብሔር መገልገያ ዕቃ ነበረ፤ ዘጸ. 35፥16፤ ዳን. 1፥2። የእግዚአብሔር ፈቃድ በሰዎች ስለሚፈጸም አንዳንድ ጊዜ ሰዎች «ዕቃ» ተብለዋል፤ ሮም 9፥20-24፤ 2ጢሞ. 2፥20:21። በተለይም ጳውሎስ ምርጥ ዕቃ ይባላል፤ ሐ.ሥ. 9፥15።

**ዕቃ ቤት፤** የቤተ መቅደስ ዕቃዎች ሁሉ የሚቀመጡበት ቤት። ሕዝቅኤል በተለይ ስለ ዕቃ ቤት አንድ ምዕራፍ ጽፏል፤ ሕዝ. 42። የዕቃ ቤቱም ጠባቂ «ዕቃ ቤት» ተብሎ ይጠራል፤ 2ነገ. 10፥22።

**ዕቡይ፤** ትዕቢተኛ፤ ምሳ. 16፥19።

**ዕብራዊ፤** ዕብራውያን፤ ቃሉ ከአብርሃም ቅድመ አያት ከዔቦር ስም የተመሠረተ ይመስላል፤ ዘፍ. 10፥21። በመ.ቅ. አብርሃምንና ዘሩን ያመለክታል፤ ዘፍ. 14፥13፤ ዘጸ. 5፥1-3፤ 1ሳሙ. 13፥3። በአ.ኪ. ዜግነትን ብቻ ሳይሆን ሕግን የመጠበቅንም ሁኔታ ያሳያል፤ ፊል. 3፥5።

## ወደ ዕብራውያን የተጻፈ መልእክት

በመልእክቱ ውስጥ አንዳንድ ፍንጮች ቢገኙም (13፥19:23-24)፥ ይህ መልእክት በማን፥ ከየት፥ ወዴት፥ በምን ጊዜና በምን ምክንያት እንደተጻፈ ለማወቅ አስቸጋሪ ነው። ከቀድሞ ጀምሮ ብዙ ሊቃውንት ጳውሎስ የጻፈው መሆኑን በማመን ርእሱን «የጳውሎስ መልእክት ወደ ዕብራውያን» ሲሉት ይታያል። ሆኖም ግን መልእክቱ የጳውሎስን ስም አይጠቅስም፤ የአባቡም አገላለጥ ከሚታወቀው የጳውሎስ አገላለጥ ለየት ይላል። ስለዚህ አንዳንድ የመጽሐፍ ቅዱስ ምሁራን በርናባስ፥ አጵሎስ ወይም ቀሌምንጦስ ጽፎታል ይላሉ። ሌሎች ደግሞ ጳውሎስ የአይሁድ ትምህርት ሊቅ በመሆኑ (ገላ. 1፥14)፥ ይህን መልእክት ለየት በሚል አገላለጥ ሊጽፍ የቻለው ለአይሁድ ሲል ነው ይላሉ። የመልእክቱ ተቀባዮች የብ.ኪ.ን ትምህርትና ታሪክ የሚያውቁ ናቸው። ከእምነታቸው የተነሣ መከራ ቢቀበሉም፥ ከወገናቸው የተገደለ አልነበረም፤ 10፥32-34፤ 12፥4። የተጻፈበት ዘመን ሮማውያን የኢየሩሳሌምን ቤተ መቅደስ ካፈረሱበት ከ70 ዓ.ም. በፊት ይመስላል፤ 13፥10። ስለ መልእክቱ ብዙ ነገር ባይታወቅም የጸሐፊው ዓላማ ግልጥ ነው፥ ይኸውም አንባቢዎች በከባድ ተጽዕኖ ምክንያት ወደ ይሁዲነት በማፈግፈግ ክርስቶስን እንዳይክዱ ለማስጠንቀቅና ክርስቶስ ሊቀ ካህናት ሆኖ ሰውን ከእግዚአብሔር ጋር ማስታረቅን ለማስገንዘብ ነው። መልእክቱ በዝርዝር ሲታይ የሚከተሉት ይዘቶች ይታዩበታል :-

ሀ) በክርስትናና በብ.ኪ. መካከል ያለው ንጽጽር። ክርስቶስ ከሁሉ እንደሚበልጥና የክርስትና መንገድ የተሻለ መሆኑ 15 ጊዜ ተጽፏል።

ለ) የአሮን ዘሌዋውያን ሥርዓት ማብራሪያዎች።

ሐ) የክህነት ትምህርት አጽንዖት።

መ) በሃይማኖት ተግባራት ተሳታፊዎች ለነበሩ ሰዎች የተሰጡ ከባድ ማስጠንቀቂያዎች፤ 2፥1-4፤ 6፥4-8፤ 10፥32-39።

ሠ) የእምነት ጀግኖች አርአያነት።

አከፋፈል :-

1. የአሁኑ የእግዚአብሔር መገለጥ ብልጫ፤ 1፥1-4

2. ከብ.ኪ. አገልጋዮች ክርስቶስ የሚበልጥ ስለመሆኑ፥

ሀ) ከመላእክት (1፥5-2፥18)፥

ለ) ከሙሴ (3፥1-4፥13)፥

ሐ) ከአሮንና በክህነቱም (4፥14-7፥28)፥ ስለሚበልጥ ምእመናን በኑሮአቸው ሁሉ ትጋትን እንጂ ቸልተኝነትን ማሳየት አይገባቸውም።

3. የክርስቶስ አገልግሎት የሚበልጥ ስለመሆኑ፥

ሀ) የተሻለውን ቃል ኪዳን ደንግጓል (ም.8)

ለ) ወደ ተሻለው መቅደስ ገብቷል (9፥1-12)

ሐ) የተሻለ መሥዋዕት አቅርቧል (9፥13-10፥18) ስለዚህ ምእመናን እስከ መጨረሻው መጽናት ይገባቸዋል፤ 10፥19-39።

4. ለአንባቢዎች ታላቅ ማበረታቻ ስለመስጠት፥

ሀ) የጥንት የእምነት ጀግኖች አሸናፊነት (ም. 11)፥

ለ) የክርስቶስ አርአያነት (12፥1-3)፥

ሐ) ልዩ ልዩ ማደፋፈሪያዎች (12፥4-13)፥

መ) ልዩ ልዩ ማስጠንቀቂያዎች (12፥14-29)።

5. መደምደሚያ፤ ም. 13

ሀ) ልዩ ልዩ ትእዛዛትና ምክር (13፥1-17)፥

ለ) የጸሎት ጥያቄ (13፥18-19)፥

ሐ) ቡራኬ (13፥20-21)፥

መ) ማስታወሻዎችና የመጨረሻ ሰላምታ (13፥22-25)።

**ዕብራይስጥ፤** የዕብራውያን ቋንቋ ማለት ነው። በመጽሐፍ ቅዱስ የከነዓን ቋንቋ፥ የአይሁድ ቋንቋ፥ ወይም ዕብራይስጥ ተብሎ ይጠራል፤ ኢሳ. 19፥18፤ 2ነገ. 18፥26፤ ዮሐ. 5፥2። ከጥቂት ምዕራፎች በቀር አብ.ክ. በሙሉ የሚቀበሉአቸው የብሉይ ኪዳን መጻሕፍት በዕብራይስጥ ተጻፉ። ከብ.ኪ. ጸሐፊዎች ዘመን ወዲህ ቀስ በቀስ በጊዜ ብዛት

የዕብራይስጥ ቋንቋ ዘመን ያመጣቸው ቃላት ተጨምረው ይለዋወጥ እንጂ ጥንት የተነገረውና ዛሬ የሚነገረው ቋንቋ አንድ መሆኑ አልቀረም።

አጻጻፉ ከቀኝ ወደ ግራ ነው። ፊደሎቹ 22 ናቸው፤ በተጨማሪም ለድምፅ ሰጪነት በተለመደ ዓይነት አነባበብና አጠራር የተለያዩ ነጥቦች በአይሁድ ሊቃውንት ተጽፈዋል። ከእነዚህም ሌላ፥ በቅዱሳት መጻሕፍት የዜማ ምልክቶች (ነጥቦች) ተጨምረው ሊጻፉ ይችላሉ።

ዕብራይስጥ፥ ዐረብኛ፥ ሱሪስት፥ አራማይክና ግእዝ ይመሳሰላሉ። ደግሞም አንዳንድ ጥሬ ቃላት ከዕብራይስጥ ወደ ግእዝና ወደ አማርኛ ገብተዋል፤ ለምሳሌ አሜን፥ መና፥ ሃሌ ሉያ፥ ሰይጣን የዕብራይስጥ ቃላት ናቸው።

ፊደሎቹ የሚከተሉት ናቸው :-

| | | | |
|---|---|---|---|
| አሌፍ | א | ላሜድ | ל |
| ቤት | ב | ሜም | מ |
| ጋሜል | ג | ኖን | נ |
| ዳሌጥ | ד | ሳምኬት | ס |
| ሄ | ה | ዔ | ע |
| ዋው | ו | ፌ | פ |
| ዛይ | ז | ጻዴ | צ |
| ሔት | ח | ቆፍ | ק |
| ጤት | ט | ሬስ | ר |
| ዮድ | י | ሳን (ሺን) | ש |
| ካፍ | כ | ታው | ת |

ለእትሞች በእነዚሁ ፊደላት ይጠቀማሉ፤ የእጅ ጽሑፉና ጥንታዊው የፊደል መልክ በመጠኑ ከዚህ ለየት ይላሉ። «አሌፋት» ይመ.

**ዕብነ በረድ**፤ እየተጠረበ፥ እየተፋቀም ለሕንፃ፥ ለሐውልትና ለቤት ዕቃ የሚሆን እንደ በረዶ ነጭነት ያለው ድንጋይ፤ አስ. 1፥6፤ 1ዜ.መ. 29፥2።

**ዕብደት**፤ የአንጎል በሽታ። እግዚአብሔር ሰዎችን በዕብደት መቅሠፍት ይመታል፤ ዘዳ. 28፥28፤ ዘካ. 12፥4። ሰው ራሱን ለዕብደት አሳልፎ ሊሰጥ ይችላል፤ መክ. 1፥17። «በሽታ»፥ «ጋኔን» ይመ.

**ዕንቍ**፤ የከበረ ድንጋይ የሚባለው ሁሉ በየዓይነቱ። ባንዳንድ የአ.ኪ. ጥቅስ ሉል ማለት ሳይሆን አይቀርም፤ እርሱም ከባሕር የሚገኝ፥ ሰዳፍ የምትወልደው ዕንቍ ነው፤ ማቴ. 13፥45፤ ራእ. 21፥21። በብ.ኪ. ዕንቆች ከወርቅና ከብር ጋር ለሚከተሉት ዕቃዎች ይጠቀሙ ነበር :- ለዘውድና ለአክሊል፥ ለአንባርና ለድሪ፥ ለጆሮ ጕትቻ፥ ለአፍንጫና ለጣት ቀለበት፥ ለእግር አልቦና ለሸቱ ዕቃ፤ ሕዝ. 16፥11:12። ጌጥ ስለሚያኮራ አንዳንድ ጊዜ ለአይሁድ እንቅፋት ሆኗል (ኢሳ. 3፥18-23)፤ በአዲስ ኪዳንም፥ ሰውነቷን በዕንቍ የምትሸልም ክርስቲያን ሴት አትመሰገንም፤ 1ጢሞ. 2፥9:10። በብ. ኪ. ሊቀ ካህናት የደረት ልብስ ላይ የዐሥራ ሁለት ዕንቆች ፈርጥ ይደረግ ነበር። ዕንቆቹም የዐሥራ ሁለቱ ነገድ መታሰቢያ ነበሩ። እንዲሁም በአ.ኪ. የአዲሲቱ ኢየሩሳሌም ዐሥራ ሁለት መሠረቶችና ዐሥራ ሁለት ደጆች በዐሥራ ሁለት ዕንቆች እንደተሠሩ ተገልጧል።

**የሚያብረቀርቅ ዕንቍ**፤ ዕንቍ፤ ብርሃን ሲያርፍበት በጣም ብልጭልጭ የሚል ቀይ ወይም አረንጓዴ ዓይነት የከበረ ድንጋይ፤ ዘጸ. 28፥17፤ ኢሳ. 54፥12።

**ዕንባቆም**፤ 600 ዓመት ያህል ከክ.ል. ትንቢት የተናገረ ነቢይ። በይሁዳ የኖረ ይመስላል፥ ስለ ሕይወት ታሪኩ ግን ማስረጃ የለም። በቤል ታሪክ ውስጥ ዕንባቆም ከአገሩ ተነጥቆ ወደ ባቢሎን በመሄድ ከነቢዩ ዳንኤል ጋር እንደተገናኘ ተተርኳል። «የቤል ታሪክ» ይመ.

**የዕንባቆም ትንቢት**፤ ዕንባቆም የተነበየው በይሁዳ በነቢዩ ኤርምያስ ዘመን እንደነበረ አይጠረጠርም። ከለዳውያንና ባቢሎናውያን እየበረቱ ሄደው በኢየሩሳሌም ላይ በተነሡበት ዘመን እንደነበረ በም. 1፥5:6 ተገልጿል። የይሁዳ ክፋት እየባሰ በሄደበት በኢዮአቄም ዘመነ መንግሥት (609-597 ከክ.ል.) ትንቢት የተናገረ ይመስላል፤ 1፥2-4። ክፋትን ተመልክቶ እግዚአብሔር እንደ ቅንነቱ የማይፈርድ መስሎት ደጋግሞ ይጠይቃል። ዋና መልሱ «ጻድቅ በእምነቱ በሕይወት ይኖራል» የሚል ነው (2፥4)፤ አ.ኪ.ም ይህን ሦስት ጊዜ ጠቅሶታል ሮም 1፥17፤ ገላ. 3፥11፤ ዕብ. 10፥38።

አከፋፈል :-

1. ጥያቄ :- እግዚአብሔር በግፈኞች ላይ ለምን አይፈርድም? (1፥1-4)።

2. መልስ :- ከለዳውያንን እልክባቸዋለሁ (1፥5-11)።

3. ጥያቄ :- እንዴት! ከእኛ የባሱ አይደሉምን? (1፥12-17)።

4. መልስ :- በተራቸው ክፉዎች ሁሉ ይፈረድባቸዋል፤ ጻድቅ (የእግዚአብሔር ሰው) ግን እግዚአብሔርን አምኖ ይድናል (ም. 2)።

5. የዕንባቆም የጸሎት መዝሙር (ም. 3)።

**ዕውር**፤ ለማየት የማይችል፤ ዘሌ. 21፥18፤ 19፥14። በብዙ ጥቅስ ላይ ያለማስተዋል ምሳሌ ነው፤ ኢሳ. 35፥5፤ ሰቈ. 4፥14፤ ማቴ. 15፥14፤ 23፥16፤ 2ቆሮ. 4፥4፤ ራእ. 3፥17። ክርስቶስ ዕውራንን ፈወሰ፤ ማቴ. 11፥5፤ 12፥22፤ ማር. 10፥46-52፤ ዮሐ. 9፥1-7። «በሽታ» ይመ.

**ዕውቀት (እውቀት)**፤ ዕውቀት ሁሉ ከእግዚአብሔር ነው፤ መዝ. 94፥10፤ ዳን. 1፥17፤

2ዜ.መ. 1፥10:12፤ 1ቆር. 1፥5። ሕይወትን የሚያስገኘው ዕውቀት ክርስቶስን ማወቅ ነው፤ ዮሐ. 17፥3፤ ፊል. 3፥8:9፤ ቆላ. 2፥2:3፤ 1ጢሞ. 2፥3-6። በመጨረሻው ዘመን በዓለም ዕውቀት ይበዛል፤ ዳን. 12፥4። ዕውቀት ሊያኰራ ይችላል፤ 1ቆሮ. 8፥1-3። ዕውቀት ከመንፈስ ቅዱስ ስጦታዎች አንዱ ነው፤ 1ቆሮ. 12፥8። «የሕይወት ዛፍ» ይመ.

**ዕዝራ፤** ካህንና ጸሐፊ። ታሪኩ በመጽሐፈ ዕዝራ ተጽፎ የሚገኘው ነው። ዕዝራ በባቢሎን ምርኮኞች መካከል አደገ። ከአሮን ቤተሰብ የተወለደና እንደ ሙሴ ሕግ ካህን ከመሆኑም በላይ በሙሴ ሕግ ፈጣን ጸሐፊ ነበረ የሚል ቃል ተጽፎለታል፤ ዕዝ. 7፥1-6፥11። የፋርስ ንጉሥ አርጤክስስ በነገሠበት በሰባተኛው ዓመት፥ ይኸውም ከክ.ቤ በ458 ዓመት ዕዝራ ከንጉሡ አስፈቅዶ፥ ፈቃደኞች ከሆኑ አይሁድ መካከል 1800 ከሚያህሉ ወንዶች ጋር ወደ ኢየሩሳሌም ተጓዘ፤ ዕዝ. 8፥1-36። ዕዝራ ከመምጣቱ በፊት በአይሁድ አገር የነበሩት፥ ከምርኮ ከተመለሱት አይሁድ በብዙ ረገድ ተቸግረው ነበር። በእግዚአብሔርም ቃል የሚመራቸውን ሰው ከማጣታቸው የተነሣ፥ ከእግዚአብሔር መንገድ መውጣታቸው አልቀረም። ካህኑ ዕዝራ ግን የእግዚአብሔርን ሕግ ይፈልግና ያደርግ ዘንድ፥ ለእስራኤልም ሥርዓትንና ፍርድን ያስተምር ዘንድ ልቡን አዘጋጅቶ ነበርና ወደ ኢየሩሳሌም የመጣው የእግዚአብሔርን ቃል ለማስተማርና ሕዝቡ የተሳሳተበትን ነገር ለማስተካከል ነው፤ ዕዝ. 7፥10፤ ነህ. 8፥8። በተለይም ከይሁዳ አገር ሰዎች ብዙዎቹ የአረትን ትእዛዝ በማፍረስ ከእስራኤል ወገን ያልሆኑትን ሴቶች አግብተው ስለነበር፥ ከእነዚህ ሴቶች እንዲለዩ ዕዝራ ምክር ሰጣቸው፤ ዕዝ. 9-10። በዚህ ዘመንም የኢየሩሳሌም ሕዝብ የፈረሰውን የኢየሩሳሌምን ቅጥር ለመሥራት ብዙ ጥረት አደረጉ። ይሁን እንጂ በብዙ ጠላቶች ተቃውሞ ምክንያት ይህ ሥራ ለጊዜው አልተሳካላቸውም፤ ዕዝ. 4፥6-23። በ445 ከክ.በ. የፋርስ ንጉሥ የጠጅ አሳላፊ የነበረው ነህምያ ወደ ኢየሩሳሌም መጥቶ ቅጥሩን ሠራ። ዕዝራ በሥራው ተባብሮ ሕግን ለሕዝቡ በሰፊው አስተማረ፤ ነህ. 8-10።

**የዕዝራ መጽሐፍ፤** መጽሐፉ የእስራኤል ሕዝብ ከባቢሎን ምርኮ እንደተመለሱ ቤተ መቅደስም እንደገና እንደሠሩ ይናገራል። መጽሐፉ ከ537 አንሥቶ ዕዝራ ራሱ ወደ ኢየሩሳሌም እስከመጣበት እስከ 458 ከክ.በ. ያለውን ታሪክ ይተርካል። የእስራኤል ሕዝብ ቤተ መቅደሱን የጨረሱት በ516 ከክ.በ. ነው። መጽሐፉን፥ ወይም መጽሐፉ የተመሠረተባቸውን ረቂቆች ዕዝራ ራሱ የጻፋቸው ይመስላል፤ 7፥27-8፥1።

አከፋፈል ፦

ም. 1. ቂሮስ የእስራኤል ሕዝብ እንዲመለስ መፍቀዱ።

ም. 2. ከምርኮ የተመለሰው 42360 ሕዝብ መመዝገቡ።

ም. 3. የቤተ መቅደስ እድሳት መጀመሩ።

ም. 4. ጠላቶች የቤተ መቅደሱን የእድሳት ሥራ መቃወማቸው።

ሀ. በቂሮስ ዘመን ቤተ መቅደስ እንዳይሠራ፤ ቊ. 1-5:24።

ለ. በአርጤክስስ ዘመን የኢየሩሳሌም ቅጥር እንዳይሠራ፤ ቊ. 6-23።

ም. 5-6. በሐጌና በዘካርያስ ቀስቃሽነት ዘሩባቤል የቤተ መቅደሱን ሥራ መፈጸሙ።

ም. 7-8. እነዕዝራ ወደ ኢየሩሳሌም መመለሳቸው።

ም. 9-10. ዕዝራ አይሁድ ያላመኑትን እንዳያገቡ ማከልከሉ።

**ዕዝራ ሱቱኤል፤** ሱቱኤል (ሰላትያል) የጸሐፊው የዕዝራ ድርብ ስም ነው። መጽሐፈ ዕዝራ ሱቱኤልም ዕዝራ በተማረከበት አገር በባቢሎን ሳለ ስላያቸው ሰባት ራእዮች የሚተርክ መጽሐፍ ነው። የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤ.ክ. ከብ.ኪ. መጻሕፍት ጋር ቈጥራ ትቀበለዋለች።

**ዕዝራ ካልእ፤** መጽሐፈ ዕዝራ ካልእ በ2 ዜና መዋዕል 35-36፥ በመጽሐፈ ዕዝራ፥ በመጽሐፈ ነህምያ 7-8 የተጻፈውን ታሪክ በድጋሚ የሚተርክ መጽሐፍ ነው። የኦርቶዶክስና የካቶሊክ አብ.ክ. ከብ.ኪ. መጻሕፍት ጋር ቈጥረው ይቀበሉታል።

**ዕዳ፤** ሰው ዕዳውን ባይከፍል ይታሰር፥ ለባርነትም ይሸጥ ነበር፤ ዘጸ. 22፥3፤ 2ነገ. 4፥1፤ አሞጽ 2፥6፤ ማቴ. 5፥25:26፤ 18፥23-25። የክርስቲያን ተገቢ ዕዳ ግን ፍቅር ብቻ ነው፤ ሮም 13፥8። መንፈስን የመከተል ዕዳም አለበት፤ ሮም 8፥12።

**ዕጣ፤** ዕድል ፈንታ፥ ድርሻ፤ ኢያሱ 15፥1። ዕጣ በዕንጨት፥ የጽሑፍ ምልክት ባለበት ጠጠር (ድንጋይ) ይጣላል። በብሉይ ኪዳን ሁለት መደበኛ ዕጣ ነበረ፤ ዘሌ. 16፥8-10። ዕጣ በስውር ይጣላል፤ ምሳ. 16፥33። የቀድሞ ሰዎች ርስትን ለማካፈል (ኢያሱ 18፥8-11)፥ ምቹ ጊዜን ለማወቅ (አስ. 3፥7)፥ ተረኛን ለመመደብ (1ዜ.መ. 24፥7-19)፥ ጥፋተኛውን ለማውጣት (ዮናስ 1፥7) ዕጣ ይጥሉ ነበር። ወታደሮች በክርስቶስ እጀ ጠባብ ዕጣ ተጣጣሉ፤ ዮሐ. 19፥24። በይሁዳ ምትክ ሰው እንዲሾም ዕጣ ተጣለ፤ ሐ.ሥ. 1፥24-26።

**ዕጣን፤** በበረሀ ከሚበቅል የዕጣን እንጨት የሚለቀም ሙጫ። ከሌላ ሽቱ ጋር ተቀምሞ በእግዚአብሔር ድንኳንና መቅደስ ውስጥ ይታጠን ነበር፤ ዘጸ. 30፥34-38፤ ዘሌ. 16፥12:13። ጢሱም የምስጋናና የጸሎት ምሳሌ ነው፤ መዝ. 141፥2፤ ማቴ. 2፥11፤ ራእ. 5፥8፤ 8፥3:4።

**የዕጣን መሠዊያ፤** የዕጣን ማጨሻ። እንደ ዋና አይወዘወዝም። ሙሴ የዕጣኑን መሠዊያ ካሠራ በኋላ በእግዚአብሔር ማደሪያ በቅድስት ውስጥ



የዕጣን ዛፍ

አኖረው፤ ዘጸ. 30፥1-10። ሰሎሞን ለቤተ መቅደስ አዲስ የዕጣን መሠዊያ አሠራ፤ 2ዜመ. 4፥19-21። የዕጣኑ መሠዊያ በታቦቱ አጠገብ ካለው መጋረጃ ፊት በቅድስት የሚገኝ ቢሆንም፥ እንደ ቅድስተ ቅዱሳን ዕቃ ይቈጠር ነበር፤ ዘጸ. 30፥6፣ 1ነገ. 6፥22፤ ዕብ. 9፥4። «ጥና» ይመ.



ከወርቅ የተሠራ የዕጣን መሠዊያ

**ዕፀ ሳቤቅ፤** እርስ በርሱ የተያያዘ ሐረግ፤ ዘፍ. 22፥13።

**ዖሜጋ፤** የግሪክ ቋንቋ የመጨረሻ ፊደል ስም፤ ራእ. 1፥8፤ 22፥13። «ግሪክ» ይመ.

**ዖዝያን፤** ትርጒሙ «እግዚአብሔር ኃይሌ ነው» ማለት ነው። በዚህ ስም የታወቀው ከ791-740 ከክ.በ. ንግሥ የነበረው የይሁዳ ንጉሥ ነው። ዖዝያን በተጨማሪ ዓዛርያስ ተብሎ ይጠራ ነበር፤ በዘመኑም ነቢዩ ኢሳይያስ ነበረ። በመጀመሪያ በመልካም ሁኔታ ነግሦ መንግሥቱን አስፋፋና አጸና፤ እግዚአብሔርም ረዳው። ከበረታ በኋላ ግን ታበየና ወደ ቤተ መቅደስ ገብቶ ዕጣን አጠነ። የካህን ሥራ ስለሠራ፥ ካህናትም ቢገሥጹት ስለተቈጣቸው በለምጽ ተቀሠፈ፤ 2ነገ. 14፥21:22፤ 15፥1-7፤ 2ዜ.መ. 26።

**ዖጽ፤** የኢዮብ አገር፤ ኢዮብ 1፥1። የት እንደነበረ ዛሬ ለማረጋገጥ አይቻልም። ነገር ግን ታሪኩን በመመልከት በኤዶም አቅራቢያ የነበረ ይመስላል። በሌላም በኩል የአብርሃም የወንድም ልጅ በዚህ ስም ይጠራ ነበርና ስለዚህ ዖጽ በዑር አካባቢ እንደነበረ የሚገምቱ አሉ፤ ዘፍ. 22፥21፤ ሰ.ኤ. 4፥21።

**ዖፌል፤** የኢየሩሳሌም ቤተ መቅደስ ለተሠራበት ተራራ ደቡባዊ ክፍል፤ 2ዜ.መ. 33፥14። «ኢየሩሳሌም» ይመ.

**ዘለላ፤** የወይን ፍሬ፤ በወይን ሐረግ ላይ ጭፍቅፍቅ ብሎ ተነባብሮና ተንዠርግጎ የማሽላ መታጂ (ራስ) መስሎ የሚታየው የወይን ፍሬ የወይን ዘለላ ይባላል፤ ዘኍ. 13፥23።

**ዘለዓለም፤** ሁልጊዜ፥ ፍጻሜና ወሰን የሌለው። እግዚአብሔር ከዘለዓለም እስከ ዘለዓለም ነው፤ መዝ. 90፥2። እርሱ ዓለምን ፈጠረ፤ ነገር ግን በጊዜ አይወሰንም፤ 2ጴጥ. 3፥8። ሰው በእግዚአብሔር መልክ ተፈጥሯልና በክብር ወይም በቅጣት ለዘለዓለም ይኖራል፤ ዳን. 12፥2፤ ማቴ. 25፥46። ቃሉ ያልተወሰነ ጊዜንም ያመለክታል፤ 1ሳሙ. 1፥22፤ ፊልሞና 15።

**የዘለዓለም ሕይወት፤** የዘለዓለም ሕይወት እግዚአብሔርን፥ አንድ ልጁን ኢየሱስ ክርስቶስን ማወቅ ነው። አብና ወልድ ለዘለዓለም ይኖራሉ፤ ሕይወትም ከእነርሱ ነውና የሚያውቃቸው ለዘለዓለም በሕይወት ይኖራል፤ ዮሐ. 5፥25:26፤ 11፥25፤ 14፥6፤ 17፥3። በክርስቶስ የሚያምን የዘለዓለም ሕይወት አሁን አለው፤ ዮሐ. 3፥16:36፤ 1ዮሐ. 5፥11:12። ይህ ሕይወት ስጦታ ነው፤ ሮም 6፥23። ምእመናን የዘለዓለም ሕይወት እንዳላቸው ማወቅ መብታቸው ነው (1ዮሐ. 5፥13)፥ መንፈስ ቅዱስም ወራሾች መሆናቸውን ያረጋግጥላቸዋል፤ ሮም 8፥15:17፤ ቲቶ 3፥6:7። ምእመናን በሥጋ ይሞታሉ፤ ነገር ግን ክርስቶስ ያስነሣቸዋል፤ ከፍርድም በኋላ ወደ መንግሥተ ሰማያት ይሄዳሉ፤ ከእርሱም ጋር ለዘለዓለም በደስታ ይኖራሉ፤ ኢዮብ 19፥25-27፤ መዝ. 16፥9-11፤ 17፥15፤ ኢሳ. 26፥19፤ ማቴ. 25፥46፤ ዮሐ. 6፥39:40፤ 2ቆሮ. 5፥1፤ ኤፌ. 2፥5-7፤ ይሁዳ 24:25፤ ራእ. 21፥1-7፤ 22፥1-5።

**ዘሌዋውያን፤** 3ኛው የሙሴ መጽሐፍ። ሌዋውያን ከ12 ነገድ የአንዱ የሌዊ ዘር ናቸው። የብ.ኪ. ካህናት ሌዋውያን ነበሩና «ዘሌዋውያን» በተባለው መጽሐፍ ውስጥ ስለ ሌዊ ክህነት በብዛት እናነባለን፤ ዕብ. 7፥11። እግዚአብሔር ራሱ ቅዱስ እንደሆነ፥ የእስራኤል ሕዝብ ከእነርሱ የተለዩ ቅዱሳን እንዲሆኑ ስለተመኘ፥ ኃጢአታቸውን የሚያስተሰርዩላቸውና ወደ እርሱ የሚያቀርቧቸው ካህናት ይሆኑላቸው ዘንድ ፈቅዶ የሌዊን ነገድ መረጠ። ከዚያም አሮንንና ልጆቹን ለክህነት ለየ። ከአሮን ወገን ያልሆኑ ሌሎችም ሌዋውያን ለእግዚአብሔር ማደሪያ አገልጋዮች እንዲሆኑ ተሾሙ፤ ዘሌ. 11፥44:45፤ ዘኍ. 1፥47-50፤ 3፥1-10፤ 18፥1-7። የዚህ መጽሐፍ ትእዛዛት የተሰጡት ሙሴ በሲና ተራራ ላይ ከእግዚአብሔር ጋር ሲነጋገር ነበር። የመጀመሪያዎቹ ትእዛዛት ሰው እግዚአብሔርን ደስ ለማሰኘት ሲወድ ምን ዓይነት መባ ማቅረብ፥ እንዴትም ማቅረብ እንደሚገባው ያስታውቃሉ (1-3)። ቀጥሎም ኃጢአተኛው ከእግዚአብሔር ተለይቶ እንዳይቀር ካህኑ ደም በማፍሰስ አስተስርዮ ኃጢአተኛውን እንዴት እንደሚያነጻና መልሶ ከእግዚአብሔር ጋር እንደሚያገናኘው ተገልጧል (4-7)። ከም. 8 ጀምሮ እስከ ም. 10 ድረስ የክህነት መቀደሻ ሕግ ስናገኝ በሚከተሉቱ ምዕራፎች ደግሞ የእግዚአብሔር ሕዝብ በመብሉ፥ በሰውነቱ፥ በልብሱ፥ በቤቱ፥ ንጹሕ (ቅዱስ) መሆን እንደሚገባው እናነባለን (11-15)። በም. 16 ላይ የታላቁ የማስተስረያ ቀን ሕግ ተሰጥቷል፤ ይህም ሕግ በተለይ በዕብ. 9 ላይ ተገልጿል። በም. 17 ሰው ደምን የማይበላበት ምክንያት ተጽፏል፤ ከእርሱ በኋላ የእግዚአብሔር ሕዝብ ከሌላ ወገን ሁሉ ልዩ መሆን ይገባቸዋልና ልዩ ልዩ ትእዛዛት ሲሰጡአቸው (18-25)፥ በመጨረሻዎቹ ምዕራፎች እግዚአብሔር «ብትሰሙኝ፥ ባትሰሙኝ» እያለ ለተሰጡአቸው ትእዛዛት ሁሉ እንዲታዘዙ ሕዝቡን ያስጠነቅቃቸዋል (26፤27)። «የአሪት ጸሐፊ» ይመ.

**ዘመን፤** ረዥም ጊዜ፥ ወይም አንድ ዓይነት አገዛዝ፥ አምልኮ፥ ሌላም ተግባር የተከናወነበት ጊዜ ሁሉ ዘመን ይባላል፤ ማር. 1፥15፤ ገላ. 4፥4፤ ኤፌ. 2፥6-7፤ 1ጴጥ. 1፥5።

**ዘመድ፤** ሥጋዊ ዝምድና ያለው። በብ.ኪ. የቅርብ ዘመዶች እንዳይጋቡ ተከልክሏል፤ ዘሌ. 18፥6-18። ሰው የዘመዱን ርስት መቤዠት ነበረበት (ዘሌ. 25፥25)፥ እንዲሁም የዘመዱን ደም መበቀል ተገቢ እንደሆነ ሊያስብ ይችል ነበር፤ ዘፍ. 9፥5:6። በአ.ኪ. ግን ቃሉ የቅርብ ዘመድን ወይም ጠቅላላውን ወገን ሊያመለክት ይችላል፤ ሉቃ. 14፥12፤ ሮም 9፥3።

**ዘምሪ፤** የባአስን ልጅ ኤላን የገደለው የእስራኤል ጦር አለቃ። ሰባት ቀን ነገሠ። ሕዝቡ ዘንበሪ የተባለውን የሠራዊት አለቃ ባነገሡ ጊዜ ዘምሪ ራሱን ገደለ፤ 1ነገ. 16፥9-20።

**ዘረፋ፤** በኃይል ሁሉን ወስዶ የራስ ማድረግ፤ ኢሳ. 42፥22።

**ዘሩባቤል፤** ዘሩባቤል ማለት የባቢሎን ዘር ማለት ነው። ከዳዊት ትውልድ፥ የምርኮኛው የዮአኪን (የኢኮንያ) የልጅ ልጅ ሆኖ በባቢሎን ተወለደ፤ በሥጋ የፈዳያ ልጅ፤ 1ዜ.መ. 3፥16-19፤ በሕግ የሰላትያል ልጅ፤ ማቴ. 1፥12። ወደ ኢየሩሳሌም ተመለሰ፤ ዕዝ. 2፥2። የይሁዳ አለቃ ሆኖ ቤተ መቅደስ አሠራ፤ ዕዝ. 3፥2፤ ሐጌ. 1፥1:14፤ ዘካ. 4፥6-10።

**ዘር፤** 1. በምድር ላይ የሚገኙ ቡቃያዎች ሁሉ የሚበዙበት ፍሬ፤ ዘፍ. 1፥11። 2. ከሰው የሚወለድ ልጅ ዘር ይባላል፤ ይህም እስከ ብዙ ትውልድ ድረስ ይሄዳል፤ ዘፍ. 3፥15፤ 13፥15፤ 21፥12፤ 28፥14። 3. ከወንድ ተከፍሎ ወደ ሴት ማኅፀን የሚተላለፈው ፈሳሽ ዘር ይባላል፤ ዘፍ. 38፥8-9፤ ዘሌ. 15፥16። ዘር ሕያው ነውና በምሳሌነት የእግዚአብሔርን ቃል (ማር. 4፥1-20፤ 1ጴጥ. 1፥23-25)፥ የእግዚአብሔርን መንግሥት እድገት (ማር. 4፥26-29)፥ የእግዚአብሔርን መንግሥት ልጆች (ማቴ. 13፥24-30:38)፥ መንግሥት ሰማያትንም (ማቴ. 13፥31:32) ይገልጣል። ደግሞም የአትክልት ዘር በመሬት ውስጥ ከፈረሰና ከበሰበሰ በኋላ ፍሬ እንደሚያገኝ ሁሉ፥ ሰውም የዘለዓለምን ሕይወት ለማግኘት ምኞቱንና ራሱን ይክዳል፤ ዮሐ. 12፥24-26። የሰው ሥጋዊ ሞትም በዘር መዘራት ተመስሏል። ይህም ወደ አዲስ ሕይወት ይደርሳል፤ 1ቆሮ. 15፥35-50።

**ዘቢብ፤** የደረቀ የወይን ፍሬ፤ 1ሳሙ. 25፥18።

**ዘብዴዎስ፤** የያዕቆብና የዮሐንስ አባት። ዓሣ አጥማጅ ነበረ፤ ማር. 1፥19:20፤ ማቴ. 27፥56።

**ዘኍልቍ፤** 4ኛው የሙሴ መጽሐፍ። «ዘኍልቍ» ማለት «የቍጥር» ማለት ነው። መጽሐፉ «ቍጥር» የተባለበት ምክንያት የእስራኤል ሕዝብ ብዛት ስለተጻፈበት ነው። ቈጠራው የተጀመረው እስራኤል ገና በሲና ተራራ ሥር ሰፍረው ሳሉ ነበር (1-5)። በመካከለኛዎቹ ምዕራፎች የምናገኘው ሕዝቡ ከሲና ተራራ ተነሥቶ እስከ ዮርዳኖስ ወንዝ ድረስ ያደረገውን የጕዞ ታሪክ ነው (6-25)። እስራኤላውያን በግማሽ መንገድ ላይ ቃዴስ በርኔ በተባለው ስፍራ ሳሉ ስላላመኑና ስላልታዘዙ፥ ያ ትውልድ ሁሉ በምድረ በዳ አለቀ፥ ስለዚህ ልጆቻቸው ከ40 ዓመት በኋላ በዮርዳኖስ ወንዝ አጠገብ ወደሚገኝ ወደ ሞዓብ አገር ሲደርሱ ሕዝቡ ዳግመኛ ተቈጠረ (26)። በዚሁ የሕዝብ ቈጠራ የወንዶች ጠቅላላ ድምር ስድስት መቶ ሺህ ያህል ሲሆን፥ ቤተሰቦቻቸው ሲጨመሩ ግን ከሁለት ሚሊዮን በላይ ሳይሆኑ አልቀሩም። ከዚያም ስለ ሙሴ መሞትና ስለ ኢያሱ መተካት፥ ስለ አሮን መሞት፥ ወደ አገራቸው ሲገቡ ስለሚያከብሩአቸው የዓመት በዓላትና ስለ አገሪቱ ድንበሮች ተገልጿል (27-36)። «የአሪት ጸሐፊ» ይመ.

አከፋፈል :-

1. በሲና ሰፍረው ሳሉ ለጕዞ መዘጋጀታቸው

(1፥1-10፥10)።

2. ከሲና ተራራ እስከ ቃዴስ ድረስ ያደረጉት ጉዞ (10፥11-ም. 12)።

3. አለመታዘዛቸውና በምድረ በዳ 40 ዓመት መንከራተታቸው (13-25)።

4. ወደ ከነዓን ለመግባት መዘጋጀታቸው (26-36)።

**ዘንዘና**፤ ከእንጨት ወይም ከብረት የሚሠራ የሙቀጫ ግልገል፤ ምሳ. 27፥22።

**ዘንበሪ**፤ ከ885 እስከ 874 ከክ.ል. ዐሥራ ሁለት ዓመት የነገሠ የዐሥሩ የእስራኤል ነገዶች ስድስተኛ ንጉሥ። አስቀድሞ የጦር ሠራዊት አለቃ ነበረ፤ 1ነገ. 16፥16:21-23። ሰማርያን መናገሻ ከተማው እንዲሆን አሠራ፤ 1ነገ. 16፥23:24። ክፉትንም ሠራ፤ 1ነገ. 16፥25-28፤ ሚክ. 6፥16። ልጁ አክዓብ፥ ከአክዓብም ልጆች ሁለቱ ከእርሱ በኋላ ነገሡ።

**ዘንዶ**፤ በበረሀ የሚኖር፥ እባብ የሚመስል ትልቅ አውሬ። በአ.ኪ. «ደራጎን» የሚለው የግሪክ ቃል በአማርኛ ዘንዶ ተብሎ ተተርጉሟል። ይህ ደራጎን በራእይ የሚታይ አስፈሪ አውሬና የሰይጣን ምሳሌ ነው፤ ራእ. 12፥3፤ 20፥2። በብ.ኪ. ዘንዶ የምድር ወይም የባሕር አውሬ ሊሆን ይችላል፤ መዝ. 91፥13፤ ኢሳ. 27፥1።

**ዘንግ**፤ 1. እንደ ሸንበቆ ያለ እንጨት። መለኪያ ሲሆን ርዝመቱ 2.7 ሜትር ያህል ነው፤ ሕዝ. 40፥5፤ ራእ. 21፥15:16። «ርዝመት» ይመ.። 2. የሥልጣንና የክብር በትር። «በትር» ይመ.

**ዘካርያ**፤ ከ753-752 ከክ.ል. የነገሠ የእስራኤል ንጉሥ፤ 2ነገ. 15፥8-10።

**ዘካርያስ**፤ ትርጉሙ «እግዚአብሔር ያስታውሳል» ማለት ነው። በብ.ኪ. በተለይ በ1ና በ2ዜና መዋዕል፥ በዕዝራና በነህምያ መጻሕፍት ከ20 በላይ የሚሆኑ ሰዎች በዚህ ስም ተጠርተዋል። ከብ.ኪ. ሁለት፥ ከአ.ኪ. አንድ በዚህ ስም ይጠሩ የነበሩትን መጥቀስ ያስፈልጋል።

1. የካህኑ ዮዳሄ ልጅ። በንጉሥ ኢዮአስ ትእዛዝ በእግዚአብሔር ቤት አደባባይ ውስጥ ተወገረ፤ 2ዜ.መ. 24፥20-22:25።

2. የበራክዩ ልጅ። በ520 ከክ.ል. ከነቢዩ ሐጌ ጋር ተነሥቶ የቤተ መቅደሱን ሥራ እንዲፈጽሙ አይሁድን አነሣሣቸው፤ ዕዝ. 5፥1። በማቴ. 23፥35 የተጠቀሰው የበራክዩ ልጅ ቢሆንም ነገሩ ስለ ዮዳሄ ልጅ መወገር ያሳስባል። ምናልባት አንድ የዱሮ ዘመን ጸሓፊ የአባት ስም ለውጦ ይሆናል፤ ሉቃ. 11፥51።

3. የመጥምቁ ዮሐንስ አባት። እንደ እግዚአብሔር ሕግ የሚኖር ጻድቅ ካህን ነበር። የገብርኤልን ቃል ባለማመኑ፥ ልጁ እስከተወለደ ድረስ ዲዳ ሆነ። የልጁን ስም ከጻፈ በኋላ መንፈስ ቅዱስ ሞላበትና እግዚአብሔርን አመሰገነ፤ ሉቃ. 1።

**የዘካርያስ ትንቢት**፤ «ዘካርያስ» 2. ይመ. አከፋፈል ፦

1. ወደ እግዚአብሔር ተመለሱ የሚል ጥሪ (1፥1-6)።

2. በስምንት ራእዮች፥ የምድር ሁሉ ጌታ እግዚአብሔር ጽዮንን ለመሥራትና ለማንጻት ያለውን አሳብ ይገልጣል (1፥7-6፥15)።

3. በኢየሩሳሌም መፍረስ ጊዜ የተደነገጉ የጾም ቀኖች ተለውጠው የደስታ በዓላት እንዲሆኑ የተሰጠ ትእዛዝ (ም. 7ና 8)።

4. እግዚአብሔር ለመፍረድም ሆነ ለማዳን ታላቅና ቅን ስለ መሆኑ (9)።

5. ስለማይረቡ እረኞች (አለቆች)ና ስለ መልካሙ እረኛ (10-13)።

6. እግዚአብሔር በምድር ሁሉ ላይ መንገሡ (14)።

ዘካርያስ ስለ ክርስቶስ ብዙ ጊዜ ትንቢት ተናግሯል፤ ከእነዚህም የታወቁት 6፥12:13፤ 9፥9፤ 11፥13፤ 12፥10፤ 13፥7 ናቸው።

**ዘውድ**፤ ንጉሥና ንግሥት የሚቀዳጁት ከሐር፥ ከወርቅ፥ ከዕንቍና ከከበረ ድንጋይ የሚሠራ የክብር አክሊል፤ 2ዜ.መ. 23፥11፤ ሕዝ. 21፥26፤ አስ. 2፥17፤ ራእ. 19፥12። ሥዕሉን በገጽ 214 ይመ.

**ዘይት**፤ ዘይት ከወይራ ፍሬ ይጨመቃል። ሰዎች ይህን ዓይነት ዘይት ለምግብ፥ ለልዩ ልዩ ቅባት፥ ለጠጉር፥ ለመድኃኒት፥ ለመብራት፥ ሰዎችንና ዕቃዎችን ለእግዚአብሔር አገልግሎት ለመለየት ይጠቀሙበት ነበር፤ 1ሳሙ. 10፥1፤ 1ነገ. 17፥2-16፤ ሉቃ. 10፥34፤ ያዕ. 5፥14። «ቀባ» ይመ.

**ዘዳግም**፤ 5ኛው የሙሴ መጽሐፍ። ይህ መጽሐፍ «ዘዳግም» ወይም «እሪት ዘዳግም» የተባለበት ምክንያት የእስራኤል ሕዝብ ወደ ከነዓን ሲቃረቡ ሙሴ እሪትን በድጋሚ ስላስታወቃቸው ነው። እስራኤላውያን ገና በሲና ተራራ ሳሉ እሪትን አንድ ጊዜ ሰምተው ነበር (ዘጸ.፤ ዘሌ.)፤ ይህ ግን ከ40 ዓመት በፊት ነበረ፤ ያን ጊዜ የሰሙት ሕዝብ ከካሌብና ከኢያሱ ዕድሜአቸውም ከ20 ዓመት ያነሰ ከሆነው በስተቀር ሁሉም በምድረ በዳ ሞተው ነበር፤ አሁንም በከነዓን አጠገብ ያሉት ሕዝብ አዲስ ትውልድ፥ እሪትን ያልሰሙ ናቸው። ስለዚህ በኢያሪኮ አንጻር በመሆን ዮርዳኖስን ተሻግረው ወደ ርስት አገራቸው ከመግባታቸው በፊት ሙሴ አሁን በናባው (በዓባሪ) ተራራ በሞዓብ አገር እሪትን በመድገም ቃል ኪዳኑ መታደሱን አሳወቀ። በዚህ መጽሐፍ የምናገኘው አሳብ ይህ ነው፤ 1፥3-5፤ 6፥1:2፤ 32፥48:49።

ሙሴ እንዲህ ብሎ ደጋግሞ ይመክራቸዋል ፦ «እግዚአብሔር ወደሚሰጣችሁ ምድር ገብታችሁ እንድትወርሷት እኔ የማስተምራችሁን ሥርዓት ስሙ፥ ጠብቁ» ቀጥሎም ፦ «እኔ ዛሬ የማዝዝህ ይህች ትእዛዝ ከባድ አይደለችም» ይልና «በፊትህ ዛሬ ሕይወትንና

ሞትን አኑሬአለሁ፤ እንግዲያውስ ሕይወትን ምረጥ» በሚል ቃል ያደፋፍራቸዋል፤ 30፥11-20። በም. 31 ሙሴ ስለ ሞቱ እንደተናገረና ኢያሱን በምትኩ እንደሾመ፥ ይህችን ሕግ እንደጻፈ፥ የሕጉን መጽሐፍ በቃል ኪዳኑ ታቦት ውስጥ ያስቀምጡት ዘንድ ካህናትን እንዳዘዛቸው እናነባለን። ም. 32-34 ከመሞቱ በፊት መዝሙሩን፥ ቡራኬውንና ሞቱን ይገልጣሉ፤ 31፥30፤ 33፥1። ሙሴ ነቢይ በመሆኑ አስቀድሞ ስለሞቱ ሊጽፍ ይችላል።

ካህኑ ኬልቅያስ በመቅደስ ያገኘውና ጸሓፊው ሰፋን በአደባባይ ቆሞ ለሕዝብ በይፋ ያነበበው፥ ክርስቶስም 3 ጊዜ በመጥቀስ ዲያብሎስን ያሸነፈበት ይህ መጽሐፍ ሳይሆን አይቀርም፤ 2ነገ. 22፥8፤ ነህ. 8፥1-3፤ ማቴ. 4፥4:7:10። «የኦሪት ጸሓፊ» ይመ.

አከፋፈል ፦

1. ም. 1-11። ማሳሰቢያ «ያለፈውን አስብ!»

2. ም. 12-26። ሕግ (ወይም ኦሪት) «ጠብቅ!»

3. ም. 27-34። ማስጠንቀቂያ «ወደፊት ተጠንቀቅ!»

**ዘጸአት**፤ 2ኛው የሙሴ መጽሐፍ። «ጸአት» ማለት መውጣት ማለት ነው። በዚህም መጽሐፍ ውስጥ ለእግዚአብሔር የተለዩት እስራኤላውያን ከግብጽ ባርነት ነፃ እንደወጡ፥ ወደ ከነዓንም እንደተጓዙ እናነባለን። ዮሴፍ ሞቷል፤ ዘመናትም አልፈዋል፤ ሌላ ንጉሥ አሁን ነግሦአል። በራብ ምክንያት ወደ ግብጽ የወረዱ የያዕቆብ ልጆች በቍጥራቸው በርክተዋል፤ ግብጻውያንም ተጸይፈዋቸዋል፤ ፈርተዋቸዋልም። «ቍጥራቸውን እንቀንሳለን» በማለት ፈርዖን ሕፃናት እንዲገደሉ እስራኤላውያንም በጽኑ ሥራ እንዲሠቃዩ አዘዘ (ም. 1)። በዚህ ጊዜ ሙሴ ተወለደ፤ እግዚአብሔርም በእርሱ እጅ እስራኤላውያንን ከግብጽ ለማውጣት ዐቀደ (2-4)።

ፈርዖን «አልለቃቸውም» ባለ ጊዜ እግዚአብሔር በአገሩ ላይ ልዩ ልዩ መቅሠፍት አወረደ። የግብጻውያን በኵር ልጆች ካለቁበት ከመጨረሻው መቅሠፍት የተነሣ ፈርዖን ለቀቃቸው (5-12)። ከግብጽ ሲወጡ የኤርትራን ባሕር ተሻገሩ፤ ወደ ሲና ተራራም ደረሱ፥ እዚያም እግዚአብሔር «ብሉይ» የተባለውን ኪዳን ሰጣቸው (13-24)። እግዚአብሔር ከሕዝቡ ጋር ሊገናኝ በመካከላቸውም ሊኖር ስለወደደ ማደሪያ የሚሆን መቅደስ እንዲሠራለት፥ በማደሪያውም በክህነት ያገለግሉ ዘንድ አሮንና ልጆቹ እንዲቀደሱ የክብር ልብስም እንዲሰፋላቸው አዘዘ (25-31)።

ሙሴ ከእግዚአብሔር ጋር ሲነጋገር በተራራው ላይ በመዘግየቱ እስራኤላውያን ትዕግሥት አጥተው ስላስገደዱት አሮን ከወርቅ የጥጃ ምስል ሠራላቸው። ሙሴ ሁለቱን የምስክር ጽላት ይዞ ከተራራው ሲወርድ የሕዝቡን ኃጢአት ተረዳና በንዴት ጽላቱን ከእጁ ወርውሮ ሰባበራቸው፤ እግዚአብሔርም «አብሬአችሁ አልወጣም» እስኪል ድረስ ተቈጣ። ሙሴ ግን ስለጸለየ እግዚአብሔር ራራላቸው። ሙሴንም ሁለተኛ ወደ ተራራው ጠራው። ሙሴ ወደ ተራራው በወጣ ጊዜ እግዚአብሔር ስሙን በፊቱ አወጀ። ኪዳኑንም እንደገና ጸፈለት (32-34)። በተከታዮቹም ምዕራፎች ልክ በተራራው ላይ በተገለጠው ምሳሌ ማደሪያው እንደተሠራ እናነባለን (35-40)። «የኦሪት ጸሓፊ» ይመ.

አከፋፈል ፦

1. እስራኤላውያን በምድረ ግብጽ፤ 1፥1-12፥36።

2. የእስራኤላውያን ጕዞ ወደ ሲና ተራራ፤ 12፥37-19፥2።

3. እስራኤላውያን በሲና ተራራ አካባቢ፤ 19፥3-40፥38።



ከግራ ወደ ቀኝ የግብጽ፥ የባቢሎንና የፋርስ ዘውዶች

**ዘፈን፤** በቅኔና በግጥም ከልዩ ልዩ መሣሪያ ጋር እየተቀነባበረ የሚቀርብ የደስታ ምልክት። ዘፈን ፦ 1. በልደት ቀን (ኢዮብ 21፥11:12፤ ማቴ. 14፥6)፥ 2. በሰርግ ቀን (ኤር. 31፥4፤ ማቴ. 11፥17)፥ 3. በድል በዓል ቀን (ዘጸ. 15፥20:21፤ መሳ. 11፥34፤ 1ሳሙ. 18፥6)፥ 4. በመንፈሳዊ በዓል ቀን (2ሳሙ. 6፥14) ይደረጋል። ከዚህም ሌላ በልዩ ልዩ የደስታ ቀን ይዘፈናል፤ ሉቃ. 15፥25። በእስራኤል የአምልኮት ሥርዓት ዘፈን (ማኅሌት) ትልቅ ቦታ ይይዝ ነበር፤ መዝ. 149፥3፤ 150፥4። ነገር ግን ባዕድ አምልኮትንና ዝሙትን የሚያስከትል ዘፈን አልተፈቀደም (ዘጸ. 32፥6:19፤ ማር. 6፥21:22)፤ ሐዋርያት ዘፈን የማይገባ መሆኑን ተናግረዋል፤ ሮም 13፥13፤ ገላ. 5፥21። በእስራኤል ዘንድ አብዛኛውን ጊዜ የሚዘፍኑ ሴቶች ነበሩ፥ ወንዶችም የዘፈኑበት ጊዜ ነበር፤ 2ሳሙ. 6፥14-16።



ግብጻውያን ዘፋኞች

**ዘፍጥረት፤** ይህ የመጽሐፍ ቅዱስ የመጀመሪያው መጽሐፍ ነው። «ዘፍጥረት» ከእርሱ ቀጥለው ለሚገኙት መጽሐፎች ሁሉ መሠረት ነው። ስለ ፍጥረትና የፍጥረት ሁሉ ፍጻሜ ስለሆነው ስለ ሰው ፍጥረት ይናገራል። እግዚአብሔር ሰውን በመልኩ እንደ ምሳሌው ሲፈጥር ሙሉ ነፃነት ይኖረው ዘንድ እንደወደደ፥ በነፃነቱም ይጠቀም ዘንድ ትእዛዝ እንደሰጠው መጽሐፉ ይነግረናል (ም. 1-2)። ሰው በነፃነቱ ተጠቅሞ የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ማፍረስ መረጠ፤ ይህንንም በማድረግ ኃጢአት፥ በኃጢአትም ሞት፥ ወደ ዓለም እንዲገባ አደረገ (3)።

ኃጢአት በዓለም ሁሉ ላይ ስለተሠራጨ የአዳም ልጅ ነፍሰ ገዳይ ሆነ፤ በኖኅም ዘመን የሰው ክፋት በምድር ላይ በዛ፤ 4፥1-6፥5። እግዚአብሔር የጥፋትን ውሃ አዘንሞ ከኖኅና ከልጆቹ በስተቀር የተፈጠረውን ሁሉ አጠፋ፤ 6፥6-9፥29። የኖኅ ልጆች ግን ከቀደሙት ሰዎች የተሻሉ ሳይሆኑ በእግዚአብሔር ላይ ዐመፁ፥ በዚህም ምክንያት እግዚአብሔር ለራሱ የሚሆነውን የተለየ ትውልድ ፈልጎ አብራምን ጠራ (10-12)።

ከም. 12 ጀምሮ እስከ ም. 23 ድረስ የአብራምን ታሪክ እናገኛለን፤ ቀጥሎም ስለ ልጆቹ ስለ እስማኤልና ስለ ይስሐቅ፥ ስለ ይስሐቅም ልጆች ስለ ዔሳውና የ12ቱ የእስራኤል ነገዶች አባት ስለሆነው ስለ ያዕቆብ እናነባለን (24-36)።

በመጽሐፉ መጨረሻ ላይ ስለ መልካሙ ሰው ስለ ዮሴፍ ስናነብ በራብ ምክንያት የያዕቆብ ልጆች ዮሴፍ ወደነበረበት ወደ ግብጽ አገር እንደወረዱ እንገነዘባለን፤ ወደ መጽሐፉ መጨረሻ ገደማ ልዩ የሆነውን የእግዚአብሔርን ሕዝብ በባዕድ አገር ተቀምጦ እናገኘዋለን፤ ዮሴፍንም ሲሞት እንመለከታለን (37-50)።

እንግዲያውስ በእግዚአብሔር መልክ እንደ ምሳሌው፥ በመፈጠሩ ጥንት ለዘለዓለም ነዋሪ የነበረው ሰው ሁሉ መልካሙም ሳይቀር ሁሉም አሁን ሟች እንደሆነ እንረዳለን። በዚህ ምክንያት ለሁሉም መድኅን አስፈላጊ ሆኗል። እግዚአብሔር ከመጀመሪያው ይህን ዐቅዶ እንደነበረ እንረዳለን፤ 3፥15፤ 1ጴጥ. 1፥18-21። «የኦሪት ጸሐፊ» ይመ.

**ዙፋን፤** የንጉሥ መንበር፤ ዘፍ. 41፥40፤ 1ነገ. 2፥19። ዙፋን ክብርን ሥልጣንንና መንግሥትን ያሳያል፤ 2ሳሙ. 3፥9:10፤ 7፥13-16።

የእስራኤል ንጉሥ በእግዚአብሔር ስለተሾመ፥ ዙፋኑ የእግዚአብሔር ዙፋን ተባለ፤ 1ዜ.መ. 28፥5። በምድር ያለ የንጉሥ ዙፋን የእግዚአብሔር ዙፋን ምሳሌ ነው (1ነገ. 22፥10:19)፥ ስለዚህም ንጉሥ በጽድቅ ሊነግሥ ይገባዋል፤ ምሳ. 16፥12፤ ኢሳ. 9፥7። የእግዚአብሔር ዙፋን በሰማይ ነው። በኪሩቤል ላይ እንደሚኖርም ተጽፏል፤ 1ሳሙ. 4፥4። እግዚአብሔር ከፍ ባለው ዙፋን ላይ እንዳለ ሆኖ ለነቢያት ተገልጧል፤ ኢሳ. 6፥1፤ ዳን. 7፥9። የዳዊት ዙፋን የክርስቶስ መንፈሳዊ ዙፋን ምሳሌ ነበረ፤ መዝ. 132፥11፤ ሐ.ሥ. 2፥29-31። ዳዊት የክርስቶስ ዙፋን ዘለዓለማዊ እንደሆነ ተናገረ፤ መዝ. 45፥6:7፤ ዕብ. 1፥8። ክርስቶስ በፍርድ ቀን በክብር ዙፋን ላይ ሆኖ ይፈርዳል (ማቴ. 25፥31፤ ራእ. 20፥11:12)፥ ዙፋን ክርስቶስን አምነው ለተከተሉ ሁሉ የመዳን ክብር ምሳሌ ነው፤ ማቴ. 19፥28፤ ራእ. 3፥21።



ጥንታዊ የግብጽ ዙፋን

**ዚፍ፤** «ወር» ይመ.

**ዛበረ፤** ከጽኑ ሕማም የተነሣ መጨነቅ፥ ማቃሰት፤ ኢዮብ 2፥9።

**ዛብሎን፤** ትርጒሙ «መኖሪያ» ማለት ነው። ልያ የወለደችለት የያዕቆብ ዐሥረኛ፥ የልያም ስድስተኛ ልጅ፤ ዘፍ. 30፥19:20፤ 35፥23። ከእስራኤል ነገዶች የአንዱ አባት ሆነ፥ በስሙም «ነገደ ዛብሎን» ተብሎ ተጠራ። በከነዓን የደረሰው የርስት ድርሻ ከንፍታሌም አጠገብ ሲሆን፥ በኋላ ገሊላ በተባለው ክፍለ አገር ነበረ፤ ኢያሱ 19፥10-16፤ ኢሳ. 9፥1:2፤ ማቴ. 4፥13-17። የዛብሎንና የንፍታሌም ሰዎች ለሰልፍ ባርቅን ተከተሉ፤ መሳ. 4፥6፤ 5፥18። ካ. 3ሀ። «ነገድ» ይመ.

**ዛንጅር፤** ወንጀለኛ የሚታሰርበት ወፍራም ሰንሰለት። እግርንም ሆነ እንገትን ለማሰር ያገለግላል፤ 2ዜ.መ. 33፥11፤ ኤር. 29፥26።

**ዛጒል፤** 1. በባሕር ውስጥ የሚኖር ፍጥረት፤ የላይ ልብሱ እንደ ድንጋይ የጠነከረ ነው። ዛጒል ሲቃጠል ኃይለኛ ሽታ ይሸታል፤ ዘጸ. 30፥34። 2. ሌላ ዓይነት በባሕር ውስጥ ይፈጠርና እንደ እንጀራ፥ እንደ ቍጥቋጦ ያለ ልዩ ልዩ ቅርጽ ያበጃል። ኀብሩ (ዓይነቱ) አብዛኛው ነጭና ቀይ ሆኖ የከበረ ጌጣጌጥ ይሠራበታል፤ ኢዮብ 28፥18፤ ሕዝ. 27፥16።

**ዜማ፤** የጨዋታ ስልት፥ የመዝሙር መሣሪያ ድምፅ፥ ሙዚቃ። ብዙ ጊዜ ዜማ ከልዩ ልዩ ዓይነት የዜማ ዕቃ ጋር ይስማማል። ዳዊትና ሌሎች ነገሥታት በእግዚአብሔር ቤት እንዲያዜሙ ሌዋውያንን አደራጁ፤ 1ዜ.መ. 6፥31:32፤ 2ዜ.መ. 29፥25:26፤ ነህ. 12፥46። ወንዶችና ሴቶች መዘምራን ነበሩ፤ ዕዝ. 2፥65። በአዲስ ኪዳንም ምእመናን በልዩ ልዩ ዓይነት መዝሙር እንዲጠቀሙ ታዘዙ፤ 1ቆሮ. 14፥26፤ ኤፌ. 5፥19፤ ቆላ. 3፥16።

**የዜማ ዕቃ፤** የልዩ ልዩ ድምፅ መስጫ፥ መዝሙር የሚዘመርበት። ከዮባል ጊዜ ጀምሮ የዜማ መሣሪያዎች ተገኝተዋል፤ ዘፍ. 4፥21። ለድል በዓል (ዘጸ. 15፥20፤ 2ዜ.መ. 20፥28)፥ በግብዣ (ዘፍ. 31፥27፤ ኢሳ. 5፥12) ይጠቀሙባቸው ነበር። እረኞችና ጕልማሳዎች በገና ይመቱ ነበር፤ 1ሳሙ. 16፥18፤ ሰ.ኤ. 5፥14። በሐዘን ጊዜም እምቢልተኞች ይገኙ ነበር፤ ማቴ. 9፥23። ዳዊት በብዙ ዓይነት የዜማ ዕቃ እግዚአብሔርን እንዲያመሰግኑ መዘምራንን አደራጀ፤ 1ዜ.መ. 15፥16። ናቡከደነፆር በብዙ ዓይነት የዜማ መሣሪያ ተጠቀመ፤ ዳን. 3፥15። በጥንት ጊዜ ሦስት ዓይነት የዜማ ዕቃ ነበረ።

1. አውታር ያለው ዕቃ። ዘማሪው በእጅ ወይም በመከርከሪያ ሲመታው ድምፅ ይሰጣል። በገና፥ ክራር፥ መሰንቆ ከባለ አውታር የዜማ ዕቃ ክፍል ናቸው።

2. የሚነፋ ዕቃ። በዚህ ዓይነት የዜማ ዕቃ ውስጥ መለከት፥ እምቢልታና ዋሽንት ተጠቅሰዋል።

3. ዕቃዎችን እርስ በርስ በማጋጠት ወይም በእጅ በኃይል በመምታት የሚጠቀሙባቸው ዕቃዎች። እነዚህም ከበሮ፥ አታሞ፥ ነጋሪት፥ ጸናጽል ናቸው።



**ዜና መዋዕል፤** የዕለታት ዜና ማለት ነው። ሁለቱ የዜና መዋዕል መጻሕፍት በጥንት ዘመን አንድ መጽሐፍ ብቻ ነበሩ፥ 70 ሊቃናት ከክርስቶስ በፊት 150 ዓመት ያህል መጽሐፉን ሲተረጕሙት ግን በሁለት ከፍለውታል። ሁለቱ የዜና መዋዕል መጻሕፍት በብዙ ረገድ የነገሥትን መጻሕፍት ይመስላሉ። በመጽሐፈ ነገሥት መጻሕፍት በየዘመኑ የነበሩ የእስራኤልና የይሁዳ ነገሥታት ታሪክ ይገኛል። በዜና መዋዕል ደግሞ ያ ታሪክ ይገኛል፤ ሆኖም አስተያየቱ ልዩ ነው። የዜና መዋዕልን መጻሕፍት የጻፈው ሰው ታሪኩን ያስፈረው ከመንፈሳዊ፥ ማለትም ሃይማኖት ነክ ከሆነ አስተያየት ጋር በማያያዝ ነው፥ በተለይ ስለ ቤተ መቅደስና ስለ ካህናት ይጽፋል። በዚህ ምክንያት ከይሁዳ መንግሥት ጋር ግንኙነት ያለው ካልሆነ በቀር፥ ስለ እስራኤል ብዙ አይጠቅስም። በትውልድ ቈጠራ ይጀምራል (1-9)፤ የሳኦልንም መሞት ተርኮ ወደ ዳዊት ይደርሳል (10)፤ እስከ 1ኛ ዜና መዋዕል መጨረሻ ድረስ ያለው የዳዊት ታሪክ ነው። ዳዊት ታቦቱን ወደ ከተማው እንዳስመጣው (13-16)፥ የእግዚአብሔርን ቤት መሥራት እንዳሰበና እንዳሰናዳ (22)፥ ሌዋውያንን ቈጥሮ ከመዘገበ በኋላ በየሥራቸው እንደ መደባቸው (23-26)፥ በሽመገለም ጊዜ ለልጁ ለሰሎሞን የቤቱን ምሳሌ በታላቅ አደራ እንደሰጠው ጸሐፊው ይተርካል (28፤ 29)።

በሁለተኛው መጽሐፍ ላይ ሰሎሞን፥ የእግዚአብሔርን ቤት እንደሠራ፥ በጸሎትም እንደቀደሳት፥ ስለ ግርማውና ስለ ንግሥተ ሳባ ጉብኝት እናነባለን (1-9)፤ በሚከተሉት ምዕራፎች እስከ መጨረሻው ማለት ከሮብዓም እስከ ይሁዳ ሕዝብ መማረክ፥ ከዚያም በላይ ወደ አገራቸው ይመለሱ ዘንድ የፋርስ ንጉሥ ቂሮስ አዋጅ እስካስነገረበት ጊዜ ድረስ ያለውን የይሁዳን ነገሥታት ታሪክ ይተርካል (10-36)።

ብዙ መምህራን «መጻሕፍቱን የጻፈው ካህኑ ዕዝራ ነው» ይላሉ፥ ይህም እውነት ይመስላል። ሆኖም የትውልድ ዝርዝሩ ከዕዝራ ዘመን በኋላ ያለውን ስለሚያመለክት ምናልባት ሌላ ሰው ጨምሮበት ይሆናል። ዘመኑ ከክርስቶስ በፊት 400 ዓመት ያህል ይሆናል። ጸሐፊውም ሲጽፍ የነገሥታት ታሪክ በተጻፈባቸው በሌሎች ጽሑፎች መጠቀሙ ታውቋል፤ 2ዜ.መ. 9፥29፤ 12፥15፤ 20፥34፤ 32፥32።

**ዜግነት**፤ የአገር ወይም የመንግሥት ሙሉ ባለመብት። የሮም ዜጎች ሳይፈረድባቸው አይታሰሩም አይገረፉምም ነበር፥ የሞት ፍርድ ሲፈረድባቸውም ራሳቸው ይቈረጥ ነበር እንጂ አይሰቀሉም ነበር፤ ሐ.ሥ. 16፥37-39፤ 22፥24-29። የክርስቲያን ዜግነት ሰማያዊ ነው፤ ኤፌ. 2፥19፤ ፊል. 3፥20።

**ዝሆን**፤ የዝሆን ጥርስ፤ ዛሬ በምድር ላይ ከሚኖሩት እንስሳት ትልቁ (ግዙፉ) ዝሆን ነው። ሀብታሞች በዝሆን ጥርስ ቤቶቻቸውን ያጌጡ፥ ምስሎችንና ዕቃዎችንም ይሠሩ ነበር። ነጋዴዎች ከልዩ ልዩ አገር ያመጡታል፤ 1ነገ. 10፥18:22፤ 22፥39፤ መዝ. 45፥8፤ አሞጽ 3፥15፤ 6፥4፤ ሕዝ. 27፥15።

**ዝሙት**፤ ከጋብቻ ውጭ የሚደረግ ማናቸውም ዓይነት የወሲብ ግንኙነት ዝሙት ይባላል። ይህም የተከለከለ ነው፤ 1ቆር. 6፥9:18። እንዲሁም ዝሙት እውነተኛ ያልሆነን አምልኮ ያመለክታል፤ ማር. 8፥38። «ምንዝር» ይመ.

**ዝማሬ**፤ ዝማሬ አብዛኛውን ጊዜ «መዝሙር» ከሚለው ቃል ጋር አንድ ነው፤ ዘጸ. 15፥2፤ መዝ. 33፥3፤ 40፥3፤ ኤፌ. 5፥19፤ ቆላ. 3፥16። እንደ ኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤ.ክ. ሥርዓት ከቅዳሴ ቍርባን በኋላ የሚዘመረው መዝሙር ዝማሬ ይባላል፤ ማቴ. 26፥30። እስራኤላውያን በባቢሎን ሳሉ ዝማሬ እንዲዘምሩ ቢጠየቁ አልዘመሩም፤ መዝ. 137፥3:4።

**ዝምታ**፤ የከባድ አሳብ ወይም የጭንቀት ምልክት፤ ዘሌ. 10፥1-3፤ ኢዮብ 2፥12-13፤ መዝ. 39፥2፤ መክ. 3፥7፤ ራእ. 8፥1። ክርስቶስ ሲከሰስ ዝም አለ፤ ማቴ. 27፥14፤ ማር. 15፥5፤ ሉቃ. 23፥9፤ ዮሐ. 19፥9፤ 1ጴጥ. 2፥22-23።

**ዝርግፍ**፤ የወርቅ ማርዳ። በአንገት ላይ የሚደረግ ጌጥ ነው፤ ዘፍ. 41፥42፤ ኤር. 2፥32።

**ዝባድ**፤ መልካም መዓዛ ያለው ሽቱ። ጥርኝ ከሚባል አውሬ አካል የሚገኝ ነው የሚሉ አሉ፤ መዝ. 45፥8።

**ዝና**፤ በአድራጎቱ አንድ ሰው ያለው ታዋቂነት፤ ዘኁ. 14፥15፤ ማቴ. 4፥24።

**ዝናብ (ዝናም)**፤ ከሙቀት የተነሣ ዳመና ከውቅያኖሶች ወደ ላይ ይወጣል፤ እንደገናም ዝናብ ሆኖ ወደ ታች ይፈሳል፤ ኢዮብ 26፥8፤ መዝ. 135፥7፤ መክ. 11፥3። በእስራኤል አገር ዝናብ ከጥቅምት እስከ ግንቦት ሊገኝ ይችላል። የፊተኛው ዝናብ በጥቅምትና በኅዳር፥ የኋለኛው ደግሞ በመጋቢትና በሚያዝያ ወር ላይ ይመጣል፤ ኤር. 5፥24፤ ያዕ. 5፥7። «ወር»፥ «ግብርና» ይመ.። የዝናብ ብዛት የእግዚአብሔርን በረከት፥ የዝናብ እጥረት ደግሞ የእግዚአብሔርን ቍጣ ይገልጣል፤ ዘዳ. 28፥9-12:15-24። ከነዓናውያን በአል የተባለውን ጣዖት የዝናብ አምላክ ነው ብለው ያመልኩት ነበር።

**ዝንጀሮ**፤ «እንስሳት» ይመ.

**ዝንጕርጕር**፤ ልብስ፤ በልዩ ልዩ ዓይነት ክር የተጠለፈ፥ በልዩ ልዩ ቀለም የተጌጠ ልብስ። በእስራኤልና በጐረቤቶችዋ በጣም ውድ ነበረ። ነገሥታት በተለይ ይለብሱት ነበር። የቤተ መቅደስ መጋረጃና የካህናት ልብስ ከዝንጕርጕር ጨርቅ እንዲሠራ፥ እግዚአብሔር ለሙሴ ትእዛዝ ሰጠ፤ ዘጸ. 28፥4-39፤ መሳ. 5፥30።

**ዝንጕርጕር ወፍ**፤ (ጣዎስ)፤ ጅራቱ አረንጓዴ ወርቅማ ዓይን መስሎ የሚብለጨለጭ፥ አንገቱና ራሱ ሰማያዊ የሆነ ወፍ። ከምሥራቅ ይመጣል፤ 1ነገ. 10፥22። «ወፎች» ይመ.

**ዝክር**፤ መታሰቢያ ማለት ነው፤ መዝ. 135፥13።

**ዝዪ (ዝዮ)**፤ አንገቱ ረጅም፥ ሣር የሚበላ፥ በውሃ ላይ የሚገኝ አሞራ፤ ዘሌ. 11፥16። «ወፎች» ይመ.

**ዝገት**፤ ብረት ረጥቦ ሲሰነብት የሚወጣበት ሽበት። በምሳሌነት ዝገት ክፋትን፥ ኃጢአትን ያመለክታል፤ ምሳ. 25፥4፤ 26፥23፤ ኢሳ. 1፥22:25፤ ማቴ. 6፥19:20፤ ያዕ. 5፥3።

**ዝግባ**፤ በቤት ሥራና በምሳሌነት የታወቀ ዛፍ፤ 1ነገ. 4፥33። «ሊባኖስ» ይመ.

**ዝግጅት**፤ ሰው ለሚመጣው ነገር ሁሉ ራሱን ለማዘጋጀት እርምጃ ሲወስድ (አሞጽ 4፥12፤ ኤፌ. 2፥10፤ 6፥14-15፤ 2ጢሞ. 2፥21፤ 1ጴጥ. 3፥15)፥ ለክርስቶስ መገለጥ (ማቴ. 3፥3፤ ዕብ. 10፥5)፥ ለዳግም ምጽአቱ እግዚአብሔር ሁሉንም ያዘጋጃል፤ ማቴ. 25፥34:41፤ ዮሐ. 14፥2፤ ራእ. 21፥2።

**ዝፍት**፤ «ቅጥራን» ይመ.

**ዞጲ**፤ ጥንካሬ ያለው የዛፍ ዓይነት፤ ሕዝ. 27፥15።

**የሆዋ**፤ ያህዌ ማለት ነው። «እግዚአብሔር» ይመ.

**የብስ**፤ ደረቅ መሬት። በጥንት ፍጥረት ዓለም በውሃ የተሸፈነ ነበር። እግዚአብሔር ውሃው በአንድነት እንዲሰበሰብ ካደረገ በኋላ ውሃ ያለበትን ክፍል ባሕር አለው፤ ውሃ የሌለበትን ደግሞ የብስ አለው። እንደ ገናም የብሱን ምድር ብሎ ጠራው፤ ዘፍ. 1፥9:10።

**የቦ**፤ የጦር ዛቢያ፤ 1ሳሙ. 17፥7።

**የተሻለ**፤ ቃሉ ከሁለት ሁኔታዎች መካከል ብልጫ ያለውን ያሳያል (ዘፍ. 29፥19፤ መክ. 4፥9፤ 7፥1-10)፥ በተለይም ከብሉይ ኪዳን አዲስ ኪዳን ብልጫ እንዳለው ያመለክታል፤ ዕብ. 7፥18:19:22፤ 8፥6።

**የውሃት**፤ ራስን ዝቅ ማድረግ፥ አለመመካት፥ እሺ ባይነት፥ ከራስ ይልቅ ለባልንጀራ ማሰብ፤ ዘፍ. 13፥5-9። ክርስቶስ የዋህ እንደሆነ (ማቴ. 11፥29፤ 2ቆሮ. 10፥1)፥ ለአማኞች ደግሞ የውሃት ተገቢ ነው፤ ኤፌ. 4፥2፤ ቆላ. 3፥12፤ ቲቶ 3፥2። የውሃት የመንፈስ ቅዱስ ፍሬ ነው፤ ገላ. 5፥23። ኢየሱስ በተራራው ስብከቱ ለየዋሆች ታላቅ ተስፋ ሰጠ፤ ማቴ. 5፥5።

**የውጣ**፤ በጥንታዊው ግሪክ ቋንቋ ዐሥረኛ፥ በዘመናዊው ግሪክ ዘጠነኛ ፊደል የውጣ ይባላል። በዕብራይስጥም ዐሥረኛው ፊደል ዮድ እንደ የውጣ ነው። በአጻጻፍ ትንሽና ቀጭን ነው። ስለዚህ ኢየሱስ «ከሕግ አንዲቱ ምንም ትንሽ ብትሆን አትሻርም» አለ፤ ማቴ. 5፥17:18። «ግሪክ» ይመ.

**ያህዌ**፤ የእግዚአብሔር ስም። «እግዚአብሔር» ይመ.

**ያሱብ**፤ «ያሱብ» በዕብራይስጥ «ሸአር ያሹብ» ነው። ትርጓሜውም «ቅሬታ ይመለሳል» ማለት ነው። የኢሳይያስ ልጅ ነው። እስራኤላውያን ምንም እንኳን ቢማረኩም፥ ቅሬታቸው ከምርኮው አገር እንደሚመለሱ በዚህ ልጅ ስም ተገለጠ፤ ኢሳ. 1፥9፤ 7፥3፤ 8፥18።

**ያሻር መጽሐፍ**፤ በዚህ መጽሐፍ ልዩ ልዩ የእስራኤል ታሪክ መዝሙርና ቅኔ የተጻፈ ይመስላል፤ ኢያሱ 10፥13፤ 2ሳሙ. 1፥18። ይህ መጽሐፍና የጦርነት መጽሐፍ አንድ ይሆን ይሆናል፤ ዘኍ. 21፥14። መጽሐፉ በሰሎሞን ዘመን የተጻፈ ይመስላል፤ በኋላ ግን ጠፋ።

**ያቦቅ**፤ ከምሥራቅ ወደ ዮርዳኖስ የሚፈስ ወንዝ። ያዕቆብ ይህን ወንዝ ተሻግሮ ሄዷል። በሙሴ ዘመን የሲዖንና የአሞን መንግሥታት ዳርቻ ነበረ፤ ዘፍ. 32፥22፤ ዘኍ. 21፥21-24፤ ኢያሱ 12፥2። ካ. 3 ሸ።

**ያክንት**፤ ሰማያዊ ቀለም ያለው የከበረ ድንጋይ፤ ራእ. 21፥20።

**ያዕቆብ**፤ ትርጕሙ «ተረከዝን ይይዛል» ማለት ነው። 1. ርብቃ ለይስሐቅ ከወለደችለት መንታዎች ታናሹ የዐሥራ ሁለቱ የእስራኤል ሕዝብ ነገዶች አባት። ከልደቱ በፊት መመረጡ ተገለጠ፤ የወንድሙን ተረከዝ ይዞ ተወለደ፤ ዘፍ. 25፥19-26። ብኵርናውን ገዛ፤ ዘፍ. 25፥27-34። አባቱን በማታለል በረከትን አገኘ፤ ዘፍ. 27። ከዔሳው ለማምለጥ፥ ሚስት ለማግኘት ወደ እናቱ ወንድም ወደ ላባ ሄደ፤ ዘፍ.27፥42-28፥9። የመሰላልን ሕልም አየ፤ የአብርሃምም ተስፋ ተሰጠው፤ ዘፍ. 28፥10-22። ሃያ ዓመት ላባን አገልግሎ ልያንና ራሔልን አገባ፥ ብዙ ልጆችንም ወለደ፥ ብዙ ከብትም አገኘ፤ ዘፍ. 29-30። እግዚአብሔር ወደ ከነዓን እንዲመለስ ባዘዘው ጊዜ ከላባ ቍጣ (ዘፍ. 31)፥ ከዔሳውም ቍጣ (ዘፍ. 32-33) ጠበቀው። እግዚአብሔር በጵኒኤል (ዘፍ. 32፥22-32)፥ በቤቴልም (ዘፍ. 35፥9-15) ተገለጠለት፤ ስሙንም «እስራኤል» ብሎ ጠራው። ብዙ ዓመት በከነዓን ከኖረ በኋላ (ዘፍ. 33፥18-45፥28) በረሃብ ጊዜ ወደ ግብጽ ሄደ፤ ዘፍ. 46-47። ትንቢት እየተናገረ የዮሴፍን ልጆች፥ የራሱንም ዐሥራ ሁለት ልጆች ከባረከ በኋላ 147 ዓመት ሲሆነው ሞተ (ዘፍ. 47፥27-49፥33)፤ በአብርሃምም መቃብር ተቀበረ፤ ዘፍ. 50። ከእርሱ የተገኘው ሕዝብ ፦ እስራኤል፥ አንዳንዴም «ያዕቆብ» ይባላል፤ ዘኍ. 23፥10፤ ኢሳ. 41፥8:14:21። ስለ መመረጡ (ሮም 9፥10-16)፥ ስለ እምነቱም (ዕብ. 11፥9:21) ተጠቅሷል።

2. የዘብዴዎስ ልጅ፥ የዮሐንስ ታላቅ ወንድም፥ ከሐዋርያት አንዱ፤ ማቴ. 10፥2። ጌታ የኢያኢሮስን ልጅ ሲያስነሣ፥ በተራራ ላይ ክብሩን ሲገልጥ፥ በጌቴሴማኒም ሲጸልይ ከጴጥሮስና ከዮሐንስ ጋር አብሮ ነበር፤ ማር. 5፥35-43፤ 9፥2-8፤ 14፥33-42። ኃይለኛና ቍጡ ከመሆኑ የተነሣ «ቦአኔርጌስ» ተብሎ ተሰይሟል (ማር. 3፥17)፤ ይህም ጠባዩ እሳት ከሰማይ ወርዶ ሰዎችን እንዲያጠፋቸው በጠየቀ ጊዜ ተገልጧል፤ ሉቃ. 9፥52-56። በሐዋርያት መካከል ከፍተኛ ማዕርግ እንዲሰጠው ፈልጎ ነበር፤ ማር. 10፥35-45። በመጨረሻ ሄሮድስ በሰይፍ አስገደለው፤ ሐ.ሥ. 12፥2። «ሐዋርያት» ይመ.

3. የእልፍዮስ ልጅ፥ ከሐዋርያት አንዱ። አንዳንድ ጊዜ ታናሹ ያዕቆብ ይባላል፤ ማቴ. 10፥3፤ ማር. 15፥40። «ሐዋርያ» ይመ.

4. የሐዋርያው የይሁዳ አባት፤ ሉቃ. 6፥16፤ ሐ.ሥ. 1፥13።

5. የጌታ ወንድም፤ ማቴ. 13፥55፤ «የጌታችን ወንድሞች» ይመ.። እስከ ትንሣኤ ድረስ በጌታ አላመነም፤ ዮሐ. 7፥5። ነገር ግን ከትንሣኤ በኋላ ጌታን አይቶ አምኗል፤ 1ቆሮ. 15፥7። በኢየሩሳሌም ለነበረችው ቤ.ክ. ከጴጥሮስ ቀጥሎ ዋና መሪ ሆነ፤ በኢየሩሳሌም ጉባኤ (ሲኖዶስ) ሊቀ መንበር ነበረ፤ ሐ.ሥ. 12፥17፤ 15፥13-21፤ 21፥18፤ ገላ. 1፥19፤ 2፥9-12። በ62 ዓ.ም. በኢየሩሳሌም በሰማዕትነት እንደሞተ ይተረካል።

**የያዕቆብ መልእክት**፤ ይህ መልእክት «የኢየሱስ ወንድሞች» ከተባሉት በአንዱ በያዕቆብ ተጻፈ። ያዕቆብ ይህን መልእክት የጻፈው ተበትነው

ለነበሩት፥ አሁን ግን ክርስትናን ለተቀበሉት አይሁድ ነው። የመልእክቱ የመጀመሪያ አንባቢዎች በመከራ ላይ ናቸው፤ በማኅበራቸውም ውስጥ ልዩ ስሕተት ገብቷል። ስለዚህ ያዕቆብ የሚጽፈው በመከራቸው ሊያጽናናቸውና ስሕተታቸውን ሊያርም ነው። መልእክቱ በ50 ዓ.ም. ገደማ ሳይጻፍ አልቀረም። የዚህ መልእክት ልዩ ይዘቶች የሚከተሉት ናቸው ፦

ሀ) አጻጻፉ እንደ ጳውሎስ መልእክቶች ለግሪክ ሰዎች ሳይሆን ለአይሁድ የሚስማማ አጻጻፍ ነው። አቀራረቡም እንደ ተራራው ስብከት ነው። 2፥5ን ከማቴ. 5፥3፤ 3፥10-12ን ከማቴ. 7፥15-20፤ 3፥18ን ከማቴ. 5፥9፤ 5፥2-3ን ከማቴ. 6፥19-20፤ 5፥12ን ከማቴ. 5፥33-37 ጋር ያስተያዩ። ትምህርቱ በአብርሃም፥ በረዓብ፥ በኢዮብና በኤልያስ ታሪኮች ተመርኩዞ ተብራርቷል።

ለ) ትምህርቱ በታላላቅ የትምህርተ መለኮት እውነቶች ላይ ሳይሆን በክርስቲያናዊ ኑሮ ጉዳታዎች፥ በትዕግሥ፥ በፈተና፥ አድልዎ ባለማድረግ፥ እንደበትን በመግታት፥ ጭቅጭቅንና ጠራትን፥ ሐሜትንም ትምክህትንም በማስወገድ፥ በትዕግሥት፥ በጸሎት ... ወዘተ ላይ ያተኩራል።

ሐ) ስለ እውነተኛ እምነት፤ 2፥14-26። አብርሃም በእምነቱ እንደጸደቀ ሲጠቅስ (2፥23)፥ እምነት ያለ ሥራ የሞተ መሆኑንና ሥራ (ምግባር) ሲታይበት ግን እውነተኛ እንደሆነ ያሳያል። ስለዚህ ሰው በእግዚአብሔር ፊት በእምነት ይጸድቃል፤ መጽደቁ ለሰዎች የሚታወቀው እምነቱ በሥራው ሲፈጸም ነው።

አከፋፈል ፦

1. እግዚአብሔር በመከራ ሳሉ ያጽናናቸዋል፤ ም.1።

2. ልዩ ልዩ ስሕተትን ያርማል፤ ም. 2-4።

3. ለትዕግሥትና ለጸሎት ያነሣሣቸዋል፤ ም. 5።

**ያፌት**፤ከኖኅ ልጆች አንዱ፤ ዘፍ. 5፥32፤ 6፥10። ከጥፋት ውሃ ዳነ፤ ዘፍ. 7፥13፤ 9፥18። የአባቱን ዕራቁትነት ሸፈነ፤ ዘፍ. 9፥20-24። አባቱም ስለ እርሱ ትንቢት ተናገረ፤ ዘፍ. 9፥27። ሰባት ልጆችን በመውለዱ የብዙ ሕዝብ አባት ሆነ፤ ዘፍ. 10፥2-5።

**ይሁዲነት**፤ «አይሁዳዊነት» የእስራኤል ሰዎች ሃይማኖት። ከአሕዛብ ወገን ተገርዘው ወደ ይሁዲነት የገቡ የሙሴን ሕግ በመቀበልና በመከታተል እንደ አይሁድ ይቈጠሩ ነበር፤ ማቴ. 23፥15፤ ሐ.ሥ. 2፥10፤ 6፥5፤ 13፥43።

**ይሁዳ**፤ ስሙ «ማመስገን» ከሚል ግሥ የተመሠረተ ነው። ልያ ለያዕቆብ የወለደችለት አራተኛ ልጅ፤ ዘፍ. 29፥35። ዮሴፍን እንሽጠው እንጂ አንግደለው አለ፤ ዘፍ. 37፥26:27። በወንድሞቹ መካከል መሪ ነበረ፤ ዘፍ. 43፥3-10፤ 44፥16-34፤ 46፥28። የቤተሰቡ ሁናቴ የሚያስነውር ነበር፤ ዘፍ. 38፤ ነገር ግን ትዕማር የወለደችለት ፋሬስ በኢየሱስ ክርስቶስ ትውልድ ሐረግ ተቈጥሯል፤ ማቴ. 1፥3። ይሁዳ ከእስራኤል ነገዶች የአንዱ አባት ሆነ፤ በስሙም ነገደ ይሁዳ ተብሎ ተጠራ። ያዕቆብ ይሁዳን በአንበሳ መስሎ አለቅነት ከይሁዳ እንደሚሆን አሕዛብ የሚታዘዙለትም ገዥ ከይሁዳ እንደሚመጣ ተነበየ፤ ዘፍ. 49፥8-12፤ ዕብ. 7፥14፤ ራእ. 5፥5። በምድረ በዳ ጕዞ የይሁዳ ነገድ ይቀድም ነበር፤ ዘኍ. 10፥14። በከነዓን ከዮርዳኖስ በስተምዕራብ በመጀመሪያ የተሰጠው የርስት ክፍል የይሁዳ ነገድ ክፍል ነበረ፤ ኢያሱ 15። ከ. 3በ። ንጉሥ ዳዊት ከይሁዳ ነገድ ተወለደ፤ ሩት 4፥12:18-22። የይሁዳ ነገድ ዳዊትን ካነገሡት ጊዜ ጀምሮ (2ሳሙ. 2፥4)፥ ለእርሱና ለልጅ ልጆቹ ተገዙ እንጂ ከሌሎች ነገዶች ጋር አላመፁም፤ 1ነገ. 12፥17። የዳዊት ቤት ነገሥታት የነገሡበት መንግሥት «ይሁዳ» ተባለ (ለምሳሌ አሞጽ 1፥1፤ 2፥4:5)። ክርስቶስ ከይሁዳ ወገን ተወለደ፤ ራእ. 5፥5። «አይሁድ»፥ «ነገድ» ይመ.

**ይሁዳ**፤ በአ.ኪ. በዚህ ስም ብዙ ሰዎች ተጠርተዋል፤ ከእነርሱም የታወቁት የሚከተሉት ናቸው ፦

1. ጌታችንን አሳልፎ የሰጠው ከሐዋርያት አንዱ የነበረው የአስቆሮቱ ይሁዳ፤ ማቴ. 10፥4። አስቆሮት በይሁዳ አውራጃ የሚገኝ ቂርያትሐጾር የሚባለው መንደር ይሆናል፤ ኢያሱ 15፥25። የሐዋርያት ገንዘብ ያዥ ሆኖ ሳለ ለራሱ ገንዘብ ይሰርቅ ነበር። ገንዘብም ስለወደደ፥ ክርስቶስን አሳልፎ ለመስጠት በ30 ብር ተስማማ፤ ማቴ. 26፥6-16፤ ዮሐ. 12፥6። ክርስቶስ ብዙ ጊዜ አስጠንቀቀው። እርሱ ግን ቃሉን አልተቀበለምና ሰይጣን ገባበት፤ ማቴ. 26፥20-25፤ ዮሐ. 13፥2:21-30። በመሳም ምልክት ኢየሱስን አስያዘ፤ ማቴ. 27፥47-50፤ ሉቃ. 22፥47:48። በኋላም አዘነ፤ ገንዘቡንም መለሰ። በመጨረሻ ራሱ ታንቆ ሞተ፤ ማቴ. 27፥3-5፤ ሐ.ሥ. 1፥15-19። በእርግጥ የጥፋት ልጅ ነበረ፤ ዮሐ. 17፥12።

2. የያዕቆብ ልጅ ከሐዋርያት አንዱ፤ ሉቃ. 6፥16፤ ዮሐ. 14፥22፤ ሐ.ሥ. 1፥13። ይህኛው ይሁዳ ታዴዎስ የተባለው ልብድዮስ ሳይሆን አይቀርም፤ ማቴ. 10፥3። «ሐዋርያ» ይመ.

3. በ6 ዓ.ም. በሮማውያን ላይ ያመፀና የተገደለ (የገሊላው ይሁዳ፤ ሐ.ሥ. 5፥37)።

4. ጳውሎስን በቤቱ ያስተናገደ የደማስቆ ሰው፤ ሐ.ሥ. 9፥11።

5. የኢየሩሳሌምን የጉባኤ ውሳኔ ለማስተላለፍ የተመረጠ በርስያን የተባለው ይሁዳ፤ ሐ.ሥ. 15፥22-33።

6. የጌታ ወንድም የሚባለው የያዕቆብ ወንድም ይሁዳ፤ ማቴ. 13፥55፤ ይሁዳ 1። «የጌታችን ወንድሞች» ይመ.

**የይሁዳ መልእክት**፤ እንደ ያዕቆብ ይሁዳ «የኢየሱስ ወንድሞች» ከተባሉት አንዱ ነው፤ ማቴ. 13፥55። የመልእክቱ ተቀባዮች የኖሩበት ስፍራ ባይታወቅም ምእመናን ነበሩ፤ ቍ. 1። ጴጥሮስ በ2ኛው መልእክቱ እንዳደረገው ሁሉ፥ ይሁዳም ሐሰትን ከሚያስተምሩት ሰዎች አንባቢዎቹን

ለማስጠንቀቅ ጽፏል፤ ቍ. 3። መልእክቱ በ65 ዓ.ም. ገደማ ሳይጻፍ አልቀረም።

ሲያስጠነቅቃቸውም ትምህርቱን ለማብራራት ከልዩ ልዩ የብ.ኪ. መጻሕፍት፥ ደግሞም ከብ.ኪ. 2ኛ ቀኖና መጻሕፍት፥ ማለትም ከ«መጽሐፈ ሄኖክ»፥ እንደዚሁም ከትውፊታዊ መጽሐፍ ይጠቅሳል፤ ቍ. 9:14። ጳውሎስም ቢያንስ ሦስት ጊዜ ከብ.ኪ. ውጭ ከሆኑት መጻሕፍት ጠቅሷል፤ ሐ.ሥ. 17፥28፤ 2ጢሞ. 3፥8፤ ቲቶ 1፥12።

አከፋፈል ፦

1. ሰላምታ፤ 1-2።
2. የመልእክቱ ምክንያት፤ 3-4።
3. የሐሰተኞች ፍርድ በብ.ኪ. ዘመን፤ 5-7።
4. የአሁኑ ዘመን ሐሰተኞች ክፋትና ፍርድ፤ 8-16።
5. ለምእመናን ማበረታቻና ቡራኬ፤ 17-25።

**ይሁዳ፤** በደቡብ ከነዓን ያለ አገር። የእስራኤል ልጆች ከባቢሎን ምርኮ ተመልሰው ወደ አገራቸው ሲመጡ አብዛኞቹ ከይሁዳ ወገን ስለሆኑ፥ በከነዓን የተቀመጡበት ስፍራ ይሁዳ ተብሎ ተሰየመ፤ ሰዎቹም አይሁድ ተባሉ፤ ዕዝ. 5፥8። በዚያ ጊዜ ይሁዳ የፋርስ መንግሥት ክፍል አገር ነበረ። በሮም ዘመን መንግሥት ለሶርያ ገዥ እንዲሆን በሮም የተሾመው የይሁዳ ገዥ በቂሣርያ ከተማ ይኖር ነበር። በክርስቶስ ዘመን ገዥው ጲላጦስ ነበረ፤ ሉቃ. 3፥1። ይሁዳ ከታላቁ ባሕር እስከ ጨው ባሕር፥ ከኢያሪኮ ከተማ እስከ ጋዛ ይደርሳል። ካሬ በእስራኤል ውስጥ ነው። ካ. 3 በ።

**የይሁዳ መንግሥት፤** ሰሎሞን ከሞተ በኋላ ኢዮርብዓም ዐሥሩን የእስራኤል ነገዶች አስከትሎ በሰሎሞን ልጅ በሮብዓም ላይ ዐመፀ፤ ሮብዓም ይሁዳን ብቻ ያዘ። መንግሥቱም ይሁዳ ተባለ። በእስራኤልና በይሁዳ መንግሥታት መካከል ብዙ ጊዜ ጦርነት ይደረግ ነበር። ሆኖም አንዱ መንግሥት ሌላውን ለማሸነፍ ስላልቻለ፥ ሁለት መንግሥታት ሆኑ። የይሁዳ ነገሥታት ብዙ ጊዜ ባዕድ አምልኮትን ተከተሉ። ደግሞም ተስፋቸውን በእግዚአብሔር ላይ በማድረግ ፈንታ በግብጽና በሌላም የውጭ እርዳታ በመተማመን እግዚአብሔርን አስቈጡት። እግዚአብሔርም ብዙ ነቢያትን ላከላቸው። አንዳንድ ነገሥታት ባዕድ አምልኮትን ለማስወገድ፥ ሕዝቡን ወደ እውነት ለመመለስ ሞከሩ። ከእነርሱም መካከል ሕዝቅያስና ኢዮስያስ የታወቁ ናቸው። ነገሥታቱና ሕዝቡ ከእግዚአብሔር እየራቁ ሄዱ። የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደነፆር እነዳንኤልን ወደ ባቢሎን ከወሰደ በኋላ ተመልሶ ዮአኪንንና ሌሎችን፥ ማለትም እነሕዝቅኤልን ማረከ። በመጨረሻም ናቡከደነፆር ኢየሩሳሌምን አፈረሰ፤ ሴዴቅያስንና ሌሎችን ወደ ባቢሎን አፈለሰ።

ሕዝቡ ከምርኮ ከተመለሱ በኋላ አንዳንዴ እስራኤል፥ አንዳንድ ጊዜ ደግሞ አገሩም ይሁዳ፥ ሕዝቡም አይሁድ ተባሉ። «የእስራኤል መንግሥት» ይመ.። በሰንጠረዡ የእስራኤልና የይሁዳ ነገሥታት፥ ነቢያታቸውና ጠላቶቻቸውም ተዘርዝረዋል። በቅንፍ ውስጥ ነገሥታት የነገሡበት፥ ነቢያት ትንቢት የተናገሩበት ዓመት ተጽፏል። አንዳንድ ጊዜ የዘመኑ ልክ በግምት ተጽፏል፤ «የብሉይ ኪዳን ስፍረ ዘመን» ይመ.። በቅንፍ ውስጥ «እ» ማለት በእስራኤል መንግሥት ተነበየ ማለት ነው።

**ይሳኮር፤** ትርጕሙ «ዋጋዬ» ማለት ነው። ልያ ለራሔል እንኮይ በመስጠት ያዕቆብን ተከራይታ የወለደችለት የያዕቆብ ዘጠነኛ፥ የልያም አምስተኛ ልጅ፤ ዘፍ. 30፥16-18፤ 35፥23። ከእስራኤል ነገዶች የአንዱ አባት ሆነ፤ በስሙም ነገደ ይሳኮር ተብሎ ተጠራ። ያዕቆብ ጠንካራ ሠራተኛነቱን በመመልከት በአህያ መሰለው፤ ዘፍ. 49፥14:15። በከነዓን የደረሰው የርስት ድርሻ ከገሊላም በስተደቡብ ነበረ። ካ. 3ሠ። አለቆቹም ዲቦራን ደገፉአት፤ መሳ. 5፥15። «ነገድ» ይመ.



የይሁዳ ሰዎች ከለኪሶ ሲማረኩ፤ በሰናክሬም ቤተ መንግሥት በነነዌ ከተገኘ ቅርጽ የተገለበጠ

| የይሁዳ ነገሥታት | ነቢያት | የእስራኤል ነገሥታት | ሌሎች መንግሥታት |
|---|---|---|---|
| ሮብዓም (931-913) | አኪያ (አ. 935-915) | ኢዮርብዓም 1ኛ (931-910) | <u>የሶርያ መንግሥት</u> |
| አቢያም (913-911) | | ናዳብ (910-909) | (በግብጽ ሺሻቅ) |
| አሳ (911-870) | ኢዩ (አ. 900) | ባኦስ (909-886) | ወልደ አዴር 1ኛ |
| | | ኤላ (886-885) | |
| | | ዘምሬ (885) | |
| | | ታምኒ (885-880) | |
| | | ዘንበሪ (885-874) | |
| ኢዮሣፍጥ (870-848) | ኤልያስ (አ. 865-853) | አክዓብ (874-853) | ወልደ አዴር 2ኛ |
| | | አካዝያስ (853-852) | |
| ኢዮራም (848-841) | ኤልሳዕ (አ. 852-798) | ኢዮራም (852-841) | |
| ጎቶልያ (841-835) | አብድዩ (840) | ኢዩ (841-814) | |
| ኢዮአስ (835-796) | ኢዩኤል (810) | ኢዮአካዝ (814-798) | አዛሄል |
| አሜስያስ (796-787) | | ዮአስ (798-782) | ወልደ አዴር 3ኛ |
| ዓዛርያስ (ዖዝያን) (787-740) | ዮናስ (770) | ኢዮርብዓም 2ኛ (782-753) | |
| | አሞጽ (አ. 760) | | |
| | ሆሴዕ (አ. 750) | ዘካርያ (753-752) | |
| | ኢሳይያስ (740-688) | ሰሎም (752) | |
| | ሚክያስ (735-688) | ምናሄም (752-742) | ረአሶን |
| | | ፋቂስያስ (742-740) | የደማስቆ ውድቀት (732) |
| ኢዮአታም (740-732) | | ፋቁሔ (740-732) | |
| አካዝ (732-716) | | ሆሴዕ (732-722) | <u>የአሦር መንግሥት</u> |
| ሕዝቅያስ (716-687) | | <u>722 የእስራኤል ምርኮ</u> | ስልምናሶር÷ሳርጎን ሰናክሬም |
| ምናሴ (687-642) | | | |
| አሞን (642-640) | | | (የኢትዮጵያ ቲርሐቅ) አሶራዶን |
| ኢዮስያስ (640-609) | ኤርምያስ (626-585) | | |
| | ሶፎንያስ (620) | | |
| | ናሆም (612) | | የነነዌ ውድቀት (612) |
| ኢዮአክስ (609) | ዕንባቆም (600) | | (በግብጽ ኒካው) <u>የባቢሎን መንግሥት</u> |
| ኢዮአቄም (609-597) | | | |
| ዮአኪን (597) | | | ናቡከደነፆር |
| ሴዴቅያስ (597-587) | ሕዝቅኤል (592-570) | | ብልጣሶር |
| <u>587 የይሁዳ ምርኮ</u> | ዳንኤል (556-538) | | የባቢሎን ውድቀት |
| የቂሮስ አዋጅ (538) | | | <u>የፋርስ መንግሥት</u> |
| ዘሩባቤል (537- 516) | ሐጌ÷ዘካርያስ (520) | | ዳርዮስ ÷ ቂሮስ |
| | ሚልክያስ (425) | | |

**ይስሐቅ**፤ ትርጉሙ «ይስቃል» ማለት ነው። የአብርሃምና የሣራ ልጅ፥ የያዕቆብ አባት። ሣራ በእርጅናዋ ወለደችው፤ ዘፍ. 17፥15-21፤ 18፥9-15፤ 21፥1-7። ከመወለዱ 25 ዓመት ቀደም ብሎ ለአብርሃም የተሰጠው የዘር ተስፋ በይስሐቅ ሊፈጸም ጀመረ፤ ዘፍ. 12፥1-3፤ ማቴ. 1፥2፤ ገላ. 3፥16። ይስሐቅ ተገረዘ፤ ዘፍ. 21፥4። «በይስሐቅ ዘር ይጠራልሃል» ስለተባለ፥ እስማኤል ተሰደደ፤ ዘፍ. 21፥8-14። አብርሃም ይስሐቅን ለመሥዋዕትነት አቀረበ፤ ዘፍ. 22። ይስሐቅ ርብቃን አገባ፤ ዘፍ. 24። ከጸለየም በኋላ ዔሳውንና ያዕቆብን ወለደችለት፤ ዘፍ. 25፥19-26። በዘመኑ ራብ በሆነ ጊዜ ወደ ፍልስጥኤም ተሰደደ፤ እግዚአብሔርም ወደ ግብጽ አትውረድ አለው፤ ዘፍ. 26፥1:2። እግዚአብሔር የአብርሃምን ተስፋ አጸናለት (ዘፍ. 26፥3-5:24)፤ ባረከውም፤ ዘፍ. 26፥12-14:28:29። ልጆቹን ባረካቸው፤ ዘፍ. 26፥34-28፥5። 180 ዓመት ሲሆነው ሞተ፤ ዘፍ. 35፥28:29። ጳውሎስ በእምነት የተወለዱትን የእግዚአብሔር ልጆች «የተስፋ ቃል ልጅ» በሆነው በይስሐቅ መሰላቸው፤ ሮም 9፥6-9፤ ገላ. 4፥21-31። የእምነት ሰው መሆኑ በዕብ. 11፥9:20 ተጽፏል።

**ይቅርታ**፤ ሰው በሀብቱ፥ በክብሩ፥ በስሙ፥ በመብቱ ወይም በሕግ ሲበደል፥ ለበደሉ አቤቱታ ባያቀርብ፥ ብድራትን ባይፈልግ፥ ቂምና በቀልም ባይኖረው መበደሉን ረስቶታልና ይቅርታ አደረገ ማለት ነው። እግዚአብሔር ይቅር ባይ ነው፤ ነህ. 9፥17፤ ኢሳ. 55፥7፤ ዳን. 9፥9:10። ነገር ግን ሰው ኃጢአቱን ባይተው፥ እግዚአብሔር ይቅር ሊለው አይፈቅድም፤ ዘዳ. 29፥19:20፤ ኤር. 5፥7። እግዚአብሔር ይቅር የሚለው በክርስቶስ ሞት መሠረት ነው፤ ማቴ. 26፥28፤ ኤፌ. 4፥32። «ማስተስረያ» ይመ.። ይቅርታን ለማግኘት ኃጢአትን መናዘዝ ያስፈልጋል፤ 1ዮሐ. 1፥9። እንደዚሁም እግዚአብሔር ይቅር ካለን ይቅር ባዮች መሆን ያስፈልገናል፤ ኤፌ. 4፥32፤ ቆላ. 3፥13። ይቅር ባንል፥ የእግዚአብሔርን ሥራ አልተረዳንም፤ ይቅርታንም አናገኝም፤ ማቴ. 6፥12:14:15፤ 18፥23-35። «መናዘዝ» ይመ.

**ይብራ**፤ (ዳክዬ)፤ እግሩ የጃንጥላ መልክ ያለው፥ በባሕር ውስጥ የሚኖር የባሕር ዶሮ ወይም አሞራ፤ ዘሌ. 11፥19። «ወፎች» ይመ.

**ይዲድያ**፤ «በእግዚአብሔር የተወደደ» ማለት ነው። ናታን ሰሎሞንን በዚህ ስም ሰየመው፤ 2ሳሙ. 12፥24:25።

**ይግባኝ**፤ ጉዳዩ ወደ የበላይ ዳኛ ይቅረብልኝ፤ ይሰማልኝ ማለት ነው። ዕብራዊ የሆነ ሁሉ በአሪት ሕግ መሠረት በመጀመሪያ ለሹሙ፥ በኋላም የከበደውን ነገር ለሙሴ ሊያመለክት ይችል ነበር፤ ዘጸ. 18፥21-27። እንደዚሁም ከሙሴ በኋላ የበላይ ዳኛ ይገኝ ነበር፤ ዘዳ. 17፥8-13። በሮም መንግሥትም ሮማዊ ዜጋ ለቄሣር ይግባኝ የማለት መብት ነበረው፤ ሐ.ሥ. 25፥9-12።

**ዮሐናን**፤ ትርጉሙ «እግዚአብሔር ጸጋ ሰጭ ነው» ማለት ነው። ኢየሩሳሌም በጠላት ከተያዘች በኋላ ጎዶልያስ ወደሚባለው ገዥ ከመጡት ከይሁዳ የጭፍራ አለቆች አንዱ ነበረ፤ 2ነገ. 25፥23፤ ኤር. 40፥8። ጎዶልያስንም ከእስማኤል ሤራ ይጠበቅ ዘንድ በማስጠንቀቅ «እንዳይገድልህ ልግደለው» አለው፤ ኤር. 40፥13-16። ጎዶልያስም ከተገደለ በኋላ በይሁዳ ለቀሩት አይሁድ መሪ ሆነ፤ ኤር. 41፥11-15። የኤርምያስንም ቃል ሳይሰማ ወደ ግብጽ ወሰዳቸው፤ ኤር. 41፥16-43፥7።

**ዮሐንስ**፤ «እግዚአብሔር ጸጋ ነው» ማለት ነው። በዚህ ስም ብዙ ሰዎች ተጠርተውበታል፤ ከእነርሱም የታወቁት መጥምቁ ዮሐንስ፥ ሐዋርያው ዮሐንስ፥ ማርቆስ ዮሐንስ ናቸው። «ማርቆስ» ይመ.

**ዮሐንስ መጥምቁ**፤ ለኢየሱስ የእስራኤልን ሕዝብ ያዘጋጀ የእግዚአብሔር መልእክተኛ፤ ማር. 1፥1-4። ዮሐንስ በማኅፀን ሳለ በመንፈስ ቅዱስ ተሞላ፥ ስለዚህም በማኅፀን ሳለ ኢየሱስን ዐውቆ ዘለለ፤ ሉቃ. 1፥15:41:44። በገብርኤል ቃል መሠረት ከዘካርያስና ከኤልሳቤጥ ተወለደ፤ ናዝራዊ ሆኖ በምድረ በዳ አደገ፤ ሉቃ. 1፥13-17:57-66:80። የእግዚአብሔር ቃል ከመጣለት በኋላ ለኃጢአት ስርየት የንስሐን ጥምቀት በዮርዳኖስ ወንዝ አቅራቢያ ሰበከ። ሰዎች ከአይሁድ አገር ሁሉ እየመጡ ተጠመቁ። ዮሐንስ የግመል ጠጕር ለበሰ፥ ምግቡም አንበጣና የበረሃ ማር ነበረ፤ ዘሌ. 11፥22። ዮሐንስ እግዚአብሔር በሕዝቡ ላይ ለመፍረድ እንደተዘጋጀ፥ ከእርሱም በኋላ ሌላ እንደሚመጣ ሰበከ። የሚመጣውም (ክርስቶስ) በመንፈስ ቅዱስ እንደሚያጠምቅ፥ ሕዝቡንም እንደሚያነጻ ገለጠ። ዮሐንስ ሁልጊዜ ራሱን ዝቅ፥ የሚመጣውን ግን ከፍ ያደርግ ነበር። ሰዎችን ሳይፈራ እንደ ሁኔታቸውና እንደ ኃጢአታቸው ወቀሳቸው፤ ማቴ. 3፥4-12፤ ማር. 1፥4-8፤ ሉቃ. 3፥1-17፤ ዮሐ. 1፥19-28። ዮሐንስ በዮርዳኖስ ወንዝ ዳር ሲያስተምር ሳለ ኢየሱስ መጥቶ እንዲያጠምቀው ጠየቀው። ዮሐንስ ቢያመነታም እንኳ፥ የክርስቶስን ትእዛዝ ለመፈጸም አጠመቀው፤ ማቴ. 3፥13-17። ዮሐንስ ሥራውን በመቀጠል «እነሆ የዓለምን ኃጢአት የሚያስወግድ የእግዚአብሔር በግ» ብሎ ስለ ኢየሱስ መሰከረ፤ ዮሐ. 1፥29-34። ሰዎች ኢየሱስን እንደሚከተሉት ሲሰማ ተደሰተ፤ ዮሐ. 3፥22-30።

ሄሮድስ የወንድሙን ሚስት በማግባቱ ዮሐንስ ስለወቀሰው አሳሰረው። ሲታሰር ሳለ ኢየሱስ መሲሕ መሆኑን ወይም አለመሆኑን እንዲጠይቁት ሁለት ደቀ መዛሙርትን ላከ። ኢየሱስ ዮሐንስ የብ.ኪ. የመጨረሻ ነቢይ መሆኑን መሰከረለት (ሉቃ. 7፥18-35፤ 16፥16)፥ በሌላም ጊዜ የሚልክያስን ትንቢት ስለ ኤልያስ እንደፈጸመ ተናገረ፤ ማቴ. 17፥9-13፤ «ኤልያስ» ይመ.። የሄሮድስ ሚስት በልጅዋ ዘፈን ምክንያት የዮሐንስን ራስ አስቈረጠችው፥ በደቀ መዛሙርቱም ተቀበረ፤ ማር. 6፥14-29። ከሞተ ከብዙ ዓመት በኋላ የዮሐንስን ትምህርት የሚከተሉ ተገኙ፤ ሐ.ሥ. 18፥24:25፤ 19፥1-7።

**ዮሐንስ ሐዋርያው**፤ የያዕቆብ ወንድም የዘብዴዎስ ልጅ፤ ማቴ. 4፥21። እናቱ ሰሎሜ ሳትሆን አትቀርም፤ ማቴ. 27፥56፤ ማር. 16፥1። ወላጆቹ ሀብታሞች ነበሩ፤ ማር. 1፥20፤ 15፥40-41። ከመጥምቁ ዮሐንስ ደቀ መዛሙርት አንዱ ሳይሆን አልቀረም፤ ዮሐ. 1፥35-42። ዓሣ በማጥመድ ላይ ሳለ ኢየሱስ ጠራው፤ ማር. 1፥19:20። ዮሐንስና ወንድሙ ያዕቆብ ኃይለኞች ነበሩና ኢየሱስ «ቦአኔርጌስ» ብሎ ሰየማቸው። ቦአኔርጌስ ማለት «የነጐድጓድ ልጆች» ማለት ነው፤ ማር. 3፥17። ይህም ስያሜ ክርስቶስን ያልተቀበሉትን ለማጥፋት፥ በክርስቶስም መንግሥት ራሳቸውን ታላቅ ለማድረግ ስለተመኙ፥ የችኩልነት ጠባያቸውን ይገልጣል፤ ሉቃ. 9፥54፤ ማር. 10፥37። ክርስቶስ ሐዋርያትን በሙሉ በማይፈልግበት ጊዜ፥ ከጴጥሮስና ከያዕቆብ ጋር ዮሐንስን ሦስት ጊዜ አስከትሎ ወጣ፤ ማር. 5፥37፤ 9፥2፤ 14፥33። ከጴጥሮስ ጋር የፋሲካ እራት አዘጋጀ፤ ሉቃ. 22፥8። በዮሐንስ ወንጌል ዮሐንስ በስሙ አልተጠቀሰም። ነገር ግን «ኢየሱስ ይወደው የነበረ ደቀ መዝሙር» ሲል ዮሐንስን እንደሚያመለክት ብዙዎቹ ያምናሉ፤ ዮሐ. 13፥23፤ 19፥26:27፤ 20፥2:8፤ 21፥20።

በሐዋርያት ሥራ ዮሐንስ ከጴጥሮስ ጋር አንካሳ ሲፈውስ፥ መከራ ሲቀበል (ሐ.ሥ. 4፥13)፥ ወደ ሰማርያ ሲሄድ እንደነበረ እንመለከታለን፤ ሐ.ሥ. 8፥14። በኢየሩሳሌም ቆይቶ ከጴጥሮስና ከያዕቆብ ጋር በቤ.ክ. ይሠራ ነበር፤ ገላ. 2፥1-9። ወደ ሕይወቱ መጨረሻ ከኤፌሶን ተሰድዶ ፍጥሞ በምትባል ደሴት ኖረ፤ ራእ. 1፥9። ዮሐንስ አንዱን ወንጌል፥ ሦስት መልእክቶችንና ራእይን እንደጻፈ ብዙዎች ያምናሉ።

**የዮሐንስ ወንጌል**፤ ስሙ በዚህ ወንጌል ባይጠቀስም «ኢየሱስ ይወደው የነበረው ደቀ መዝሙር» ሐዋርያው ዮሐንስ እንደሆነ ይታመናል። ይህን ወንጌል ሲጽፍ በመጀመሪያ በየትኛው ቀንና ሰዓት ከኢየሱስ ጋር እንደተገናኘ፥ እንደዚሁም በስንት ሰዓት ክሥተቶች እንደተፈጸሙ ይመዘግባል፤ 1፥40፤ 4፥6:52፤ 19፥14። አንዳንዶች ከ85 ዓ.ም. በኋላ፥ ሌሎች ደግሞ ኢየሩሳሌም ከወደቀችበት ከ70 ዓ.ም. በፊት ወንጌሉ እንደተጻፈ ይገምታሉ።

የዮሐንስ ወንጌል ማቴዎስ፥ ማርቆስና ሉቃስ ከጻፏቸው ወንጌላት ይለያል። የዮሐንስ ወንጌል በገሊላ ሳይሆን በኢየሩሳሌምና በዓመት በዓላት ላይ በተፈጸሙ ድርጊቶች ላይ ያተኩራል። የታወቁትን ምሳሌዎች አይመዘግብም፥ ከተአምራቱም ሰባቱን ብቻ መርጦ ይጠቅሳል። በዚህም ፈንታ ረጅም መግቢያ፥ ከአይሁድ መሪዎች ጋር የተደረገ ክርክር፥ በመጨረሻው እራት ከአብና ከመንፈስ ቅዱስ ጋር ስላለው ግንኙነት ጌታ ለሐዋርያት የሰጠው ትምህርት፥ በታሰረበት ሌሊት ያቀረበው ጸሎት ተመዝግቧል። እንደሌሎች ወንጌላት ሁሉ የክርስቶስን ሞትና ትንሣኤ ግን በሰፊው ይተርካል።

የዮሐንስ ወንጌል ዓላማ ግልጥና ጣምራ ይዘት ያለው ነው፤ ይኸውም ሰዎች ክርስቶስ የእግዚአብሔር ልጅ መሆኑን እንዲያምኑና አምነው በስሙ ሕይወትን እንዲያገኙ ነው፤ 20፥31። ወንጌሉ ለእነዚህ ሁለት ነገሮች ትኩረት ሲሰጥ እንደሚከተለው ነው ፡-

1. ክርስቶስ የእግዚአብሔር ልጅ ነው። ይህ በብዙ መንገድ ይታያል፥ በጸሐፊው መግቢያ፥ ለደቀ መዛሙርት ኢየሱስ በሰጠው ትምህርት፥ ከአይሁድ መምህራን ጋር በተካሄደው ክርክር፥ በአገልግሎቱና በትንሣኤው። በተለይ ማንነቱ ደግሞ በሚከተሉት ይገለጣል ፡-

ሀ) ኢየሱስ የእግዚአብሔር «ቃል» ነው፤ 1፥1-18።

ለ) ሰባቱ «ምልክቶች» የክርስቶስን ሥልጣን በለውጥ (2፥1-11)፥ በርቀት (4፥46-54)፥ በጊዜ (5፥1-9)፥ በመጠን (6፥5-13)፥ በተፈጥሮ (6፥19-21)፥ በበሽታ (9፥1-7) እና በሞት ላይ ያሳያሉ፤ 11፥38-44።

ሐ) ሰባት ጊዜ «እኔ ... ነኝ» በማለቱ አስፈላጊውን ነገር ሁሉ በራሱ እንደሚፈጽም ለአማኙ ገልጧል፤ 6፥35፤ 8፥12፤ 10፥7:11፤ 11፥25፤ 14፥6፤ 15፥1። በዘጸ. 3፥14 ላይም «እኔ ነኝ» በማለቱ ከእግዚአብሔር ጋር አንድ መሆኑን ያረጋግጣል።

መ) ኢየሱስ አስቀድሞ የነበረ፥ ከአብ የመጣና ወደ አብ ተመልሶ የሄደ ጌታ ነው፤ 3፥13፤ 8፥42:58፤ 16፥27-28፤ 17፥5:8:24፤ 20፥17።

ሠ) ኢየሱስ ከአብ የተለየ አካል ቢሆንም ከእርሱ ጋር በመለኮት እኩል ነው፤ 3፥16፤ 5፥17-23፤ 10፥30፤ 14፥8-11፤ 17፥3-5። ልጅነቱን የገለጠው ወደ አብ በመመልከቱ፥ የአብን ቃል በመናገሩ፥ ሥራውን በመሥራቱና ፈቃዱን በመፈጸሙ ነው፤ 4፥34፤ 5፥36፤ 14፥10:24፤ 17፥4:8። ልጅ ሆኖ በመለኮትና በባሕርይ ሳይሆን በቅደም ተከተል የአብን ብልጫ አሳየ፤ 14፥28። የእርሱ ልጅነት የባሕርይ ነውና ከሌሎች የተለየ ነው፤ 3፥16፤ 20፥17።

ረ) መንፈስ ቅዱስ እንደ እርሱ ያለ «ሌላ አጽናኝ» ነው፤ 14፥15-16:26፤ 15፥25-26፤ 16፥7-15።

ሰ) የትንሣኤው ታሪኮች አምላክነቱን ያሳያሉ፤ 20፥17:28።

ሸ) የክርስቶስ ዳግም ምጽአት ልዕልናውን ያሳያል፤ 5፥24:28-29፤ 14፥1-3፤ 21፥22።

2. የዘለዓለም ሕይወት ክርስቶስን በማመን ይገኛል፤ 1፥12፤ 3፥16:36፤ 6፥47። ይህም ሕይወት በራሱ በክርስቶስ ነው፤ 5፥26፤ 6፥53-54፤ ደግሞም የ1 ‹ሐ›ን ጥቅሶች ይመ.። ሰው የኃጢአት ባሪያ በመሆኑ ወደ ክርስቶስ አይሄድም (3፥19፤ 8፥34)፥ ስለዚህ እግዚአብሔር በሰው ልብ ካልሠራ በስተቀር ወደ ክርስቶስ ሊደርስ አይችልም፤ 1፥13፤ 3፥3-5፤ 6፥37:44:65።

መንፈስ ቅዱስ ሰውን ስለ ኃጢአት፥ ስለ ጽድቅና ስለ ፍርድ ይወቅሳል (16፥8)፤ የእግዚአብሔርን መንግሥት እንዲያይና እንዲገባበት ይወስደዋል (3፥3:5)፤ ተትረፍርፎ ባለው ሕይወት

እማኙን ይሞላል (7፥38-39፤ 10፥10)፤ ያጽናዋልና ክርስቶስን ወደ ማወቅ ይመራዋል (14፥15-17:26፤ 15፥26፤ 16፥13-14)፤ ለአገልግሎቱም ኃይልን ይሰጠዋል፤ 14፥26፤ 20፥21-23። እማኙ በዚህ ሁኔታ ሲገኝ የዘለዓለም ሕይወት ሙሉ ዋስትና አለው፤ 5፥24፤ 10፥28-29።

ሰዎች የክርስቶስን ቃል ሰምተው በእምነት ሲያድጉ ይታያሉ። ይህም በተለይ በጴጥሮስ ታሪክ ጎልቶ ሲገለጥ፥ በእንድርያስ፥ በፊልጶስ፥ በናትናኤል፥ በኒቆዲሞስ፥ በማርታና በማርያም፥ በቶማስና በራሱ በዮሐንስ ታሪክ ይታያል። ሰዎች ቃሉን ባይቀበሉ ግን የሚደርስባቸው ምን እንደሆነ በይሁዳና በጲላጦስ ታሪኮች ተመልክቷል።

ክርስቶስ ትምህርቱን በማቅረቡ (13፥13-15)፥ ትምህርት በማስተማሩ (16፥1)፥ ጸሎት በመጸለዩ (17፥6-18)፥ መንፈስ ቅዱስን በመስጠቱ (20፥21-23)፥ ተአምር በማድረጉ (21፥1-14) እና ለጴጥሮስ የመሪነት ጥሪውን በማደሱ (21፥15-23) ሐዋርያትን በሚመጣው የመንፈስ ቅዱስ ዘመን ለወንጌል ስብከት አዘጋጃቸው።

የዮሐንስ ወንጌል በሁለት ይከፈላል፤ ይኸውም ከም. 1-12 በውጭ ሆኖ ክርስቶስ ያደረገውንና ያስተማረውን ሲገልጥ፥ ከም. 13-21 ያለው ደግሞ ለሐዋርያት ያስተማረውን፥ ለአባቱ የጸለየውን፥ መያዙን፥ መሰቀሉንና ከሙታን መነሣቱን ይገልጣል። «ወንጌል» ይመ.

**የዮሐንስ መልእክት - 1ኛው፤** ይህን መልእክት ቅዱስ ዮሐንስ በኤፌሶን ሲኖር ሳለ በ90 ዓ.ም. ገደማ የጻፈው ይመስላል። የጻፈውም እስያ በሚባለው አውራጃ የነበሩት የአብ. ክ. አባሎች የዘለዓለም ሕይወት እንዳላቸው እንዲያውቁ ነበር፤ 5፥13። ምእመናኑ ይህን ለምን አላወቁም? ለዚህ የሚሰጡ ብዙ ምክንያቶች ቢኖሩም ከምክንያቶቹ አንዱ ግን ለየት ያለ ነበር፤ ይኸውም የግኖስቲኮች ትምህርት ነው፤ «ግኖስቲክ» ይመ.። የዚህ ትምህርት ዐዋቂዎች «ኢየሱስ ክርስቶስ በሥጋ አልመጣም» በማለት አምላክነቱንና ፍጹም ሰው መሆኑን ክደዋል፤ 4፥1-6፤ 5፥1-12። ከእግዚአብሔር ልዩ ዕውቀት እንደተቀበሉና ያለእነርሱ እውነተኛ ክርስቲያን እንደሌለ ያስቡ ነበር፤ 2፥19። ዮሐንስ በመደጋገም «እናውቃለን» እያለ ምእመናን ስለ መዳናቸው ጥርጥር እንዳይኖራቸው የትምህርቱን ተከታዮች ሐሰተኞች «የክርስቶስ ተቃዋሚዎች»፥ «ውሸታም»፥ «የሚያስቱአችሁ» እና «የዲያብሎስ ልጆች» በማለት አጋለጣቸው፤ 2፥18:22:26፤ 3፥10። ዮሐንስ፥ ሰው ክርስቲያን መሆኑን ለማረጋገጥ ሦስት የብቃት መለኪያዎችን ሰጠ፤ እነርሱም 1ኛው የእግዚአብሔርን ትእዛዛት መፈጸም፥ 2ኛው ወንድሞችን ማፍቀር፥ 3ኛው ትክክለኛ ትምህርትን መቀበል ናቸው። እነዚህን ሦስት መለኪያዎች እየጠቀሰና ምሥጢራቸውንም በስፋት እያብራራ ይቀጥላል፤ ከዚሁም ጋር ስለ አንዳንድ ነገሮች ተጨማሪ ማስታወሻዎችን ይሰጣል።

አከፋፈል :-

1. መግቢያ፤ ዮሐንስ ስለ ራሱ የሰጠው ምስክርነት፤ 1፥1-4።
2. ሦስቱ የግኖስቲክ ውሸቶች፤
ሀ) ኃጢአት ኅብረታችንን አያፈርስም፤ 1፥5-7።
ለ) ኃጢአት በክርስቲያን አይኖርም፤ 1፥8-9።
ሐ) ክርስቲያን ኃጢአት አይፈጽምም፤ 1፥10-2፥2።
3. የሦስቱ መለኪያዎች 1ኛ ማብራሪያ፤
ሀ) የግብረገብ መለኪያ :- መታዘዝ፤ 2፥3-6።
ለ) የኅብረተሰብ መለኪያ :- ፍቅር፤ 2፥7-11።
ሐ) ስለ ቤ.ክ. ተጨማሪ መግለጫ፤ 2፥12-14።
መ) ስለ ዓለም ተጨማሪ መግለጫ፤ 2፥15-17።
ሠ) የትምህርተ መለኮት መለኪያ :- እምነት፤ 2፥18-27።
4. የሦስቱ መለኪያዎች 2ኛ ማብራሪያ፤
ሀ) የምራል መለኪያ :- ጽድቅ፤ 2፥28-3፥10።
ለ) የኅብረተሰብ መለኪያ :- ፍቅር፤ 3፥11-18።
ሐ) ስለ አለኝታ ተጨማሪ መግለጫ፤ 3፥19-24።
መ) የትምህርተ መለኮት መለኪያ :- እምነት፤ 4፥1-6።
5. የሦስቱ መለኪያዎች 3ኛ ማብራሪያ፤
ሀ) የኅብረተሰብ መለኪያ :- ፍቅር፤ 4፥7-12።
ለ) የፍቅርና የእምነት አንድነት፤ 4፥13-21።
ሐ) የሦስቱ መለኪያዎች አንድነት፤ 5፥1-5።
6. ሦስቱ ምስክሮች፤ 5፥6-12።
7. ከትምህርቱ የተነሣ የሚገኝ አለኝታ፤ 5፥13-17።
8. ሦስቱ ዋና ዋና ነጥቦች፤ 5፥18-21።

**የዮሐንስ መልእክት - 2ኛው፤** እንደ መጀመሪያይቱ መልእክት ሆና ይህችም በሐዋርያው ዮሐንስ በኤፌሶን ከተማ በ90 ዓ.ም. ገደማ የተጻፈች ይመስላል። ዮሐንስ ወደ አንዲት እማኝ ሴት ጽፎ በመጀመሪያይቱ መልእክት ላይ ከተጠቀሱት መናፍቃንና ትምህርታቸው ያስጠነቅቃታል።

**የዮሐንስ መልእክት - 3ኛው፤** የዚህች መልእክት ጸሐፊና የተጻፈችበት ዘመን የተላከችበትም ከተማ እንደ ሁለቱ መልእክታት ነው። ዮሐንስ ጋይዮስ ወደተባለው እማኝ ሰው ጽፎ እንግዶችን ስለሚቀበል ያመሰግነውና በዚያች ቤ.ክ. ውስጥ ስለገባው መለያየት በመናገር መልካም ያደረገውን አንዱን ሰው ይደግፋል።

**የዮሐንስ ራእይ፤** ይህ የትንቢት መጽሐፍ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ በመልአኩ በኩል ለሐዋርያው ዮሐንስ የገለጠለት ራእይ ነው፤ 1፥1:4:9፤ 22፥8። ቅዱስ ዮሐንስ በእስያ አውራጃ ለነበሩት 7 አብ.ክ. ራእዩን በጽሑፍ አስተላለፈላቸው፤ 1፥19። ራእዩ የተጻፈው በስደት ዘመን በ95 ዓ.ም. ገደማ ሊሆን ይችላል። በ11፥19 ግን ቤተ መቅደሱ አሁንም እንዳለ ስለሚታይ፥

አንዳንድ ሊቃውንት የዮሐንስ ራእይ ኢየሩሳሌም ሳይፈርስ ከ70 ዓ.ም. በፊት እንደተጻፈ ይገምታሉ።

1. <u>የመጽሐፉ አጻጻፍ</u>፤

ከሌሎች የአ.ኪ. መጻሕፍት ለየት ያለ ሆኖ የሕዝቅኤልን፥ የዳንኤልንና የዘካርያስን የትንቢት መጻሕፍት ያሳስባል። ከመጽሐፉ 404 ቍጥሮች ውስጥ 278ቱ የብ.ኪ.ን አሳብ ያንጸባርቃሉ። መጽሐፉን ስናነብ የሚከተሉትን ይዘቶች እንመለከታለን :-

ሀ) ጠቅላላ አቀራረቡ ታላቅ የመንፈሳዊ ተግባር (ድራማ) አቀራረብ ነው። ራእዩ በመጀመሪያ በእስያ አብ.ክ. ሲነበብ አድማጮቹ የሚሰሙት በዓይን ሕሊና እየታያቸው የሚቀጥለውን «ትርዒት» በጉጉት ሳይጠብቁ አልቀሩም። እያንዳንዱ ትርዒት ከፍተኛ ደረጃ ላይ በደረሰ ክሥተት ይደመደማል፤ እነዚህም ክሥተቶች በየትርዒቱ የአድማጮቹን ስሜት በይበልጥ እየቀሰቀሱ ይሄዳሉ።

ለ) ብዙ ጊዜ የዒድን፥ ከግብጽ የመውጣት፥ የኤልያስና የምርኮ ታሪኮች ለመግለጫ መሠረት ናቸው፤ «ትንቢተ ኢሳይያስም» ብዙ ጊዜ ተጠቅሷል።

ሐ) ክርስቶስ በሰጠው የትንቢት ቅደም ተከተል ላይ እንደተመሠረተ (በተለይ ም. 6ን ከማቴ. ም. 24 ጋር አስተያይ)፥ እንደዚሁም ከ2ተሰ. 1፥3-2፥2፥12 ጋር እንደሚስማማ ይታያል።

መ) ቍጥሮች አብዛኛውን ጊዜ የሚያመለክቱት ብዛትን ሳይሆን አሳብን ነው። ለምሳሌ ቍጥር 7 ብዙ ጊዜ «ፍጹምነትን» በማመልከት 52 ጊዜ ጥቅም ላይ ውሏል። «ቍጥር» ይመ.

ሠ) ለእያንዳንዱ ክሥተት፥ ቃል፥ ምሳሌ... ወዘተ ዋና ትርጉም ባይሰጥም ጠቅላላው ተግባር መልእክቱን ይሰጣል።

2. <u>የመጽሐፉ መልእክት</u>፤

ጠቅላላ ራእዩ ለሚከተሉት ነጥቦች አጽንዖት ይሰጣል :-

ሀ) የእግዚአብሔር ልዕልና፥

ለ) የሰይጣን ኃይል፥ ጥላቻና የሚፈረድበት መሆኑ ፥

ሐ) የዓለም ኃይል፥ ከንቱነትና አላፊነት፥

መ) ቤ.ክ. የምትቀበለው መከራ፥

ሠ) የመጨረሻው ፍርድ መቃረብ፥

ረ) የክርስቶስ ድልና የመገለጡ ክብር፥

ሰ) እስከ መጨረሻው ምእመናን መታገሣቸው፥ ጥበቃቸውና ብፅዕናቸው።

3. <u>የመጽሐፉ አተረጓጎም</u>፤

ስለ መጽሐፉ ብዙ ዓይነት አተረጓጎም እንዳለ ይታወቃል። አንዳንዶች የመጽሐፉን አሳብ ከዓለም ታሪክ ጋር ለማዛመድ ሲሞክሩ፥ ከዮሐንስ ዘመን ወይም ከዓለም መጨረሻ ዘመን ወይም ደግሞ ከጠቅላላ የቤ.ክ. ዘመን ጋር ያያይዙታል። ሌሎች ግን በመጽሐፉ መንፈሳዊ አሳብ ቅደም ተከተል ላይ እንጂ በዓለም ታሪክ ቅደም ተከተል ላይ አያተኵሩም። ይህንም ሲያደርጉ አሳቡ በይበልጥ እየከበደ ሲሄድና ወደ ፍጻሜው ሲቀርብ ይመለከቱታል። የተቀሩት ደግሞ ስለ ክርስቶስ ተቃዋሚ፥ ስለ ታላቁ መከራ፥ ስለ እስራኤል ሕዝብ ምድራዊ ተስፋና ስለ ሺህ ዓመት ላላቸው የአስተሳሰብ ትርጉም አጽንዖት ይሰጣሉ፤ አርእስቱን በመዝገበ ቃላት ይመ.። ቢሆንም የመጀመሪያ አድማጮቹ እምነት በገሃዱ ላይ አሸናፊ እንደሆነ፥ ፍርድ ቢዘገይም እንደማይቀርና በዓለም ታሪክ ላይ ክርስቲያን ያለው አመለካከት እንደሚስተካከል ተረድተው መደሰት እንደቻሉ ሁሉ፥ እኛም ሐሤት ማድረግ ይገባናል።

4. <u>የመጽሐፉ አከፋፈል</u>፤

እንደ አተረጓጎሙ ዓይነት ብዙ አከፋፈል አለ። የሚከተለው አጭር አከፋፈል «በየዕለቱ ከእግዚአብሔር ጋር» 4ኛ ዓመት መጽሐፍ ገጽ 222-223 ከሚገኘው ሰፊ አከፋፈል የተወሰደ ነው።

1. መግቢያ፤ ለ7ቱ አብ.ክ. ሰላምታ፤ 1፥1-8።
2. 7 መልእክታት ለአብ.ክ.፤ 1፥9-3፥22።
3. 7 የተፈቱ ማኅተሞች፤ የቤ.ክ. መከራ፤ 4፥1-8፥1።
4. 7 መለከቶች፤ ለዓለም ማስጠንቀቂያ፤ 8፥2-11፥18።
5. 7 ራእዮች፤ የዓለም ታሪክ ተግባር (ድራማ)፤ 11፥19-15፥4።
6. 7ቱ መቅሠፍቶች፤ የዓለም ቅጣት፤ 15፥5-16፥21።
7. 7 የፍትሕ ውሳኔዎች በባቢሎን ላይ፤ 17፥1-19፥10።
8. 7 ራእዮች፤ ከዓለም ታሪክ በስተኋላ ያለው ትግል፤ 19፥11-21፥8።
9. 7 የመጨረሻ መግለጫዎች፤ 21፥9-22፥19።
10. መደምደሚያ፤ 22፥20-21።

**ዮርዳኖስ**፤ ወራጅ ማለት ነው። ከአርሞንዔም ተራራ የሚነሣ በገሊላ ባሕር አልፎ ወደ ጨው ባሕር የሚፈስ ወንዝ፤ ከገሊላ ባሕር እስከ ጨው ባሕር በአየር 100 ኪ.ሜ. ሲሆን ወንዙ ጠመዝማዛ ስለሆነ ከገሊላ ባሕር እስከ ጨው ባሕር ድረስ 270 ኪ.ሜ. ይሆናል፤ የወንዙ ጥልቀት እንደ ዝናሙ ብዛት ከአንድ እስከ ሦስት ሜትር፥ ስፋቱም እስከ 30 ሜትር ይሆናል። እስራኤላውያን በኢያሪኮ ፊት ለፊት በተአምር ተሻገሩት (ኢያሱ 3፥14-17)፤ እንደዚሁም ኤልያስና ኤልሳዕ በተአምር ተሻገሩት (2ነገ. 2፥8-14)፤ ንዕማን በዮርዳኖስ ውሃ ታጥቦ ከለምጹ ነጻ (2ነገ. 5፥10:14)፤ ኢየሱስም በዚሁ ወንዝ በተጠመቀ ጊዜ መንፈስ ቅዱስ ወርዶ አረፈበት፤ ማቴ. 3፥13። ከ. 5።

**ዮሴፍ**፤ ትርጉሙ «ይጨምር» ማለት ነው። የያዕቆብ ዐሥራ አንደኛ ወንድ ልጅ፤ የራሔልም በኵር

ልጅ፤ ዘፍ. 30፥22-24። ከጠባዩ መልካምነትና ከዝናው፥ ከፈጸመውም ታላቅ ሥራ የተነሣ ከያዕቆብ ልጆች ሁሉ የተከበረ ሆነ። አባቱ በተለይ ወደደው። ብዙ ሕልም ስላየና ስለ ወንድሞቹ መጥፎ ወሬ ለአባታቸው ስላወራ፥ ጠልተው ሸጡት፤ ዘፍ. 37። በግብጽ ባሪያ ሆኖ ሳለ በጲጥፋራ ቤት ለአስተዳዳሪነት ተሾመ። የጲጥፋራ ሚስት በሐሰት ስትከሰው ግን በግዞት ታሰረ። እዚያም ሞገስን አግኝቶ ከግዞት ቤት አለቃ በታች ኀላፊ ሆነ፤ ዘፍ. 39። ሕልሞችን ለመተርጐም ስለቻለ፥ ፈርዖን ፈታው፤ በአገሩም ሁሉ ላይ አለቃ አደረገው፤ ዘፍ. 40፤41። ሰባት ዓመት እህልን እየሰበሰበ በረሀብ ዘመን ብዙ ሰዎችን፥ የገዛ ራሱን ቤተሰብ ጭምር ከሞት አዳነ፤ ዘፍ. 42-45፤ 47፥13-26።

ግብጻዊቷን አስናትን አግብቶ ምናሴንና ኤፍሬምን ወለደ፤ ዘፍ. 41፥50-52። አባቱንና ወንድሞቹን ወደ ግብጽ አስመጥቶ መገባቸው፤ ዘፍ. 46፥1-47፥12። አባቱን በከነዓን ቀበረው፤ ዘፍ. 49፥29-50፥14። በወንድሞቹ ቂም አልያዘም፤ ዘፍ. 50፥15-21። ሳይሞት ዐፅሙን በከነዓን እንዲቀብሩት የእስራኤልን ልጆች በማማሉ፥ እምነቱን ገለጠ፤ ዘፍ. 50፥22-26፤ ኢያሱ 24፥32፤ ዕብ. 11፥22። ከእስራኤል ነገዶች የሁለቱ አባት ሆነ። ያዕቆብ፥ ብኵርናው ለዮሴፍ ይሁን በማለት የዮሴፍን ልጆች ምናሴንና ኤፍሬምን ባረከ፤ በስሞቻቸውም ነገደ ምናሴና ነገደ ኤፍሬም ተብለው ተጠሩ፤ 1ዜ.መ. 5፥1፤ ዘፍ. 48፤ ዘኍ. 1፥4:9:10፤ ዘዳ. 33፥13-17። «ነገድ» ይመ.

**ዮሴፍ የማርያም እጮኛ፤** በናዝሬት በአናጢነት ሥራ ይተዳደር ነበር፤ ማቴ. 1፥16፤ 13፥55። ከዳዊት ዘር ተወለደ፤ ሉቃ. 2፥4-5። ጻድቅ ሰው ነበረና ማርያም እንደፀነሰች ባወቀ ጊዜ በስውር ሊተዋት አሰበ። የእግዚአብሔር መልአክ በመንፈስ ቅዱስ እንደፀነሰች ካስረዳው በኋላ ግን እንደ መልአኩ ትእዛዝ ማርያምን ወሰዳት፤ ኢየሱስም በእርሱ ቤት አደገ። እንደ አባት ሆኖ በ40 ቀኑ ወደ ቤተ መቅደስ፥ በዐሥራ ሁለት ዓመቱ ለፋሲካ በዓል ከማርያም ጋር ኢየሱስን ወደ ኢየሩሳሌም ወሰደው፤ ማቴ. 1፥18-25፤ 2፥13-15:19-23፤ ሉቃ. 2፥22-24;41-52። ከዚያ በኋላ ግን ስለ ዮሴፍ ምንም ስላልተጻፈ፥ ኢየሱስም እናቱን ለዮሐንስ አደራ ስለሰጠ ዮሴፍ ሞቶ ይሆናል። «ማርያም ድንግል» ይመ.

**ዮሴፍ የአርማትያሱ፤** በራሱ መቃብር ኢየሱስን የቀበረ ቅንና ጻድቅ የነበረ የሸንጎ አማካሪ። በፊት አይሁድን ስለፈራ ክርስቶስን በስውር ተከተለው፤ ክርስቶስ ከተሰቀለ በኋላ ግን በድፍረት ከጲላጦስ የኢየሱስን ሥጋ ለመነ፤ ማቴ. 27፥57-60፤ ዮሐ. 19፥38፤ ሉቃ. 23፥50:51።

**ዮቶር፤** የምድያም ካህን፥ የሙሴ አማት። ራጉኤል የሚል ሌላ ስም ነበረው። ሙሴ ከግብጽ በሸሸ ጊዜ በቤቱ ተቀበለው፤ ልጁንም ሲፓራን ሚስት እንድትሆነው ሰጠው፤ ዘጸ. 2፥16:21፤ 3፥1፤ 4፥18። ለእስራኤል ያደረገውን ሁሉ በሰማ ጊዜ እግዚአብሔርን አከበረ፤ ዘጸ. 18፥1-12። ለሙሴም ጥሩ ምክር ሰጠው፤ ዘጸ. 18፥13-24። ኦባብ የሚባል ልጅ ነበረው፤ ዘኍ. 10፥29-32፤ መሳ. 4፥11።

**ዮናስ፤** ትርጕሙ «ርግብ» ማለት ነው። በዳግማዊ ኢዮርብዓም ዘመነ መንግሥት የነበረ ነቢይ። ኢዮርብዓም ሶርያውያንን አባርሮ የእስራኤልን ድንበር እንደሚመልስ ትንቢት ተናገረ። የዮናስ መኖሪያ በገሊላ በጋትሔፌር ከተማ ነበረ፤ አባቱም አማቴ ይባል ነበር፤ 2ነገ. 14፥25፤ ዮናስ 1፥1። እግዚአብሔር ሄደህ በነነዌ ላይ ስበክ ባለው ጊዜ ትእዛዙን ጥሶ በመርከብ ሸሸ። እግዚአብሔር ታላቅ ነፋስን፥ ነቢዩን የሚውጠውንም ታላቅ ዓሣ በማዘጋጀት ወደ ምድር መለሰው፤ ዮናስ 1፣2። እንደገና በተጠራ ጊዜ ግን ወደ ነነዌ ሄደ፥ ነነዌ እንደምትገለበጥ ሰበከ፤ የነነዌም ሰዎች ንስሓ በገቡ ጊዜ እግዚአብሔር ማራቸው፤ ዮናስ 3። ነቢዩ ግን በከተማይቱ መዳን አልተደሰተም፤ እግዚአብሔርም ቅልን ምሳሌ በማድረግ ምሕረት መልካም መሆኑን አስረዳው፤ ዮናስ 4።

**የዮናስ ትንቢት፤** በሌሎች የትንቢት መጻሕፍት የሚገኘው ዋና አሳብ የትንቢት መልእክት ሲሆን፥ በዚህ መጽሐፍ ግን የሚበልጠው ክፍል ስለ ራሱ ስለ ነቢዩ የሚተርክ ነው (በ1ነገ. 17-19 ስለ ኤልያስ የሚናገረውን ያነጻጽሩ)። መጽሐፉን የጻፈው ዮናስ ራሱ መሆኑ አልተገለጠም፤ ነገር ግን ሌላ ሰው ከዮናስ አፍ ሰምቶ የጻፈው ይመስላል። የመጽሐፉ ዋና መልእክት የእስራኤል አምላክ ብቻ ሳይሆን፥ የምድር ሕዝቦች ሁሉ አምላክ የሆነው እግዚአብሔር መሐሪ ነው (4፥2:11)፤ ነቢዩንም ሆነ (2፥5:10)፥ የነነዌን ሰዎች (3፥10) ወደ ንስሓ መርቶ ሊምራቸው እንደወደደ ዓለሙን የሚወድ ነው፤ ዮሐ. 3፥16። ክርስቶስ የዮናስን ከዓሣው ሆድ መውጣት የራሱ ትንሣኤ ምሳሌ አድርጎታል፤ ማቴ. 12፥39-42፤ ሉቃ. 11፥30-32።

አከፋፈል ፦

1. የዮናስ መኰብለልና መገታቱ፤ ም. 1።
2. የዮናስ ጸሎትና ወደ ቀድሞው ጥሪ መመለሱ፤ ም. 2።
3. የዮናስ ስብከትና ውጤቱ፤ ም. 3።
4. የዮናስ ቍጣና መገሠጹ፤ ም. 4።

**ዮናታን፤** ትርጕሙ «እግዚአብሔር ሰጥቷል» ማለት ነው። የእስራኤል ንጉሥ የሳኦል ታላቅ ልጅ፥ የዳዊትም ወዳጅ ነበረ፤ 1ሳሙ. 14፥49፤ 1ዜ.መ. 8፥33። ብርቱ የጦር አለቃ ሆኖ በጀግንነት ታላቅ ድል አገኘ፤ 1ሳሙ. 13፥2:3፤ 14፥1-23። ሕዝቡም ወደው ያከብሩት ነበር፤ 1ሳሙ. 14፥38-46። ከዳዊት ጋር ቃል ኪዳን ገባ፤ 1ሳሙ. 18፥1-4። ከሳኦልም ጋር አስታረቀው፤ 1ሳሙ. 19፥1-7። ከሳኦል ቍጣ ሊያድነው በማሰብ በስውር አሰናበተው፤ 1ሳሙ. 20። ሊያጽናናው ጐበኘው፤ 1ሳሙ. 23፥16-18። ከአባቱ ከሳኦል ጋር ፍልስጥኤማውያንን ሲወጋ ሞተ፤ 1ሳሙ.

31፥2:8-13። ዳዊትም ጆናንነቱንና ፍቅሩን አስታውሶ አለቀሰለት፤ ቅኔም ተቀኘለት፤ 2ሳሙ. 1፥22-26።

**ዮአስ፤** ትርጉሙ «እግዚአብሔር ሰጥቷል» ማለት ነው። የእስራኤል ንጉሥ የኢዩ የልጅ ልጅ ነው። ከ798 ከክ.በ. ጀምሮ 16 ዓመት በእስራኤል ላይ ነገሠ። ኢዮርብዓምም የጀመረውን አምልኮ ባዕድ አልተወም፤ እንደ ነቢዩ እንደ ኤልሳዕ ቃል በሶርያ ላይ ሦስት ጊዜ ድል ተቀዳጀ። የመጣበትንም የይሁዳን ንጉሥ አሸነፈ፤ 2ነገ. 13፥10-19:25፤ 14፥8-16።

**ዮአኪን፤** ትርጉሙ «እግዚአብሔር ያቆማል» ማለት ነው። ከአባቱ ከኢዮአቄም በኋላ በኢየሩሳሌም ሦስት ወር ነገሠ። 597 ከክ.በ. ከቤተሰቦቹና ከአለቆቹ፥ በጠቅላላ ከዐሥር ሺህ ሰዎች ጋር ወደ ባቢሎን ተማርኮ ሄደ፤ 2ነገ. 24፥8-17፤ 2ዜ.መ. 36፥9:10። ከምርኮኞቹም መካከል ሕዝቅኤል ሳይገኝ አልቀረም፤ ሕዝ. 1፥2። ኤርምያስ «ኢኮንያን» በሚለው ስሙ ሲጠራው፥ ከልጆቹ በዳዊት ዙፋን ላይ የሚነግሥ እንደማይገኝ ተናገረ፤ ኤር. 22፥24-30። በተማረከ በ37ኛው ዓመት በባቢሎን ከእስራት ተፈታ፤ 2ነገ. 25፥27-30። በባቢሎን ልጆችን ወለደ፤ የልጅ ልጁ ዘሩባቤል ከምርኮ ተመልሶ የይሁዳ ገዥ ሆነ። ይሁን እንጂ አልነገሠም፤ 1ዜ.መ. 3፥17-19፤ ዕዝ. 2፥2፤ ሐጌ 1፥1።

**ዮካብድ፤** ትርጉሙ «እግዚአብሔር ክብር ነው» ማለት ነው። የሙሴ እናት የሆነች የሌዊ ልጅ፤ ዘመድዋን እንበረምን አግብታ፥ ምርያምን፥ አሮንንና ሙሴን ወለደችለት፤ ዘጸ. 6፥20፤ ዘኍ. 26፥59። የእምነቷ ሥራ በዕብ. 11፥23 ተመስከረላት፤ ዘጸ. 2፥1-10።

**ዮዲት፤** መጽሐፈ ዮዲት ንጉሡ ናቡከደነፆር እስራኤላውያንን ለመውጋት የላከው ሆሎፎርኒስ የተባለው የጦር መሪ በእስራኤላዊቷ ዮዲት እጅ እንዴት እንደተገደለ የሚተርክ መጽሐፍ ነው። የኦርቶዶክስና የካቶሊክ አብ.ክ. ከብ.ኪ. መጻሕፍት ጋር ቈጥረው ይቀበሉታል።

**ዮዳሄ፤** ትርጉሙ «እግዚአብሔር ያውቃል» ማለት ነው። በክፉ ዘመን የዳዊት የመንግሥቱ ዘር እንዳይጠፋ ኢዮአስን ያሳደገው ካህን። የይሁዳ ንጉሥ አካዝያስ ከሞተ በኋላ፥ የአክዓብ ልጅ የሆነችው እናቱ ጎቶልያ፥ የልጅ ልጆችዋን በማጥፋት መንግሥቱን ያዘች። ነገር ግን የአካዝያስ እኅት የካህኑ የዮዳሄ ሚስት፥ ዮሳቤት፥ ሕፃኑን ኢዮአስን ከነሞግዚቱ ሸሸገችው፤ እርስዋና ዮዳሄም አሳደጉት። ሕፃኑ ሰባት ዓመት በሆነው ጊዜ ዮዳሄ ሕዝቡን ሰብስቦ አነገሠው። ጎቶልያም የሕዝቡን የደስታ ጩኸት ሰምታ ስትመጣ አውጥተው ገደሏት። እስከ ዕለተ ሞቱ ድረስ ዮዳሄ የኢዮአስ አማካሪ ነበረ። 130 ዓመት ሲሆነው ሞተ፤ ስለሠራው ውለታ ሁሉ በነገሥታት መቃብር ቀበሩት፤ 2ነገ. 11 እና 12፤ 2ዜ.መ. 22፥10-24፥16።

**ዮፍታሔ፤** ትርጉሙ «እግዚአብሔር ይከፍታል» ማለት ነው። ከእስራኤል መሳፍንት አንዱ። አንዲት ጋለሞታ ሴት ገለዓድ ለሚባለው ሰው የወለደችለት ልጅ ነበረ። የአባቱ ሚስት ልጆች ካደጉ በኋላ አባረሩት። ሽፍቶም ተከታዮችን ሰበሰበ። አሞናውያን በእስራኤል ላይ በተነሡ ጊዜ የገለዓድ ምድር አለቆች ወደ ዮፍታሔ ሄደው፥ አለቃችን ሁን አሉት። ዮፍታሔ መልእክተኞችን በመላክ የአሞንን ንጉሥ እንዲመለስ መከረው። ባልሰማውም ጊዜ አሞናውያንን በእግዚአብሔር መንፈስ ኃይል መትቶ አሸነፋቸው፤ ይህንም ያደረገው በእምነት ነበር፤ ዕብ. 11፥32። የእግዚአብሔርንም ሕግ ካለማወቁ የተነሣ (ዘዳ. 12፥29-31)፥ የተሳለውን ስለት እንዲፈጽም የሚወዳትን ሴት ልጁን ሠዋ። የኤፍሬም ሰዎች በተነሡበት ጊዜም አሸነፋቸው። ስድስት ዓመት በእስራኤል ላይ ፈራጅ ሆነ፤ መሳ. 10፥17-12፥7።

**ደመሰሰ፤** አጠፋ፤ ጽሕፈትን ሰረዘ፤ ኃጢአትን ሰረየ፤ ዘጸ. 32፥32፤ ዘዳ. 9፥14፤ መዝ. 51፥1፤ 69፥28፤ ራእ. 3፥5።

**ደመና፤** እግዚአብሔር ብዙ ጊዜ በደመና ይገለጣል፤ ዘጸ. 19፥9፤ 24፥16፤ 1ነገ. 8፥10፤ ሉቃ. 9፥34። ክርስቶስ በደመና ዐረገ (ሐ.ሥ. 1፥9)፤ በደመና ይመለሳል፤ ራእ. 1፥7። በምሳሌነት ደመና ፍርድን (ሕዝ. 30፥3)፥ አደጋን (ኢዮብ 3፥5)፥ በቶሎ የሚያልፉ ነገሮችን (ኢዮብ 7፥9፤ ኢሳ. 44፥22)፥ ኃይልን (ኢሳ. 19፥1) ሊያመለክት ይችላል።

**የደመና ዐምድ፤** እግዚአብሔር እስራኤልን ከግብጽ ሲያወጣ በምድረ በዳም ሲጓዙ በደመና ዐምድ መራቸው፤ ዘጸ. 13፥21:22፤ 33፥10፤ ዘኍ. 9፥17-23፤ 1ቆሮ. 10፥1-4።

**ደመወዝ፤** የሥራ ዋጋ። በልዩ ልዩ ዓይነት ይከፈል ነበር፤ ዘፍ. 29፥15:20፤ 30፥28-34፤ ማቴ. 20፥2። የሞያተኛ ደመወዝ ሳያድር እንዲከፈል በሕግ ታዘዘ፤ ዘሌ. 19፥13፤ ዘዳ. 24፥14-15። ሰው እንደ ሥራው ደመወዙን ሊቀበል ይገባዋል (ሉቃ. 10፥7፤ ሮም 4፥4)፥ ደመወዙንም አለመስጠት ግፍ ነው፤ ኤር. 22፥13:14፤ ሚል. 3፥5፤ ያዕ. 5፥4።

የወንጌል ሠራተኞች ከሚያገለግሉበት ደመወዝ መቀበል ይገባቸዋል (2ቆሮ. 11፥8፤ 1ጢሞ. 5፥17:18)፥ ነገር ግን ለገንዘብ ብለው እንዳያገለግሉ ተከልክለዋል፤ ሚክ. 3፥11፤ ቲቶ 1፥7፤ 1ጴጥ. 5፥2። እግዚአብሔር ለምእመናን ስለ ሥራቸው የሚሰጣቸው በደመወዝ ምሳሌ ተገልጧል፤ ሉቃ. 6፥23-35፤ 1ቆሮ. 3፥14፤ 2ዮሐ. 8። ነገር ግን ይህ እንደ ጸጋው እንጂ እንደ ሥራቸው መጠን አይደለም፤ ማቴ. 20፥1-16፤ ሉቃ. 17፥10፤ 2ቆሮ. 9፥6-11። ደግሞም ሞት የኃጢአት ውጤት በመሆኑ እንደ ደመወዝ ይቈጠራል፤ ሮም 6፥23።

**ደማስቆ፤** ሁለት ሺህ ዓመት ከክ.በ. የተሠራ እስከ ዛሬ ድረስ የሶርያ መናገሻ ከተማ የሆነ። «ቅን» የተባለው ጥንታዊ መንገድ እስከ አሁን ይገኝበታል፤ ሐ.ሥ. 9፥11። በአቅራቢያው አባናና ፋርፋ የተባሉ ሁለት ወንዞች ይፈሳሉ፤ 2ነገ. 5፥12። ከምሥራቅ ወደ ታላቁ ባሕር፥ ከሰሜንም ወደ ግብጽ የሚሄዱ

መንገዶች የሚገናኙበት ስለሆነ፥ ብዙ ነጋዴዎች የሚመላለሱበት መናኸሪያ ከተማ ነበር። አብርሃም በአቅራቢያው ይኖር ነበር፤ ዘፍ. 14፥15። እነዳዊት የደማስቆን ሰዎች ድል ነሡ፤ 2ሳሙ. 8፥5:6። በእስራኤል ታሪክ ውስጥ ስማቸው ተጽፎ የምናገኛቸው የሶርያ ገዥዎች የሚከተሉት ናቸው ፦ ሬዞን (1ነገ. 11፥23-25)፥ ወልደ አዴር (1ነገ. 15፥18)፥ አዛሄል (2ነገ. 13፥22)፥ ወልደ አዴር 2ኛ (2ነገ. 13፥24)፥ ረአሶን (2ነገ. 16፥5፤ ኢሳ. 7፥1)።

ጳውሎስ ወደ ደማስቆ ሲሄድ ሳለ ክርስቶስ ተገለጠለት፤ ወንጌልን ማስተማር በደማስቆ ጀመረ፤ ሐ.ሥ. 9። በ628 ዓ.ም. የእስልምና ሃይማኖት ተከታዮች ከተማውን ማረኩና የእስልምና ትምህርት ማስፋፊያ አደረጉት። ካ. 1ለ።

**ደም**፡ የሥጋ ሕይወት በደም ነው። ሰው ደም እንዳይበላ በሁለት ምክንያት ተከለከለ። 1. ነፍስ የእግዚአብሔር እንደሆነች እንዲያስተውል፥ 2. እግዚአብሔር ደምን ለነፍስ ማስተስረያ እንዲሆን ስለሰጠ ነው፤ ዘፍ. 9፥4፤ ዘሌ. 17፥10-14፤ ዘዳ. 12፥23። እግዚአብሔር ሰውን በመልኩ ፈጥሮታልና ደሙ ቢፈስ ደሙን ይመለከታል፤ ደም አፍሳሹንም ይበቀላል፤ ዘፍ. 4፥10፤ 9፥4-6፤ ዘኍ. 35፥33። እስራኤላውያን ከግብጽ ሲወጡ ደም ከመቅሠፍት የመዳን ምልክት ሆነላቸው፤ ዘጸ. 12፥3-27። የመሥዋዕት ደም ሲፈስ በሰው ፈንታ ሌላ እንደሞተ ያመለክታል፥ ኃጢአትም በደሙ መሠረት ይሰረያል፥ ደም ሳይፈስ ስርየት የለምና፤ ዘሌ. 5፥17-19፤ ዕብ. 9፥22። ምእመናን አንድ ጊዜ በፈሰሰው በክርስቶስ ደም ይነጻሉ፤ ኤፌ. 2፥13፤ 1ጴጥ. 1፥2:18፤ 1ዮሐ. 1፥7።

**ደም ተበቃይ**፡ የሙዋቹን ደም መበቀል የነበረበት ዘመድ፤ ዘኍ. 35፥11-34።

**ደረት**፡ ሰዎች ደረትን በመድቃት ሐዘናቸውን ይገልጡ ነበር፤ ሉቃ. 18፥13፤ 23፥48።

**ደርቤን**፡ በትንሹ እስያ በሊቃኦንያ አገር የነበረች ከተማ። ጳውሎስ እዚህ ወንጌልን ሰበከ፤ ሐ.ሥ. 14፥20-23፤ 16፥1። የጋይዮስ ከተማ ነበረች፤ ሐ.ሥ. 20፥4። አሁን ፈርሳለች። ካ. 6በ።

**ደሴት**፡ በባሕር የተከበበ መሬት፤ ኢሳ. 42፥15፤ ኤር. 2፥10። ብዙ እስራኤላውያን ወደ ደሴቶች አይሄዱም ነበርና ደሴቶች በሩቅ ያሉትን ሕዝቦች ሊያመለክቱ ቻሉ፤ ኢሳ. 41፥5፤ ሶፎ. 2፥11።

**ደስታ**፡ ከእግዚአብሔር የሚመጣ (መዝ. 104፥31፤ ዮሐ. 15፥11)፥ መንፈስ ቅዱስም በአማኝ ውስጥ የሚያፈራው ስሜት፤ ገላ. 5፥22-24። ከመከራና ከሐዘን ጋር አብሮ ሊገኝ ይችላል፤ ሐ.ሥ. 16፥23-33፤ 2ቆሮ. 6፥10፤ ያዕ. 1፥2:3፤ 1ጴጥ. 1፥8:9፤ ኢሳ. 53፤ ዕብ. 12፥1:2። በጌታ ሁልጊዜ እንድንደሰት ተነግሮናል፤ ፊል. 4፥4፤ 1ተሰ. 5፥16።

**ደቀል**፡ የሸራ መጋረጃ የሚዘረጋበት የመርከብ ምሰሶ፤ ምሳ. 23፥34፤ ኢሳ. 33፥23።

**ደቀ መዝሙር**፡ የሃይማኖት ትምህርት ተከታይ፥ ተማሪ። ደቀ መዝሙር የመሪውን አኗኗር ይከተላል። ደቀ መዛሙርት ብዙ ጊዜ ከመሪያቸው፥ ወይም ከመምህራቸው ጋር ይኖራሉ፤ ይዘዋወራሉም፤ ኢሳይያስ (ኢሳ. 8፥16)፥ መጥምቁ ዮሐንስ (ማቴ. 9፥14)፥ ፈሪሳውያን (ሉቃ. 5፥33)፥ ኢየሱስም ደቀ መዛሙርትን ያስከትሉ ነበር። ስለ ኢየሱስ « ደቀ መዛሙርት» ሲል በጠቅላላ ትምህርቱን ይከታተሉ የነበሩትን ሁሉ (ዮሐ. 6፥66)፥ ዐሥራ ሁለቱን (ማቴ. 10፥1)፥ ወይም ምእመናንን ሁሉ ሊያመለክት ይችላል፤ ሐ.ሥ. 6፥1። ምእመናን «ክርስቲያን» በሚል ስም ከመጠራታቸው በፊት ደቀ መዛሙርት ተብለው ይጠሩ ነበር፤ ሐ.ሥ. 11፥26። «ሐዋርያ» ይመ.

**ደበሎ**፡ የእረኛ ልብስ። ከበግ ቆዳ ተቀጣጥሎ ይሰፋል። ደበሎና ለምድ ተመሳሳይ ነው፤ ኤር. 43፥12፤ ማቴ. 7፥15።

**ደቡብ**፡ የሰሜን ተቃራኒ አቅጣጫ። ብዙ ጊዜ በመ.ቅ. ቃሉ ከይሁዳ በስተደቡብ የሚገኘውን ደረቅ ምድረ በዳ ያመለክታል፤ 1ሳሙ. 27፥10፤ 30፥14። አገሩ አሸዋ የሞላበት ድንጋያማ ሲሆን ዋና ከተማው ቤርሳቤሕ ነው። ዛሬ የእስራኤል መንግሥት ከገሊላ ባሕር በቦይና በቧንቧ ውሃ ስላስገባበት ለም ሆኗል።

**ደብረ ዘይት**፡ የወይራ ዛፍ ያለበት ተራራ ማለት ነው። ከኢየሩሳሌም በስተምሥራቅ ይገኛል። በደብረ ዘይትና በኢየሩሳሌም መካከል የቄድሮን ሸለቆ ይገኛል። ከቤተ መቅደስ አደባባይ ደብረ ዘይት ሰባ አምስት ሜትር ገደማ ከፍ ይላል። ዳዊት ከአቤሴሎም በሸሸ ጊዜ ወደ ደብረ ዘይት ዐቀበት ወጣ፤ 2ሳሙ. 15፥30። ቤተ ፋጌና ቢታንያ ከደብረ ዘይት ተራራ ግርጌ ናቸው፤ ኢየሱስ በሆሳዕና ዕለት ከደብረ ዘይት ወደ ኢየሩሳሌም ገባ፤ ማር. 11፥1። ኢየሱስ በደብረ ዘይት ተቀምጦ ስለ ኢየሩሳሌም መፍረስና ስለ ዓለም መጨረሻ አስተማረ፤ ማር. 13፥3። ኢየሱስ ከደብረ ዘይት ግርጌ ባለው በጌቴሴማኒ በአይሁድ ጭፍሮች ተያዘ፤ ማቴ. 26፥30:36። ኢየሱስ ከደብረ ዘይት ወደ ሰማይ ዐረገ (ሉቃ. 24፥51:52፤ ሐ.ሥ. 1፥12)፤ እንደገናም በዓለም ፍጻሜ በደብረ ዘይት ይወርዳል የሚል ትንቢት ተነግሯል፤ ዘካ. 14፥4።

**ደቦል**፡ የአንበሳ፥ የውሻ የሌላም አውሬ ልጅ፤ ግን በብዛት ትንሽ ዕድሜ ላለው አንበሳ ይነገራል፤ መሳ. 14፥5። ይሁዳና ዳን በአንበሳ ደቦል ተመስለዋል፤ ዘፍ. 49፥9፤ ዘዳ. 33፥22። የአንበሳ ደቦል ለነገሥታት ልጆች ሁሉ ምሳሌ ሆኖ ተጠቅሷል፤ ሕዝ. 19፥1-9።

**ደግነት**፡ በሥጋ ሆነ በመንፈስ ከማንኛውም ዓይነት ክፋትና ጉዳት መዳን ማለት ነው። 1. በክርስትና ሃይማኖት ሰው የእግዚአብሔርን ከፍተኛ በረከት እንዳይቀበል ከሚከለክለው ነገር ሁሉ

የሚድንበት ጠቅላላ ሥራ፤ 2. የእግዚአብሔርን በረከት መቀበልና በእርሱ መደሰት ነው።

በብ.ኪ. እግዚአብሔር ሕዝቡን ከልዩ ልዩ ነገር አዳናቸው። ለምሳሌ በጦርነት ጊዜ ከመሸነፍ ያድናቸው ነበር (ዘጸ. 15፥2)፤ ከችግር (መዝ. 34፥6)፣ ከጠላቶቻቸው (2ሳሙ. 22፥18)፣ ከግፍ (2ሳሙ. 22፥3)፣ ከነቀፋ (መዝ. 57፥3)፣ ከምርኮኝነት (መዝ. 106፥47)፣ ከሞት (መዝ. 6፥4)፣ ከኃጢአት (ሕዝ. 36፥29) እና ከባርነት ያድናቸው ነበር (ዘጸ. 3፥7:8)። ያዳናቸው እግዚአብሔር ስለሆነ መድኃኒት ተብሎ ይጠራል፤ ኢሳ. 43፥3:11:12፤ ኤር. 14፥8። በብ.ኪ. ሰው ደኅንነትን እንዲቀበል በእግዚአብሔር በፍጹም እምነት መታመን ያስፈልገው ነበር፤ መዝ. 86፥2። ደግሞ ሕጉን መጠበቅና ከኃጢአት ተመልሶ መሥዋዕትን ማቅረብ ያስፈልግ ነበር፤ ዘዳ. 30፥2:3፤ ዘሌ. 4፥1-4፤ ምሳ. 28፥13። ደኅንነት ለአሕዛብ ጭምር እንደሚሰጥ እግዚአብሔር በቃሉ ገለጸ፤ ኢሳ. 49፥5:6፤ 55፥1-5።

በአ.ኪ. ደኅንነት ማለት ከብዙ ዓይነት ነገር መዳን ማለት ቢሆንም (ማቴ. 14፥30፤ ማር. 5፥34፤ ሐ.ሥ. 27፥31-44)፣ አብዛኛውን ጊዜ አዲስ ሕይወትን መቀበልና ከኃጢአት መዳን ማለት ነው። ይህም ሥጋ በለበሰው በእግዚአብሔር ልጅ በማመን የሚገኝ ነው፤ ዮሐ. 3፥16። ክርስቶስ በሕማማቱ፣ በሞቱና በትንሣኤው ደኅንነትን አስገኘልን፤ ሮም 4፥24:25፤ ኤፌ. 2፥13-18። ደኅንነት ከሚመጣው ፍርድ መዳን ብቻ ሳይሆን በሕይወት ሳሉ ከኃጢአት ኃይል መዳን ነው፤ ሮም 6። በክርስቶስ የሚያምን ሰው ብዙ የደኅንነት በረከት ይቀበላል። የእግዚአብሔር ልጅ ይሆናል (ዮሐ. 1፥12)፣ ከኃጢአት ይለያል (ሮም 6፥2፤ ገላ. 5፥24)፣ አዲስ ፍጥረት ይሆናል (2ቆሮ. 5፥17)፣ ከሕግ ባርነት አርነት ይወጣል (ሮም 6፥14፤ 7፥6፤ ገላ. 5፥1:13:18)፣ ለክርስቶስ የተለየ ገንዘብ ይሆናል (ቲቶ 2፥14)፣ ከኃጢአት ይነጻል (ይጸድቃል፤ ሐ.ሥ. 13፥38:39)፣ ይከብራል (ሮም 8፥30)፣ ይቀደሳል (1ቆሮ. 6፥11)።

በእግዚአብሔር በኩል ደኅንነት የሚገኘው በጸጋ ብቻ ነው፤ ኤፌ. 2፥8:9። እግዚአብሔር ደኅንነቱን ለሚቀበለው ለማንኛውም ሰው ይሰጣል፤ ዮሐ. 3፥16፤ 2ጴጥ. 3፥9። ክርስቶስ ለሕዝቡ ያዘጋጀው ደኅንነት የሚፈጸመው ምእመናን የሥጋን ትንሣኤ ከተቀበሉ በኋላ ነው፤ ኤፌ. 4፥30፤ 1ቆሮ. 15፥42-58፤ 1ጴጥ. 1፥3-5። በተጨማሪም ፍጥረት ራሱ በቃጠሎ አልፎ ይታደሳል፤ 2ጴጥ. 3፥8-14፤ ሮም. 8፥18-23።

**የማይጠፋ ዘለዓለማዊ ደኅንነት፤** ሰው ከመንፈስ ቅዱስ ከተወለደ፣ በልቡም ካመነ በኋላ ለዘለዓለም ይኖራል። በመጀመሪያ ማስተዋል የሚገባን ደኅንነት ከእግዚአብሔር እንደሆነ የሚቀጥሉት አሳቦች በትኩረት የሚያስገነዝቡ መሆናቸውን ነው።

1. ሰው የሚድነው በእግዚአብሔር ጸጋ ነው፤ ሮም 8፥29:30፤ 9፥16፤ ኤፌ. 2፥8።

2. እግዚአብሔር በሰው ልብ የሚዘራው ዘር የማይጠፋ ነው፤ 1ጴጥ. 1፥23።

3. አማኝ የእግዚአብሔር ልጅ ስለሆነ እግዚአብሔር መንግሥቱን ያወርሰዋል፤ ፊል. 1፥6፤ 2ጢሞ. 1፥12፤ 1ጴጥ. 1፥3-5።

4. ክርስቶስ ለተከታዮቹ የሚሰጠው ሕይወት የዘለዓለም ሕይወት ነውና ማንም ከእጁ ሊነጥቃቸው አይችልም፤ ዮሐ. 10፥27:28።

5. አማኙ በኃጢአት ቢወድቅም እግዚአብሔር በንስሐ ያነሣዋል፤ ሰ.ኤ. 5፥21፤ ሆሴዕ 14፥4፤ ዕብ. 12፥5:6። ስለዚህ አማኙ በእግዚአብሔር ኃይል እስከ መጨረሻ ይጸናል፤ የጽድቅ አክሊልንም ይቀበላል፤ ማቴ. 24፥13፤ 2ጢሞ. 4፥8።

ሰው ከመንፈስ ቅዱስ ከተወለደ በኋላ ሊጠፋ አይችልም የሚለውን ትምህርት የማይቀበሉ ሰዎች በተለይ ሁለት ማስተባበያ ምክንያቶችን ያቀርባሉ ፦ (ሀ) ሰው ወንጌልን እንዳይክድ፣ እስከ መጨረሻም እንዲጸና ብዙ ማስጠንቀቂያዎች አሉ፤ ማቴ. 24፥12-13፤ 1ቆሮ. 9፥27፤ ቆላ. 1፥23፤ ዕብ. 2፥1፤ 3፥14። የሚያምኑና የአማኝን አለመጥፋት የሚቀበሉ ግን እነዚህ ጥቅሶች አማኝ ራሱን እንዲመረምርና እንዲቈጣጠር ይቀሰቅሱታል እንጂ ሊጠፋ እንደሚችል አያስተምሩም ይላሉ። (ለ) አንዳንድ ሰዎች ካመኑ በኋላ እንደጠፉ እናነባለን የሚሉ አሉ፤ 1ጢሞ. 1፥19:20፤ 2ጢሞ. 4፥10፤ 2ጴጥ. 2፥1:2፤ ዕብ. 6፥4-6። የአማኙን አለመጥፋት የሚቀበሉ ግን እንደሚከተለው መልስ ይሰጣሉ። እነዚህ ሰዎች እውነተኛ እምነት እንደነበራቸው አናውቅም። ወንጌልን የሚያውቁና የሚሰብኩ፣ ነገር ግን በእውነት ከልብ የማያምኑ ለእግዚአብሔር የማይታዘዙ ከቤ.ክ. አይጠፉም፤ ማቴ. 7፥21-27፤ ሮም 9፥6፤ 1ዮሐ. 2፥9፤ ራእ. 3፥1። ሐዋርያው ዮሐንስ ስለ እነዚህ ሰዎች «ከእኛ ወገን አልነበሩም» ብሏል፤ 1ዮሐ. 2፥19። እንግዲህ ሰው የክርስቶስን ፈቃድ በመፈጸም እምነቱ እውነተኛ እምነት መሆኑን ማረጋገጥ ይገባዋል፤ ማቴ. 7፥20-21፤ 25፥31-46፤ ገላ. 5፥6፤ 1ዮሐ. 2፥5። ከዚያም በኋላ ክርስቶስ እስከ መጨረሻ እንደሚያደርሰው ያውቃል፤ ዕብ. 7፥25። «ቅዱስ»፣ «ቤዛ»፣ «መመለስ»፣ «ጽድቅ» ይመ.

**ደንቈሮ (ደንቆሮ)፤** የማይሰማ፤ ዘጸ. 4፥11፤ ዘሌ. 19፥14፤ ማቴ. 11፥5፤ ማር. 7፥32፤ 9፥25። የእግዚአብሔርን ቃል ለማይቀበልና ለማያስተውል ምሳሌ ነው፤ መዝ. 38፥13፤ ኢሳ. 42፥18። «በሽታ» ይመ.

**ደንገል፤** በባሕር ዳርና በረግረግ ቦታ የሚበቅል ሦስት ረድፍ ያለው፣ ቄጠማን የሚመስል፣ ለታንኳ ሥራ የሚሆን ወፍራም ሣር፤ ዘጸ. 2፥3፤ ኢዮብ 8፥11። ሥዕሉን በገጽ 230 ይመ.

**ደንገጥር፤** ትልቅ ሴትን የምትከተልና የምታገለግል ሴት ወይዘር፤ ዘጸ. 2፥5፤ አስ. 4፥4:16።



የደንገል ተክል

**ደዌ**፦ ማናቸውም ዓይነት በሽታ፤ ማቴ. 4፥24፤ ማር. 1፥34። «በሽታ» ይመ.

**ደጅ**፦ መግቢያ፤ በአ.ኪ. ደጅ ማለት ክርስቶስ ወደ ሰው ሕይወት የሚገባበትን፣ ወንጌልንም የመቀበልና የማስተማርን ዕድል ሊያመለክት ይችላል፤ ራእ. 3፥20፤ ማቴ. 25፥10፤ ሐ.ሥ. 14፥27፤ ቆላ. 4፥3።

**ደጋሚ**፦ በድግምት የሚጠነቁል፣ የተወሰኑ ቃላትን ይደግማል፤ አንድ ነገር እንዲሆን ወይም እንዳይሆን አደርጋለሁ ይላል፤ ዘዳ. 18፥11። «ጥንቈላ» ይመ.

**ደጎብያ**፦ «አንበጣ» ይመ.

**ደፍ**፦ የላይና የታች ጉበን። ሳንቃ የሚቆምበት ከመሬት ላይ ያለው ጥርብ እንጨትና በላይ በኩል ሳንቃው የሚጋጠምበት እንጨት ደፍ ይባላል፤ 1ነገ. 6፥31።

**ዱሪ**፦ ጥቍር። የፈረስ መልክ ዓይነት መግለጫ ነው፤ ዘካ. 6፥2።

**ዱር**፦ በዱሮ ዘመን በእስራኤል ተራራዎች ላይ ብዙ ዛፎች ነበሩ፤ ሰሎሞን ለቤተ መቅደስ መሥሪያ የሚሆን ዝግባና ጥድ ከሊባኖስ ዱር አስመጣ፤ 1ሳሙ. 22፥5፤ 2ነገ. 19፥23።

**ዱር ጠባቂ**፦ የደን ሀብት ጠባቂና ተቈጣጣሪ፤ ነህ. 2፥8።

**ዱቄት**፦ የተፈጨ እህል፤ ዘሌ. 2፥2፤ 1ሳሙ. 28፥24፤ ማቴ. 13፥33፤ «ወፍጮ» ይመ.

**ዲቃላ**፦ ከጋብቻ ውጭ የተወለደ (የልጅነት መብት የሌለው)፤ ዘዳ. 23፥2፤ ዕብ. 12፥8።

**ዲብ**፦ የመሬት ከፍታ። እንደ ተራራ ሳይሆን የዐፈርና የአሸዋ ቁልል የበዛበት ማለት ነው፤ ሐ.ሥ. 27፥41።

**ዲቦራ**፦ ትርጕሙ «ንብ» ማለት ነው። የለፊዶት ሚስት፣ የእስራኤል ነቢይትና ዳኛ። በጦርነት ጊዜ በጦር አዝማችነት፣ በሰላምም ጊዜ በፈራጅነት እስራኤልንና እግዚአብሔርን ያገለግሉ ከነበሩት መሳፍንት ዲቦራ አንዷ ነበረች። ኢያቢስ የተባለው የከነዓናውያን ንጉሥ እስራኤልን ባስጨነቀ ጊዜ ወደ አምላካቸው ጮኹና በዲቦራ አማካይነት ከእግዚአብሔር ዘንድ ረድኤትን አገኙ። ነቢይቱ ባርቅ የተባለውን ሰው አነሣሥታ፣ ሲሣራ የተባለውን የኢያቢስን የሠራዊት አለቃ በጦርነት እንዲገጥመው አደፋፈረችው። ባርቅም ፦ አንቺ ከእኔ ጋር ብትሄጂ እሄዳለሁ፣ ባትሄጂ ግን አልሄድም ቢላት አብራው ሄደች። ጠላትም በእግዚአብሔር ኃይል ተሸነፈ፤ መሳ. 4። እግዚአብሔር በባርቅና በዲቦራ አገልግሎት እስራኤልን ድል አድራጊ ካደረገው በኋላ፣ ዲቦራ በመጽሐፈ መሳፍንት በምዕራፍ 5 ላይ የሚገኘውን የምስጋና መዝሙር ለእግዚአብሔር ክብር ዘመረች።

**ዲና**፦ ትርጕሙ «ፈረደ» ማለት ነው። ልያ የወለደችለት የያዕቆብ ሴት ልጅ፤ ዘፍ. 30፥21፤ 46፥15። ሴኬም ዲናን ስላስነወረ ወንድሞቿ የሴኬምን ሰዎች ገደሉ፤ ዘፍ. 34።

**ዲናር**፦ የሮም መንግሥት የብር ምንዛሪ፤ ማቴ. 20፥2፤ ማር. 12፥15-17፤ ሉቃ. 10፥35። «ገንዘብ» ይመ.





የሮም ዲናር፤ በ1ኛው ገጽ «አውግስጦስ ቄሣር»፣ በሌላው «ታላቁ ገዥ»

**ዲን (ድኝ)**፦ ከእሳተ ገሞራ ዙሪያ የሚገኝ ብጫ ዓይነት ዐፈር። ሰውን የሚያስቅቅ ጢስ እያወጣ ይነዳል። ከዚህም የተነሣ የፍርድ ምሳሌ ነው፤ ዘፍ. 19፥24፤ መዝ. 11፥6፤ ኢሳ. 30፥33፤ ሕዝ. 38፥22፤ ራእ. 9፥17።

**ዲዮስቆሮስ**፦ እንደ ግሪክ ታሪክ መርከበኞችን የሚረዱ የግሪክ አምላክ የዜውስ ልጆች ስም፤ ሐ.ሥ. 28፥11።

**ዲያቆን**፦ አገልጋይ ማለት ነው። ለድሆች በትክክል እርዳታ ለማዳረስ፣ በማዕድም ለማገልገል ሰባት ሰዎች በኢየሩሳሌም ቤ.ክ. ተመርጠው ነበር። ዲያቆናት ተብለው ባይጠሩም፣ ይህ ሥራ የዲቁና ሥራ ነውና ብዙ ጊዜ ሰባቱ ዲያቆናት ይባላሉ፤ ሐ.ሥ. 6፥1-6። በኋላም እየቆየ ዲቁና በቤ.ክ. እንደ አንድ ማዕረግ ሆነ። ጳውሎስም ስለ ዲያቆናት ጠባይና ስለ ዲቁና ሥራ ክብር ጽፏል፤ 1ጢሞ. 3፥8-13።

ሴቶችም በቤተ ክርስቲያን አገልግለዋል (ሮም 16፥1)፥ ነገር ግን የዲቁና ማዕረግ ተሰጥቷቸው እንደነበር በመ.ቅ. አልተጻፈም። «የቤተ ክርስቲያን አስተዳደር» ይመ.

**ዲያብሎስ፤** ሰይጣን የዕብራይስጥ ቃል ሲሆን፥ ዲያብሎስ የግሪክ ቃል ነው። ስለዚህ ዲያብሎስ የሚለው ቃል በአ.ኪ. እንጂ በብ.ኪ. አይገኝም። «ሰይጣን»፥ «መልአክ» ይመ.

**ዲዳ፤** ለመናገር የማይችል፤ ዘጸ. 4፥11፤ ሉቃ. 1፥20፤ ማቴ. 9፥32:33፤ 12፥22፤ ማር. 9፥25። ጠቃሚ ነገርን ለማይናገር ምሳሌ ነው፤ ኢሳ. 56፥10። «በሽታ» ይመ.

**ዲድስቅልያ፤** ዲድስቅልያ ማለት ትምህርት ማለት ነው። መጽሐፈ ዲድስቅልያ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤ.ክ. በሐዋርያት ተጽፏል ብላ ከአዲስ ኪዳን መጻሕፍት ጋር ቈጥራ የምትቀበለው በ43 ምዕራፎች የተከፈለ የቤ.ክ. ሥርዓት ትምህርት መጽሐፍ ነው።

**ዳሌ፤** የወገብና የጭን መጋጠሚያ አካል፤ መ.መ. 7፥2።

**ዳማ፤** ደም የሚመስል ቀይ። የፈረስ መልክ መግለጫ ነው፤ ራእ. 6፥4።

**ዳረገ፤** የተወሰነ ስጦታ፥ ለምሳሌ ቀለብ፥ ገንዘብ፥ መሬት ሰጠ ... ወዘተ ማለትን ያሳያል፤ 1ነገ. 11፥18።

**ዳሪክ፤** የፋርስ መንግሥት የወርቅ ገንዘብ፤ ዕዝ. 2፥69።

**ዳርዮስ፤** ዳርዮስ በሚለው ስም የተጠሩት ሦስት ሰዎች ተጠቅሰው ይገኛሉ ፦

1. ሜዶናዊው ዳርዮስ። የአሕሻዊሮስ ልጅ፤ ዳን. 5፥31፤ 9፥1። ይህ ሰው በንጉሥ ቂሮስ ዘመነ መንግሥት ውስጥ የኖረ፥ በባቢሎንም ላይ ገዥ ይሆን ዘንድ ቂሮስ የሾመው ነው ተብሎ ታስቧል። ይሁን እንጂ ከቂሮስ በታች ሆኖ ባቢሎንን ያስተዳደረው ለአጭር ጊዜ ብቻ ይመስላል፤ ዳን. 10፥1፤ 11፥1። ዳንኤልን ወደ አንበሶች ጕድጓድ የጣለው ይህ ገዢ ነበረ፤ ዳን. 6፥1-28።



2. ዳርዮስ የሂስታስጴስ ልጅ። ዘመነ መንግሥቱ 521-486 ከክ.በ. ነበረ። ከፋርስ ነገሥታት መካከል በኃያልነት፥ በክብርም የአንደኛነትን ማዕርግ ያገኘ ይህ ንጉሥ ነው። የመንግሥቱን ግዛት ያስፋፋ፥ አስተዳደሩንም ያሻሻለ ከመሆኑም በላይ በየአገሩ ብዙ ደማቅ ሕንፃዎችን በማቋቋሙ ስመ ጥርነትን አትርፏል። በቂሮስ ፈቃድ ከባቢሎን ምርኮ የተመለሱት አይሁድ የቤተ መቅደሱን ሥራ መጀመራቸው ይታወሳል። ግን ተቃዋሚዎች ስለተነሡባቸው፥ ሥራው ለረጅም ጊዜ ተቋረጠ። ይሁዳ ከፋርስ ግዛቶች አንዱ በመሆኑ ንጉሥ ዳርዮስ ጕዳዩን ተመልክቶ በመደገፍ ሥራው እንዲቀጥል ንጉሣዊ ትእዛዝ አስተላለፈ። ሥራውም ከፍጻሜ ደረሰ፤ ዕዝ. 4፥5፤ 5፥5-7፤ 6፥1-12፤ ሐጌ. 1፥1፤ 2፥1:10። ዳርዮስ በ486 ዓመት ከክ.በ. በሞት ከዚህ ዓለም በተለየ ጊዜ፥ ዘርክሲዝ የተባለው የቂሮስ የልጅ ልጅ መንግሥቱን ወረሰ።



የፋርስ ንጉሥ ቀዳማዊ ዳርዮስ ዙፋን ላይ እንደተቀመጠ (በሱሳ ከድንጋይ ቅርጽ የተገኘ)

3. ዳርዮስ ፋርሳዊው (ነሀ. 12፥22)፥ ወይም ኩዶማኑስ የተባለው ከ336-330 ከክ.በ. የነገሠ የፋርስ መንግሥት የመጨረሻው ንጉሥ። በ330 ከክ.በ. ታላቁ እስክንድር በጦርነት አሸንፎት መንግሥቱን ወረሰ።

**ዳስ፤** ከልዩ ልዩ ዛፎችና ቅጠሎች የሚሠራ ጊዜያዊ ቤት። አይሁድ ዓመታዊ በዓል በዳስ ያከብራሉ፤ ዘዳ. 16፥13:16፤ ነሀ. 8፥14-17።

**ዳታን፤** ከነገደ ሮቤል የሆነ፥ ከቆሬና ከአቤሮን ጋር በመተባበር በሙሴና በአሮን ላይ የተነሣ ሰው። የእስራኤል ልጆች በምድረ በዳ በነበሩበት ጊዜ ዳታንና

ወንድሙ አቢሮን ከሌዋዊው ቆሬ ጋር ሆነው በምቀኝነት በሙሴና በአሮን ላይ በመነሣት ለአሮን ብቻ የተሰጠውን የክህነት አገልግሎት ለራሳቸው ተመኙ። በእግዚአብሔር አገልጋዮች ላይ በመነሣታቸው የእግዚአብሔርን ቅዱስ ፈቃድ ሲቃወሙ ተገኙና እግዚአብሔር ቀሠፋቸው።

እነርሱና ቤተሰቦቻቸው ከሙሴ የእግዚአብሔርን ቃል ለመስማት ተሰብስበው ሳሉ የቆሙባት ምድር በድንገት አፏን ከፍታ አጥፊዎቹን ከነቤተሰባቸው፥ የቤት ዕቃቸውንም ጥምር ዋጠች። በሕይወታቸው ተቀበሩ፤ ዘኁ. 16፥1-35፤ ዘዳ. 11፥6፤ መዝ. 106፥16-17።

**ዳን፤** ትርጕሙ «ዳኛ» ማለት ነው። ያዕቆብ ባላ ከተባለችው ከራሔል ባሪያ የወለደው ልጅ፤ ዘፍ. 30፥6። ከእስራኤል ነገዶች የአንዱ አባት ሆነ፥ በስሙም ነገደ ዳን ተብሎ ተሰየመ። ዳን አንድ ልጅ ብቻ ከመውለዱ በስተቀር ስለ ሕይወት ታሪኩ የምናውቀው ነገር የለም፤ ዘፍ. 46፥23። ያዕቆብን በእባብ፥ ሙሴንም በአንበሳ መሰሉት፤ ዘፍ. 49፥17፤ ዘዳ. 33፥22። የእስራኤል ልጆች የከነዓንን አገር ወርሰው በተካፈሏት ጊዜ ነገደ ዳን በይሁዳና በታላቁ ባሕር መካከል ርስት አገኘ፤ ካ.3ሰ። ድርሻቸው ከሁሉም አነስተኛ ቢሆንም የተቀመጡበት አገር የተፈጥሮ ሀብት ያለው ነበረ። ከንግድም ዓሣ ከማጥመድም ገቢ ገንዘብ ይገኝ እንደነበረ ይታመናል፤ ነገር ግን በአካባቢአቸው ይኖሩ የነበሩ አሞራውያን የዳንን ሰዎች ያስቸግሯቸው ስለነበር፥ ስድስት መቶ የሚያህሉ ሰዎች ርስታቸውን ለቅቀው ሌላ አገር ለመፈለግ ወደ ሰሜን ተጓዙ። በዚያም ሌሳ የተባለችውን ከተማ ወርረው በማቃጠል መልሰው



የናቡከደነፆር ሕልም

ከሠሯት በኋላ ዳን ብለው ሰየሟት፤ ኪ.3ለ፤ መሳ. 18፥11-29። ከእስራኤል ከተማዎች በሰሜን የሚገኘው ዳን የመጨረሻው ስለነበረ እስራኤላውያን «ከዳን እስከ ቤርሳቤህ» ሲሉ አገሩ በሙሉ ማለታቸው ነበር፤ መሳ. 20፥1። ከመሳፍንት አንዱ ሶምሶን ከዳን ወገን የተወለደ ነበር፤ መሳ. 13፥2።

**ዳንኤል**፤ ትርጉሙ «እግዚአብሔር ፈራጅ ነው» ማለት ነው። ነቢዩ ዳንኤል በይሁዳ አገር ከንጉሣዊ ወይም ከመሳፍንት ቤተሰብ የተወለደ ይመስላል። ብዙ ችሎታም ነበረው። 605 ከክ. በ. ናቡከደነፆር ዳንኤልንና ሌሎችን ወደ ባቢሎን ወሰደ። በዚያም ዳንኤል ብልጣሶር ተባለ፤ የከለዳውያንንም ትምህርትና ቋንቋ ተማረ፤ ዳን. 1፥1-7። ዳንኤል እግዚአብሔርን አልረሳምና እንዳይረክስ በልቡ አሰበ፤ እንዳሰበም ሆነለት፤ ዳን. 1፥8-16። ተምሮም በባቢሎን ተሾመ፤ ዳን. 1፥17-21። ዳንኤል እስከ 536 ከክ.በ. ናቡከደነፆርን፥ ብልጣሶርን፥ ዳርዮስንና ቂሮስንም በማስተማር፥ ሕልምን በመፍታት፥ ጽሑፍንም በመተርጐም አገለገለ። ለእግዚአብሔርም ሕዝብ እየጸለየ ብዙ ራእይ አየ። ዳንኤል ጣዖት ባለማምለኩ በአንበሳ ጕድጓድ ተጣለ፥ እግዚአብሔር ግን አዳነው። ዳንኤል በመልካም አካሄዱ የታወቀ ሰው ነበር፤ ሕዝ. 14፥14:20።

**የዳንኤል ትንቢት**፤ ዳንኤል የተረጐማቸው ሕልሞችና ያያቸው ራእዮች ብዙ ምሥጢር ያለባቸው ናቸውና ሊቃውንት በአተረጓጐማቸው አይስማሙም። ዋና የትንቢቱ ዓላማ ግን በመጨረሻ እግዚአብሔርና ሕዝቡ እንደሚያሸንፉ ለመግለጥ ነው። ትንቢቱ የሚመለከታቸው በዓለም ታሪክ የተፈጸሙ ድርጊቶች በአከፋፈሉ ውስጥ በአጭሩ ተገልጠዋል።

አከፋፈል ፦

ም.1 የዳንኤል ወደ ባቢሎን መማረክና መሾም።

ም.2 ዳንኤል አንደኛውን የናቡከደነፆርን ሕልም መተርጐሙ፤ ሥዕል ይመ.

ም.3 ሲድራቅ፥ ሚሳቅና አብደናጎ በእሳት እቶን መጣላቸውና መዳናቸው።

ም.4 ዳንኤል ሁለተኛውን የናቡከደነፆርን ሕልም መተርጐሙና የሕልሙ ፍጻሜ።

ም.5 ዳንኤል በግድግዳ ላይ ስለ ብልጣሶር የተጻፈውን ቃል መተርጐሙና የቃሉ ፍጻሜ።

ም.6 ዳንኤል ዳርዮስን እያገለገለ በአንበሳ ጕድጓድ መጣሉና መዳኑ።

ም.7 በም. ሁለት የተገለጡት አራት መንግሥታት በአራት አራዊት መመሰላቸው። ግዛትና መንግሥት የሰው ልጅ ለሚመስል (ለክርስቶስ) መሰጠቱ።

ም.8 አውራ ፍየል (ግሪክ) አውራውን በግ (ፋርስን) ማሸነፉ። የአውራው ፍየል ታላቅ ቀንድ (እስክንድር) ይሰበራል፤ አራት ቀንዶች (ከእስክንድር በኋላ የተነሡ አራት መንግሥታት) ይወጣሉ። ከመካከላቸው ራሱን ከፍ ከፍ የሚያደርግ ትንሽ ቀንድ በመቃብያን ዘመን ቤተ መቅደስን ያረከሰ አንጥያኮስ ይጠፋል።

ም.9 ዳንኤል ከምርኮ ስለ መመለስ መጸለዩ። መሲሕ እስከሚመጣ ሰባ ሱባዔ እንደሚያልፍ ትንቢት መናገሩ።

ም.10-12 ከታላቁ እስክንድር በኋላ በሶርያና በግብጽ መንግሥታት መካከል ስለሚደረገው ጦርነት፥ ስለ እግዚአብሔርም ሕዝብ መከራ ትንቢት መናገሩ።

**ዳኛ**፤ ፈራጅ። በብ.ኪ. ዘመን ነገሥታት፥ መሳፍንት፥ አለቆች፥ የቤተሰብ አባቶችና የከተማ ሽማግሌዎች ፍርድ ይሰጡ ነበር። ሙሴ ዮቶር እንደ መከረው ዳኞችን በእስራኤል ላይ ሾመ፤ ዘጸ. 18፥13-26፤ ዘዳ. 1፥9-17። እነሳሙኤል በታማኝነት ይፈርዱ ነበር፤ ብዙዎች ግን ፍርድን ያጣምሙ ነበር፤ 1ሳሙ. 8፥1-3፤ 12፥1-5፤ ኢሳ. 1፥23፤ አሞጽ 5፥12፤ ሉቃ. 18፥1-6። በመጨረሻ ሰዎች ሁሉ እውነተኛ ፈራጅና የሁሉ ዳኛ በሚሆን በእግዚአብሔር ፊት ይቆማሉ፤ 2ጢሞ. 4፥8፤ ዕብ. 12፥23፤ ያዕ. 5፥9።

**ዳካ**፤ ከብርና ከወርቅ ከሌላም የሚሠራ ጕድጓዳ ሳሕን። በብ.ኪ. በቤተ መቅደስ መገልገያ ዕቃ ነበረ፤ ዕዝ. 1፥10፤ ዘኍ. 14፥20። የከብር ዕቃ ሆኖ ታላላቅ ሰዎች እንዲጠጡበት ይቀርባል፤ መሳ. 5፥25።

**ዳዊት**፤ ከእስራኤል ነገሥታት ሁሉ ታላቅና ተወዳጅ የሆነ ንጉሥ። ዘመነ መንግሥቱ ከ1011-971 ከክ.በ. ነበረ ተብሎ ይገመታል። በእስራኤል ስሙ የገነነ ንጉሥ እንደመሆኑ መጠን በመ.ቅ. ታሪኩ ረጅም ስለሆነ፥ በ1ሳሙ. ም. 16 ተጀምሮ እስከ 1ነገ. ም. 2 ድረስ ይደርሳል። በ1ዜ.መ. ምዕራፍ 11-29 ተመሳሳዩ ታሪክ ተጽፎ ይገኛል።

ዳዊት በይሁዳ በቤተ ልሔም አገር እሴይ ከተባለ ሰው ተወለደ፤ 1ሳሙ. 16፥10-11። ከእሴይ ልጆች መካከል የሁሉም ታናሽ ሆኖ የአባቱን በጎች በመጠበቅ በእረኝነት የልጅነት ዘመኑን አሳለፈ፤ 1ሳሙ. 16፥11፤ 17፥34-36። በንጉሥ ሳኦል ቦታ ተተክቶ የእስራኤል ንጉሥ ይሆን ዘንድ በሳሙኤል እጅ ተቀባ፤ 1ሳሙ. 16፥13። ዙፋኑን ከመውረሱ በፊት ግን ለሳኦል ጋሻ ጃግሬው በመሆን ያገለግለው ነበር። ሳኦልንም ለማስደሰት በፊቱ በገና ይደረድር ነበር፤ 1ሳሙ. 16፥18-23።

በእግዚአብሔር ስምና ኃይል ጎልያድ የተባለውን ፍልስጥኤማዊ በወንጭፍ ድንጋይ ገደለ፤ 1ሳሙ. 17፥45-51። ይህንን ጀብዱ በመሥራቱ በሕዝቡ ዘንድ ተወዳጅነትን አተረፈ። ነገር ግን በዚሁ መጠን ንጉሥ ሳኦል ምቀኛ ሆነበትና ዳዊትን ሊገድለው ፈለገ። የሳኦል ልጅ ዮናታን ግን ይወደውና ይረዳው ነበር። ነፍሱን ለማዳን ከንጉሡ ፊት ሸሽቶ በፍልስጥኤማውያን መካከል በስደተኝነት ተቀመጠ፤ 1ሳሙ. 20፤ 21። ወደ ዓዶላምም ዋሻ ኰብልሎ ተደበቀ፤ 1ሳሙ. 22፥1።

በምድረ በዳ ሳለ 400 የሚያህሉ ሰዎች ተከታዮቹ ሆኑ። ለእነርሱም የጦር አለቃ በመሆን የእስራኤልን ጠላቶች ይወጋ ነበር፤ 1ሳሙ. 23።

ንጉሥ ሳኦል በፍልስጥኤማውያን ወረራ መካከል በጊልቦዓ ተራራ ላይ በራሱ እጅ ከሞተ በኋላ ዳዊት

አስቀድሞ በይሁዳ፥ በኋላም በመላ እስራኤል ላይ ንጉሥ ሆነ፤ 2ሳሙ. 2-4፤ 5፥1-5።

ንጉሥ ዳዊት በዘመነ መንግሥቱ ልዩ ልዩ ታላላቅ ሥራዎችን በማከናወኑ በስመ ጥሩነት ተወዳዳሪ የሌለው ንጉሥ ሆኗል። ከሥራዎቹ ጥቂቶቹ ቀጥሎ በሚገኘው ዝርዝር ተጠቅሰዋል ፦

ሀ) ከመሳፍንት ዘመን ጀምሮ እስራኤልን ሲያጠቁት የኖሩትን ፍልስጥኤማውያን አሸንፎ ጸጥ አደረጋቸው፤ 2ሳሙ. 5፥18-25።

ለ) በደቡብ፥ በምሥራቅና በሰሜን የእስራኤል ጎረቤት የሆኑትን ሕዝቦች በማስገበር የመንግሥቱን ድንበሮች በሁሉም በኩል በማስፋት መንግሥቱን ከመጠን በላይ ትልቅ አደረገው፤ 2ሳሙ. 8፤ 12፥26-31።

ሐ) ኢያቡሳውያንን በማሸነፍ ኢየሩሳሌም የተባለችውን የተመሸገች ከተማ ወርሮ የመንግሥቱ መናገሻ ከተማ አደረጋት። የዳዊትም ከተማ ተባለች፤ 2ሳሙ. 5፥1-10።

መ) ኢየሩሳሌም ለሕዝቡ ሁሉ መንፈሳዊ መሰብሰቢያ ስፍራ ትሆን ዘንድ ታቦቱን ከነበረበት ቦታ አምጥቶ በተተከለለት ድንኳን አኖረው። የመቅደሱንም ሥነ ሥርዓት አሻሻለ፤ 2ሳሙ. 6፤ 1ዜ.መ. 15፥16፤ 25። ቤተ መቅደስ ለመሥራት ፈለገ ግን እግዚአብሔር ከለከለው፤ 1ዜ.መ. 28፥3።

ሠ) ብዙዎች መዝሙራትን ጻፈ። በመ.ቅ. «የዳዊት መዝሙር» የሚለው ርእስ ያላቸው መዝሙራት 73 ናቸው።

ዳዊት ታላቅና ገናና ንጉሥ ከመሆኑ የተነሣ በመ.ቅ. መንግሥቱ የመሲሕ መንግሥት ምሳሌ ሆኗል። መሲሑም ራሱ ብዙ ጊዜ በዳዊት ስም ተጠቅሶ ይገኛል፤ 2ሳሙ. 7፥8-17፤ ኢሳ. 9፥7፤ ኤር. 23፥5-6፤ 33፥14-17፤ ሕዝ. 34፥23፤ 37፥24፤ ሆሴዕ 3፥5። በአ.ኪ. ኢየሱስ የዳዊት ልጅ በሚለው ስም የሚጠራው በዚህ ምክንያት ነው፤ ማቴ. 9፥27፤ 12፥23። በትውልድ መጽሐፉም ላይ ከዳዊት ቤትና ወገን የተወለደ መሆኑ ተነግሮለታል፤ ማቴ. 1፥1።

ነገር ግን ከፍ ብለው በተዘረዘሩት ምክንያቶች ሁሉ ንጉሥ ዳዊት ክብርን የተጐናጸፈ ንጉሥ ቢሆንም፥ አንዳንድ ጊዜ በሚያሳዝን ኃጢአት መውደቁ ተጽፎበታል። በዝሙት ኃጢአት ወደቀ። በኋላም የሴቲቱን ባል አስገድሎ አገባት፤ 2ሳሙ. 11-12። ሕዝቡንም በመቍጠሩ እግዚአብሔርን አስቈጣ፤ 2ሳሙ. 24። በእነዚህ ኃጢአቶች ዳዊት በራሱና በሕዝቡ ላይ ብዙ መቅሠፍት አመጣ፤ ልጁ አቤሴሎም ዐመፀበት (2ሳሙ. 15-18)፤ ሰሎሞን መንግሥቱን እንደሚወርስ ከተወሰነ በኋላ አዶንያስ መንግሥቱን ለመያዝ ሞከረ፤ 1ነገ. 1። ሆኖም ዳዊት እግዚአብሔርን በመፍራቱ ከኃጢአቱ ተመለሰ፤ እግዚአብሔርም ይቅር አለው፤ 2ሳሙ. 12፥13-14።

**ዳውጃ**፤ ከቄጠማ፥ ከግርና ከለፕ የሚሠራ ምንጣፍ፤ 2ሳሙ. 17፥19።

**ዳግም ልደት**፤ አንደኛ ልደት በሥጋ ከአባትና ከእናት ሲሆን፥ ዳግመኛ ልደት ከመንፈስ መወለድ፥ መታደስ፥ መለወጥ፥ ወደ አዲስ ሁኔታ መግባት ማለት ነው። ሰው ዳግመኛ ካልተወለደ በቀር የእግዚአብሔርን መንግሥት ሊያይና ሊገባበት አይችልም፤ ዮሐ. 3፥3:5። ሰው ዳግመኛ የሚወለደው ከውሃና ከእግዚአብሔር መንፈስ ነው፤ ዮሐ. 1፥13፤ 3፥3-8፤ ቲቶ 3፥5። ብዙዎች ውሃ ሲል ጥምቀትን፥ ሌሎች መንጻትን፥ ሌሎች የእግዚአብሔርን ቃል ያመለክታል ይላሉ። ሰው ዳግመኛ የሚወለደው የእግዚአብሔርን ቃል ሰምቶ ሲያምን ነው (1ጴጥ. 1፥23-25፤ ያዕ. 1፥18)፤ ዳግመኛ የተወለደ ጽድቅን ያደርጋል (1ዮሐ. 2፥29)፤ ኃጢአትን አያዘወትርም (1ዮሐ. 3፥9፤ 5፥18)፤ ፍቅርን ያሳያል (1ዮሐ. 4፥7)፤ ክርስቶስን ያምናል (1ዮሐ. 5፥1)፤ ዓለምንም ያሸንፋል (1ዮሐ. 5፥4)። «መመለስ» ይመ.

የሙታንም ትንሣኤ ዳግም ልደት ይባላል። ይህም በክርስቶስ ዳግም ምጽአት የሚገኘውን የአዲስ መንፈስ ሁኔታ ያመለክታል፤ ማቴ. 19፥28። ብዙ ጊዜ ዳግም ልደት በኃጢአት ምክንያት መንፈሱ በሞተ ሰው ልብ ውስጥ የእግዚአብሔርን ሥራ ያሳያል፤ ኤፌ. 2፥1-5። «ኃጢአት» ይመ.

**ዳግም ምጽአት**፤ የክርስቶስ ሁለተኛ መምጣት። ኢየሱስ እንደገና እንደሚመጣ ተነግሯል፤ ማቴ. 24፥30፤ 26፥64፤ ዮሐ. 14፥3። ከዐረገ በኋላ መላእክት (ሐ.ሥ. 1፥11)፥ ሐዋርያትም ይህን አስተማሩ፤ ፊል. 3፥20፤ 1ተሰ. 4፥15:16፤ 2ተሰ. 1፥6-10፤ ቲቶ 2፥12:13፤ ዕብ. 9፥28። መምጣቱ የቤ.ክ. ተስፋ ነው።

ሳይመጣ የሚከተሉት ነገሮች ይፈጸማሉ።

1. ወንጌል ለአሕዛብ ሁሉ ይሰበካል፤ ማቴ. 24፥14፤ ቆላ. 1፥6:23።

2. ወደ መጨረሻው ከእስራኤል ወገን ብዙዎች በክርስቶስ ያምናሉ፤ ሮም 11፥25-29፤ 2ቆሮ. 3፥15:16።

3. መጨረሻ ላይ ትልቅ ክህደት (ማቴ. 24፥12፤ 2ተሰ. 2፥3፤ 2ጢሞ. 3፥1-7፤ 4፥3:4)፥ ከኢየሩሳሌም ውድቀት በፊት እንደነበረውም ታላቅ መከራ ይሆናል፤ ማቴ. 24፥15-22።

4. የዐመፅ ሰው የሚባለው የክርስቶስ ተቃዋሚ ይነሣል፤ 2ተሰ. 2፥3:4፤ ራእ. 20፥7-9። «ተቃዋሚ» ይመ.

5. በሰማይና በምድር አስፈሪ ምልክትና ለውጥ ይታያል፤ ማቴ. 24፥29:30።

ከዚህ ሁሉ በኋላ ኢየሱስ ይመጣል። ሰዎች ሳያስቡ ይመጣል። ምእመናን ቀኑንና ሰዓቱን ባያውቁም ምልክቶችን እያዩ በተስፋ ይጠባበቁታል፤ ማቴ. 24፥32-44፤ 1ተሰ. 5፥3:4።

ኢየሱስ የሚመጣው በሥጋ (ሐ.ሥ. 1፥11፤ ቲቶ 2፥13:14፤ ራእ. 1፥7)፥ በደመና ላይ (ማቴ. 24፥30)፥ በመላእክት አለቃ ድምፅ፥ በእግዚአብሔር

መለከት (1ተሰ. 4፥16)፥ ከመላእክት ጋር (ማቴ. 24፥31፤ 2ተሰ. 1፥6:7) ነው። በክርስቶስ የሞቱ ይነሣሉ፤ በምድር ያሉ ሕያዋን ምእመናን ተለውጠው ይነጠቃሉ፤ ሌሎችም ይነሣሉ፤ (ማቴ. 24፥40:41፤ ዮሐ. 5፥28:29፤ 1ቆሮ. 15፥51:52፤ 1ተሰ. 4፥13-18። ኢየሱስ ከመጣ በኋላ ጻድቃንንና ኃጥአንን ይለያል፤ ማቴ. 25፥31-46። ለምእመናን እንደ ሥራቸው ዋጋ ይሰጣል (ማቴ. 25፥20-23፤ ሉቃ. 19፥16-19፤ 2ቆሮ. 5፥10)፤ በሰይጣንና ባላመኑት ላይ ይፈርዳል፤ 2ተሰ. 1፥6-10፤ ራእ. 20፥10-15። ለኢየሱስ መምጣትና ለፍርዱ ተዘጋጅተን መኖር ይገባናል፤ ሉቃ. 21፥34-36። «ፍርድ» ይመ.

አንዳንድ ሊቃውንት የክርስቶስ ዳግም ምጽአት በአንድ ትልቅ ድርጊት፥ በአንድ ጊዜም እንደሚፈጸም ያምናሉ። ሌሎች ክርስቶስ በመጀመሪያ ለምእመናን፥ በኋላ ለፍርድ እንደሚመጣ ያምናሉ። በመካከልም ሺህ ዓመት ይኖራል ይላሉ። አንዳንዶች ደግሞ ከታላቁ መከራ በፊት፥ ሌሎች ከታላቁ መከራ በኋላ ምእመናን ይነጠቃሉ ይላሉ። ትንቢቱ ሳይፈጸም አፈጻጸሙ እንዴትና መቼ እንደሚሆን ለማወቅ አይቻልም፥ ሲፈጸም ግን የትንቢት ፍጻሜ መሆኑን እናውቃለን። «ትንቢት»፥ «ሺህ ዓመት» ይመ.

**ዳጎን**፤ በፍልስጥኤም፥ በሶርያና በመስጴጦምያ አገሮች ከሚመለኩ አማልክት አንዱ ነበረ። ከጥንት ዘመን የተገኙ ምስሎች እንደሚያሳዩት ይህ አምላክ ልዩ መልክ ያለው ሆኖ ከወገቡ በላይ ያለው የአካሉ ቅርጽ ሰውን፥ ከወገቡ በታች ደግሞ ዓሣን ይመስል ነበር። ዳጎን «የእርሻ አምላክ ነበረ» ተብሎ ይታሰባል። ለዚህ ጣዖት ፍልስጥኤማውያን በአዛጦን በጋዛም መቅደሶችን ሠርተውለት ነበር። ሶምሶንን ማርከው ካሳወሩት በኋላ በጋዛ የነበረውን የዳጎንን ቤት አፈረሰው፤ መሳ. 16፥21-30።

በዘመነ መሳፍንት መጨረሻ ላይ ፍልስጥኤማውያን እስራኤልን አሸንፈው የእግዚአብሔርን ታቦት ማርከው በአዛጦን በዳጎን ቤት ቢያኖሩት፥ የጣዖቱ ምስል በታቦቱ ፊት ወደቀ። እንሥተውም ወደ ቦታው ከመለሱት በኋላ ለሁለተኛ ጊዜ ወድቆ ተሰባበረ፤ 1ሳሙ. 5፥1-5።



**ዳጥ**፤ ከዝናም ወይም ከማናቸውም ፈሳሽ ነገር የተነሣ የሚያዳልጥ፥ የድንጋይ ንጣፍ የሌለበት መንገድ ዳጥ ይሆናል። የመከራ ምሳሌ ነው፤ መዝ. 35፥6፤ 73፥18።

**ዴማስ**፤ ከጳውሎስ ጋር የወንጌል ሥራ የሠራ ሰው፤ ቆላ. 4፥14፤ ፊልሞና 24። በኋላ ግን ዓለምን ወድዶ ጳውሎስን ትቶት ሄደ፤ 2ጢሞ. 4፥10።

**ድሀ**፤ በእስራኤል ኅብረተሰብ ድሆች የሚባሉ ባል የሌላት ሴት፥ ወላጆች የሌሉአቸው ልጆችና መጻተኞች ነበሩ። የእስራኤል ሕዝብ የሰባተኛውን ዓመት ፍሬ፥ በየዓመቱም የሚገኘውን ቃርሚያ ለድሆች እንዲተዉ ታዝዘዋል፤ ዘጸ. 23፥11፤ ዘሌ. 19፥9-10። የድሀ ርስት እንዳይነጠቅ የኢዮቤልዩ ሕግ ተሰጠ፤ ዘሌ. 25፥25-30። በመያዣ ምክንያት እንዳይጐዱ፥ ደመወዙም በቀኑ መከፈል ይገባዋል የሚል ሕግ ተሰጠ፤ ዘጸ. 22፥25-27፤ ዘዳ. 24፥15። እግዚአብሔር ድሀውን ይመለከታልና ያለው ሰው እንደ ችሎታው ሊረዳው ይገባዋል፤ ዘዳ. 15፥1-11፤ ኤፌ. 4፥28። የቤተ ክርስቲያን መሪዎች ለድሆች የመረዳጃ ድርጅት ነበራቸው፤ ሐ.ሥ. 6፥1-6፤ ገላ. 2፥10። ድሀን መናቅ አይገባም፤ ምሳ. 14፥31፤ ያዕ. 2፥1-9።

**ድል ነሣ**፤ ተዋግቶ ማሸነፍ ማለት ነው። ክርስቶስ ድል እንደነሣ ሁሉ፥ ተከታዮቹም ድል ይነሣሉ፤ ቆላ. 2፥15፤ 2ቆሮ. 2፥14፤ ራእ. 3፥21፤ 17፥14። ክፉውን ድል የሚነሡ የክርስቶስን ሥራ እየሠሩ መንፈሳዊ በረከት፥ ኃይልና ሽልማት ያገኛሉ፤ ራእ. 2፥7:11:17:26-27፤ 3፥5:12:21፤ 21፥7። እነርሱም በበጉ ደምና በተናገሩት የምስክርነት ቃል ድል ይነሣሉ፤ ራእ. 12፥11። «አሸነፈ» ይመ.

**ድሪ**፤ ሴቶች በአንገታቸው የሚያንጠለጥሉት፥ ከብርና ከሌላም የሚሠራ ጌጥ፤ ሕዝ. 16፥11። በብ.ኪ. በሊቀ ካህናቱ የክብር ልብስ ላይ ድሪ ይደረግ ነበር፤ ዘጸ. 28፥24።

**ድሪም**፤ ትንሽ የምንዛሬ ገንዘብ፥ የብር ማማሽ፤ ሉቃ. 15፥8።

**ድርጭት**፤ ቆቅን የሚመስል፥ ትንሽ ወፍ። በዐረብ አገር የሚዘምትበት ዘመን አለ። መሬት ለመሬት እየተጠጋ ትልልቅ መንጋ እየሆነ ይበርራል። የእስራኤል ልጆች በሲና በረሃ ሥጋ ለመብላት በተመኙ ጊዜ እግዚአብሔር ድርጭቶችን በብዛት ላከላቸው፤ ዘጸ. 16፥13፤ ዘኍ. 11፥31። «ወፎች» ይመ.



**ድቅድቅ ጨለማ**፤ ምንም ብርሃን የሌለበት ፍጹም ጨለማ፤ 2ጴጥ. 2፥17። በፍርድ ቀን የሚሆነው ድርጊት በድቅድቅ ጨለማ ተመስሏል፤ ሶፎ. 1፥15:16።

**ድብ፤** ጥፍሩና ጠጉሩ ረጅም የሆነ፥ ጅራት የሌለው ኃይለኛ አውሬ። በጥንት ጊዜ በእስራኤል፥ ዛሬም በሊባኖስና በእስያ የሚገኝ፥ በዕብራይስጥ ቋንቋ «ዶብ» ይሉታል። ቅጠል፥ ሥር፥ ማርና ሥጋ ይበላል። ሴት ድብ ቡችሎቿን ለማዳን ብላ ስትቈጣ ሰውን መግደል ትችላለች፤ 1ሳሙ. 17፥34-36፤ 2ሳሙ. 17፥8።



**ድብ፤** የአውሬ (የድብ) ቅርጽ የሚመስል ለሚናዊ የከዋክብት ሠራዊት ወይም ክምችት፤ ኢዮብ 9፥9።

**ድብልቅ ሕዝብ፤** በአንድነት የሚኖር የልዩ ልዩ አገር ሕዝብ ወይም ክልስ ሕዝብ ማለት ነው፤ ዘጸ. 12፥38፤ ዘኍ. 11፥4-6፤ ነህ. 13፥3፤ ኤር. 25፥20።

**ድብቅ፥ መደበቅ፤** አስፈላጊ ሲሆን እግዚአብሔር የተሰወረውን ነገር ለሰው ይገልጣል፤ ዘዳ. 18፥17፤ 1ቆሮ. 2፥7። ሰው ለመልካም (ሉቃ. 2፥19:51) ወይም ለክፋት ሁኔታ ብዙ ነገርን ይደብቃል፤ ዘፍ. 4፥5-8፤ ኢያሱ 7፥19-21፤ መሳ. 20፥23። ሰዎች ከእግዚአብሔር ለመሸሸግ ወይም ለመደበቅ ቢፈልጉ አይችሉም፤ ዘፍ. 3፥8-10፤ ኢዮብ 14፥13፤ መዝ. 139፥7-10፤ 1ቆሮ. 4፥5።

**ድኅነት፤** ከኃጢአት፥ ከፍርድና ከዘላለማዊ ሞት መዳን። ከእግዚአብሔር በክርስቶስ የሚገኝ መዳን ነው፤ ሐ.ሥ. 28፥28። «ደኅንነት» ይመ.

**ድንቅ፤** «ተአምር» ይመ.

**የድንበር ምልክት፤** የግል ርስትን ክልል የሚወስን ምልክት፤ ይህንም ምልክት መንቀል ከባድ ወንጀል ነበረ፤ ዘዳ. 19፥14፤ ምሳ. 22፥28።

**ድንቢጥ፤** ልዩ ልዩ መልክ ያለው አነስተኛ ወፍ፤ ማቴ. 10፥29። «ወፎች» ይመ.

**ድንብላል፤** የወጥ ቅመም የሚሆን ትንሽ ዘር፤ ዘኍ. 11፥7፤ ዘጸ. 16፥31።



ድንቢጥ

**ድንክ፤** በትክክል ያላደገ፥ አጭር ሰው። በብ.ኪ. በመሠዊያ ሊያገለግል አልተፈቀደለትም ነበር፤ ዘሌ. 21፥20። «በሽታ» ይመ.

**ድንኳን፤** በተራዳዎች ላይ የተዘረጋ፥ በገመድ አውታር የተያዘ፥ ከተፈተለ የፍየል ጠጕር ወይም ከቆዳ የተሠራ መኖሪያ፤ ኢሳ. 54፥2። ሥዕሉን በገጽ 237 ይመ.

**ድንጋይ፤** በከነዓን ልዩ ልዩ ዓይነት ድንጋዮች በብዛት ይገኛሉ፤ ሰዎች ለሕንጻ (1ነገ. 5፥17፤ አሞጽ 5፥11)፥ ለድንበር መለያ (ኢያሱ 15፥6)፥ ለጦር መሣሪያ (1ሳሙ. 17፥40)፥ ለጣዖት (ኢሳ. 57፥3-7)፥ ለመቍረጫ (ዘጸ. 4፥25)፥ ለመዝጊያ (ዘፍ. 29፥2፤ ማቴ. 27፥60)፥ ለመታሰቢያ (ኢያሱ 4፥20)፥ ለሌላም ሁሉ በድንጋይ ይጠቀሙ ነበር። በምሳሌነት ሕይወት የሌለው ነገር (1ሳሙ. 25፥37፤ ሕዝ. 11፥19:20) ወይም መሠረት ያለውን ቋሚ ነገር ሁሉ ሊያመለክት ይችላል፤ ዳን. 2፥34:35፤ መዝ. 118፥22። ምእመናን በሕንጻ ድንጋዮች



ድንብላል



ድንኳን

ተመስለዋል፤ 1ጴጥ. 2፥5። «የማዕዘን ድንጋይ»፥ «ዓለት» ይመ.

ድንጋይ፥ የከበሩ ድንጋዮች(ዕንቁች)፤

ከጥንት ጀምሮ የከበሩ ድንጋዮች ለዘውድና ለመስለው ሁሉ ለሕንጻም እንደ ጌጣጌጥ ተቈጥረው በሰው ዘንድ ተወድደዋል፤ ዘጸ. 28፥15-21፤ ዘኁ. 9፥16፤ 2ዜ.መ. 3፥6። የዕንቍ ስምና መልክ ብዙ ነው። በመ.ቅ. የተጠቀሱት የዕንቍ ዓይነቶች መልክ ለመለየት ያስቸግራል። ስማቸው ግን እንደሚከተለው ነው፤ መረግድ፥ ሰርድዮን፥ ሰርዶንክስ፥ ሰንፔር፥ ቀይ ዕንቍ፥ በሉር፥ ቢረሌ፥ ቶጳዝዮን፥ አልማዝ፥ አሜቴስጢኖስ፥ ኢያስጲድ፥ ኬልቄዶን፥ ክርስቲሎቤ፥ ክርስጵራስስ፥ ወራውሬ፥ ዕብነ አልማዝ፥ የሚያብረቀርቅ ዕንቍ፥ ያክንት። በየስማቸው ይመ.፤ ደግሞም «ዕንቍ» ይመ.

**ድንግል፥ ደናግል፦** ወንድ ያላወቀች ሴት፥ ወይም ሴት ያላወቀ ወንድ፤ ዘፍ. 24፥16፤ ዘጸ. 22፥16:17፤ አስ. 2፥2:3፤ ራእ. 14፥4። በብ.ኪ. የድንግል መብት በሕግ የተጠበቀ ነበር፤ ዘዳ. 22፥13-29። ቃሉ ለመንግሥታት፥ ለሕዝብ፥ ለአገር ምሳሌ በመሆን ብዙ ጊዜ ተጠቅሶ ይገኛል፤ ኢሳ. 23፥12፤ 37፥22፤ 47፥1፤ ኤር. 18፥13፤ አሞጽ 5፥2። ጌታችን ኢየሱስ ከድንግል ተወለደ፤ ኢሳ. 7፥14፤ ማቴ. 1፥22:23፤ ሉቃ. 1፥26:27። ጳውሎስ ደናግል ለሆኑ ወንዶችና ሴቶች የግል ምክር ሰጥቷል፤ 1ቆሮ. 7፥25-38። እንደዚሁም ምእመናንን በድንግል መስሎአቸዋል፤ 2ቆሮ. 11፥2።

**ድኩላ፦** «እንስሳት» ይመ.

**ድያ፦** ገራኮች ጥና አምላክ ነው ብለው ያመለኩት የነበረ፤ ሐ.ሥ. 14፥12:13። ደግሞም ድዮስ ወይም ዜዎስ ተብሎ ይጠራል።

**ድድ፦** ጥርስ የሚበቅልበት ሥጋ ወይም የጥርስ መሠረት፤ ኢዮብ 19፥20።

**ድግ፦** ወንድ ወደ መንገድ ሲሄድ የሚታጠቀው እንደ መቀነት ያለ ረጅም ጨርቅ፤ ምሳ. 31፥24።

**ድጥ፦** ዳጥ ማለት ነው። «ዳጥ» ይመ.

**ድፍረት፦** ሰዎች ልዩ ልዩ ነገርን ማድረግ ሲደፍሩ (አስ. 4፥16፤ ሮሜ 5፥7)፥ በእግዚአብሔር ፊት ግን ብዙ ጊዜ አይደፍሩም፤ ማቴ. 22፥46፤ ማር. 12፥34፤ ዮሐ. 21፥12፤ ሐ.ሥ. 5፥13፤ 7፥32። ለወንጌል ሥራ ድፍረት ያስፈልጋል፤ ሐ.ሥ. 9፥27፤ 1ተሰ. 2፥2።

**ዶለተ፦** በሰው ላይ ክፉ መከረ፤ አሴረ፤ አደመ፤ 1ሳሙ. 22፥13።

**ዶሮ፦** ከንጋት በፊት ይጮኻል፤ ማር. 13፥35፤ 14፥30:68:72። የዶሮ ጫጩቶቿን መሰብሰብ የክርስቶስን ፍቅር ያሳስባል፤ ማቴ. 23፥37።



**ዶታይን፦** ከሰማርያ በስተሰሜን 20 ኪ.ሜ. ርቆ የሚገኝ ከተማ። በዚህ ቦታ የዮሴፍን ወንድሞቹ ለነጋዴዎች ሸጡት፤ ዘፍ. 37፥13-28። በዶታይን ኤልሳዕ የሶርያን ጦር ሠራዊት አሳወረ፤ 2ነገ. 6፥11-23። ካ. 4ሀ።

**ዶፍ፦** ጉርፍ እስከሚሆን ድረስ የሚዘንም ኃይለኛ ዝናም። የጨካኝ ሰው ምሳሌ ሆኖ ተጠቅሷል፤ ምሳ. 28፥3።

**ጀልባ፦** ትንሽ መርከብ። የእስራኤል ሕዝብ ምንም እንኳን በታላላቅ መርከቦች ባይጠቀሙም፥ በገሊላ ባሕር ዓሣን ለማጥመድና ለመሻገሪያ ያህል በጀልባ ይጠቀሙ ነበር። ጀልባዎች ዐሥራ አምስት የሚያህሉ ሰዎችን የሚይዙ ሲሆኑ ብዙ ጊዜ በመቅዘፊያ ያስሄዱቸው ነበር፤ ማቴ. 4፥21፤ 9፥1፤ ዮሐ. 6፥19።

**ጀርት፦** «እንስሳት» ይመ.

**ጃንደረባ፤** ቃሉ ሁለት ትርጉም አለው፥ 1. ከፍ ባለ ማዕረግ የሚሠራ ጠባቂ፤ ዘፍ. 39፥1:8፤ አስ. 1፥10። 2. ስልብ ሰው፤ ኢሳ. 56፥3። ጃንደረቦች ታማኞች ሆነው ስለተቈጠሩ፥ ብዙ ጊዜ በቤተ መንግሥት ይገኙ ነበር፤ ሐ.ሥ. 8፥27። በእስራኤል ዘንድ ግን ጃንደረባ እንደ ነውረኛ ተቈጥሮ የተቀደሰን ነገር አያቀርብም፤ ወደ ጉባኤም አይገባም ነበር፤ ዘሌ. 21፥20፤ ዘዳ. 23፥1። በኋላ ግን በልጅ ፈንታ መታሰቢያ እንደሚቀምላቸው በትንቢት ተነገረ፤ ኢሳ. 56፥ 1-8። ሰውንም ጃንደረባ ለማድረግ አይፈቀድም ነበር፤ ዘዳ. 25፥11። እንደዚሁም ከእናታቸው ማኅፀን ጀምሮ ጃንደረቦች የሚሆኑ አሉ። በምሳሌነትም በወንጌል ምክንያት ሚስት ያላገባ፥ ሌላውንም የተፈቀደውን ምኞት የተወ ጃንደረባ ይባላል፤ ማቴ. 19፥11:12።

**ጅረት፤** እንደ ዐባይና እንደ በሽሎ ያለ ፈሳሽ ወንዝ፤ ዘዳ. 8፥7።

**ጅን፤** በግርጣ ሌሊት የሚሰማ ድምፅ፥ የምትሐት ነው ቢባልም፥ ያንድ ዓይነት ጉጉት ድምፅ ነው፤ ኢሳ. 34፥14። «ወፎች» ይመ.

**ጅንጅላቴ ወፍ፤** በራሱ ላይ ጉትያ (ቁንጮ) ያለው ዠንጉርጉር ወፍ። እንድርማሚት ተብሎም ይጠራል፤ ዘሌ. 11፥19። «ወፎች» ይመ.



ጅንጅላቴ ወፍ

**ጆሮ፤** ካህናት ለአገልግሎት ሲለዩ፥ ለምጻሞች ሲነጹ ጆሮአቸው በደም ይቀባ ነበር፤ ዘጸ. 29፥20፤ ዘሌ. 14፥14። ሰው ለጌታው ለዘለዓለም አገልጋይ መሆን ሲፈልግ፥ ጌታው ጆሮውን በወስፌ ይበሳው ነበር፤ ዘጸ. 21፥5:6። ሰው የእግዚአብሔርን ቃል እንዲያስተውል የሚሰማ ጆሮ ያስፈልገዋል፤ ማቴ. 11፥15።

**ገሃነም፤** የሄኖም ሸለቆ ማለት ነው። በዚህ ሸለቆ የኢየሩሳሌም ከተማ ቆሻሻ ሁሉ ይጣልና ይቃጠል ነበር፤ እሳትም ከዚያ አይጠፋም ነበር። ስለዚህ ለኃጢአተኞች መግቢያ ቦታ ምሳሌ ሆነ። እግዚአብሔር የኃጢአተኞችን ሥጋና ነፍስ በገሃነም ያኖራል፤ ማቴ. 10፥28። ከዚያም አይወጡም፤ እሳቱ አይጠፋም ትሉ አያንቀላፋም፤ ማቴ. 5፥22:29:30፤ ማር. 9፥43-48፤ ያዕ. 3፥6። «ሲኦል» ይመ.

**ገለበጠ፤** የአንድን ነገር አቀማመጥ ቀየረ፥ አዛወረ፤ ዘፍ. 19፥25፤ ዘዳ. 29፥23፤ ዮናስ 3፥4፤ ማቴ. 21፥12፤ ዮሐ. 2፥15።

**ገለዓድ፤** የምናሴ የልጅ ልጅ። ከእርሱ ገለዓዳውያን ተወለዱ። አገራቸውም ገለዓድ ተባለ፤ ዘኍ. 26፥29-30። እንደ ዮፍታሔ አባት ገለዓድ የተባሉ ሌሎችም አሉ፤ መሳ. 11፥1-3።

ገለዓድ፤ ከዮርዳኖስ ማዶ በስተምሥራቅ በእስራኤል የነበረ አገር። እስራኤላውያን የተስፋይቱን አገር በወረሱ ጊዜ ገለዓድ ለሮቤልና ለጋድ ነገዶች ለምናሴም ነገድ ግማሽ ተሰጠ፤ ዘዳ. 3፥13-15። በገለዓድ የሚገኝ የቅባት መድኃኒት የታወቀና ለውጭ አገር የሚሸጥ ነበር፤ ዘፍ. 37፥25፤ ኤር. 8፥22። አገሩ ብዙ ጫካ ያለበት ተራራማ ስለሆነ የሚሸሹ ሰዎች ይሸሸጉበት ነበር፤ ለምሳሌ ያዕቆብ (ዘፍ. 31፥21)፥ እስራኤላውያን (1ሳሙ. 13፥6፡7)፥ ዳዊት፤ 2ሳሙ. 17፥22። ካ. 3ሠ።

**ገለገለ፤** ያልታረሰውን መሬት ለመጀመሪያ ጊዜ አረሰ፤ ኢሳ. 28፥24።

**ገሊላ፤** ከሦስቱ የእስራኤል ክፍለ አገሮች ሰሜናዊቱ። በመካከል ሰማርያ ስትገኝ ከዚያም ቀጥሎ በስተደቡብ ይሁዳ ትገኛለች። ገሊላም በምሥራቅ ከዮርዳኖስና ከገሊላ ባሕር፥ በሰሜን ከሶርያ፥ በምዕራብ ከፊንቄ አገር ትዋሰናለች። ከእስራኤል ምርኮ በኋላ አሕዛብ ወደዚች አገር ገቡ፤ 2ነገ. 15፥29፤ 17፥24። ስለዚህ የአሕዛብ ገሊላ ተባለች፤ ማቴ. 4፥14-16። ደግሞ በገሊላ የኖሩት አይሁድ ቋንቋቸውና ሃይማኖታቸው ትንሽ ለየት ያለ ሆነ፤ ማቴ. 26፥73። በዚህ ምክንያት ሌሎቹ አይሁድ ናቁአቸው፤ ዮሐ. 7፥52፤ 1፥47።

ኢየሱስ ከሌላ ቦታ ይልቅ ብዙ ጊዜ በገሊላ እየተዘዋወረ ያስተምርና ተአምራትም ያደርግ ነበር፤ ሉቃ. 4፥14:15፤ ዮሐ. 1፥44። ደቀ መዛሙርቱ የገሊላ ሰዎች ነበሩ፤ ሐ.ሥ. 1፥11፤ 2፥7። ኢየሱስ ወምድር ሳለ ሄሮድስ በገሊላ ገዥ ነበረ፤ ሉቃ. 3፥1:19፤ 13፥32። ከክርስቶስ ዕርገት በኋላ በገሊላ ይኖሩ የነበሩ ብዙ አይሁድ በሮም መንግሥት ላይ ስላመፁ ሮማውያን በ70 ዓ.ም. ኢየሩሳሌምን አፈረሱ። ከዚያም በኋላ ገሊላ በሃይማኖት ትምህርት ቤቶቿና በትልልቅ ምኵራቦቿ ገናና ሆነች። ካ. 5ለ።

**የገሊላ ባሕር፤** በብሉይ ኪዳን የኪኔሬት ባሕር ተብሎ ይጠራል (ዘኍ. 34፥11፤ ኢያሱ 12፥3)፤ በአዲስ ኪዳንም 1. የጌንሳሬጥ ባሕር (ሉቃ. 5፥1)፥ 2. የጥብርያዶስ ባሕር በመባል ይጠራል (ዮሐ. 6፥1)፤ ጥብርያዶስ በባሕሩ ዳር ያለ ዋና ከተማ ነውና የባሕሩ ርዝመት 20 ኪ.ሜ፥ ስፋቱም 12 ኪ.ሜ. ያህላል። ከታላቁ ባሕር ጠለል 212 ሜትር

ይቀንሳል። በዙሪያው ተራራ ስላለ፥ በድንገት ዐውሎ ነፋስ ሊነካ ይችላል። ክርስቶስ በምድር ሳለ በዙሪያው 9 ከተማዎች ነበሩ፤ ጥብርያዶስም የአራተኛው ክፍል ገዥ የሄሮድስ ዋና ከተማ ነበረ። ኢየሱስ የማስተማሩን ሥራ በገሊላ ባሕር አካባቢ ጀመረ። ዓሣ አጥማጆችንም ደቀ መዛሙርቱ እንዲሆኑ ከዚሁ ባሕር አጠገብ ጠራቸው፤ ማር. 1፥16። በባሕሩ ላይ ተራመደ (ማር. 6፥45-51)፤ ዐውሎ ነፋስንም ገሠጸ (ማር. 4፥35-41)፤ ደቀ መዛሙርቱ ከዚህ ባሕር ዓሣ በማጥመድ ላይ ሳሉ ሁለት ጊዜ በተአምራት ረዳቸው፤ ሉቃ. 5፥1-11፤ ዮሐ. 21፥1-11። ካ. 3ለ።



የገሊላ ባሕር

**ገላትያ፤** ገላትያ አውራጃ ነው፥ የሚገኘውም ዛሬ ቱርክ በሚባለው አገር ውስጥ ነው። ይህ አውራጃ በአገሪቱ መሐል ከሰሜን እስከ ደቡብ የሚገኘው ነው፤ በደቡቡ የገላትያ ክፍል የጲሲድያ የምትሆን አንጾኪያ፥ ኢቆንዮን፥ ልስጥራንና ደርቤን የሚባሉ ከተሞች ተገኝተዋል፤ እነዚህም ሐዋርያው ጳውሎስ ወንጌልን ሊሰብክ ለመጀመሪያ ጊዜ ሲወጣ የጐበኛቸው ከተሞች ናቸው፤ ሐ.ሥ. 13፥14-14፥28። በ2ኛና በ3ኛ የስብከት ጒዞዎቹም ጐብኝቷቸዋል፤ ሐ.ሥ. 16፥6፤ 18፥23። ካ. 6በ።

**የገላትያ አብያተ ክርስቲያናት፤** በጳውሎስ የተመሠረቱ ሲሆኑ፥ በኋላ ግን ከትምህርቱ አፈገፈጉ። ቢሆንም፥ ከጥቂት ዓመታት በኋላ ሐዋርያው ለቆሮንቶስ ቤ.ክ. ሲጽፍ «ለገላትያ አብያተ ክርስቲያናት እንደ ደነገግሁት» በማለቱ፥ መልእክቱ ከደረሳቸው በኋላ በስሕተታቸው ተጸጽተው የተመለሱ ይመስላል፤ 1ቆሮ. 16፥1።

**የገላትያ መልእክት፤** ጳውሎስ በገላትያ አብ.ክ.ን ከተከለ በኋላ ወደ ሶርያ ተመለሰ። ከጥቂት ቀን በኋላም ሰዎች ወደ ገላትያ ሄደው ሐዋርያዊ ሥልጣኑንና ትምህርቱን እየነቀፉ «ካልተገረዛችሁና የሙሴን ሕግ ካልጠበቃችሁ በክርስቶስ ማመን ብቻ በቂ አይደለም» ብለው ስላስተማሩ፥ ምእመናን ከጳውሎስ ትምህርት ዘወር በማለት የእነርሱን ተቀበሉ። ሐዋርያው የገላትያ ምእመናን በሌላ ትምህርት መወሰዳቸውን ሲሰማ ይገሥጻቸውና ወደ እውነት ይመልሳቸው ዘንድ ይህን መልእክት ጻፈ። መልእክቱ ከጻፋቸው መልእክቶች መካከል የመጀመሪያው ሳይሆን አልቀረም። መልእክቱ ከተጻፈበት ዓላማና ምክንያት የተነሣ የመልእክቱ መንፈስ ከበድ ያለ ነው፤ 1፥6፤ 3፥1፤ 5፥12፤ 6፥17።

ሐዋርያው በዚህ መልእክት በተለይ በሦስት የሃይማኖት ክፍሎች ላይ ያተኵራል፤ እነርሱም ፦ የሰበከው ወንጌል ሥልጣን፥ ኃጢአተኛ የሚጸድቅበት መንገድና አማኝ የሚኖርበት እውነተኛ ነፃነት ናቸው። ምዕራፍ 2 ቍጥር 16 የመልእክቱ «ቍልፍ» ነው። አማኝ ከሕግ ባርነት ነፃ ወጥቷል፤ ሆኖም ይህ አርነት የመንፈስ ቅዱስን ሥራ ለመሥራት እንጂ የሥጋን ምኞት ለመፈጸም አልተሰጠም።

ይህን ትምህርት ሲሰጥ ጳውሎስ ስለ ጸጋና ስለ ሕግ፥ ስለ እምነትና ስለ ሥራ፥ ስለ ነፃነትና ስለ ግዝረት ተደጋጋሚ ማብራሪያ ሰጥቷል። ይህን ትምህርት በቀራንዮ ከተፈጸመው የክርስቶስ ሥራ ማለትም ክርስቶስ በመስቀሉ ከአሁኑ ክፉ ዓለም ያዳነው ከመሆኑ (1፥3-5)፥ አማኙን ለሕግ እንደሞተ ከማስቆጠሩ (2፥19-21)፥ ለአማኙ ዓላማና መልእክት ከመስጠቱ (3፥1-5)፥ በአማኙ ስፍራ የሕግን እርግማን ከመሸከሙ (3፥10-14)፥ አማኙን በስደት ውስጥ ከማስገባቱ (5፥11፤ 6፥12)፥ አማኙ ሥጋውን እንዴት እንደሚገድል ከማሳየቱ (5፥24)፤ እና ለአማኙ የሚመካበትን ከመስጠቱ (6፥14) አኳያ ልንመለከተው እንችላለን።

አከፋፈል ፦

1. መግቢያ፤ የጳውሎስ ሐዋርያነት፥ አጭር ሰላምታ፥ የክርስቶስ ሥራ፥ አንድ ወንጌል ብቻ እንዳለ፤
   1፥1-10።

2. አንዱ ወንጌል ለጳውሎስ በቀጥታ መገለጡ፤
   2፥11-14።

ጳውሎስ፥ ሀ) ወንጌሉን ከሰው ሳይሆን ከራሱ ከኢየሱስ ክርስቶስ መቀበሉን (1፥11-12)፥ ለ) ወንጌሉን ከመስበኩ በፊት አክራሪ የአይሁድ እምነት አራማጅ መሆኑን (1፥13-17)፥ ሐ) ሌሎች ሐዋርያት የሰበከውን ወንጌል ማጽደቃቸውን (1፥18-2፥10)፥ መ) የጴጥሮስን አካሄድ የተቃወመው መሆኑን (2፥11-14)፥ ሠ) ወንጌሉ፥ ሰው በክርስቶስ እምነት መጽደቁን እንደሚያውጅ (2፥15-21) ገለጠ።

3. ወንጌሉ ከሕግ ብልጫ ያለው መሆኑ፤
   3፥1-4፥31።

ጳውሎስ፥ ሀ) አንባቢዎች በሕግ ሳይሆን በእምነትና በመንፈስ መባረካቸውን (3፥1-5)፥ ለ) አብርሃም በሕግ ሳይሆን በእምነት መጽደቁን (3፥6-9)፥ ሐ) ክርስቶስ አማኞችን ከሕግ እርግማን መዋጀቱን (3፥10-14)፥ መ) ሕግ የተስፋውን ቃል መሻር አለመቻሉን (3፥15-18)፥ ሠ) የሕግ ዓላማ ሰዎችን ወደ ክርስቶስ ማድረስ መሆኑን (3፥19-29)፥ ረ) ወንጌሉ ሰዎችን ከባርነት አውጥቶ የእግዚአብሔር ልጆች ማድረጉን (4፥1-7)፥ ሰ) ወደ ድሮ ልማድ መመለስ ባርነት መሆኑን (4፥8-11)፥ ሸ) መልካምን

ነገር ሁሉ ለአንባቢዎቹ መመኘቱን (4፥12-20)፥ ቀ) ሕጋዊ ባርነትና ነፃነት በአጋርና በሣራ ታሪክ መብራራታቸውን (4፥21-31) አሳየ።

4. ወንጌሉ ወደ እውነተኛ ነፃነት መምራቱ፤ 5፥1-6፥10።

ጳውሎስ፥ ሀ) ወንጌሉ ግዝረትንና ሕግን በመፈጸም ድኅነት ይገኛል የሚለውን አመለካከት ማስቀረቱን (5፥1-6)፥ ለ) የስሕተት ትምህርት ወንጌሉን መበከሉን (5፥7-12)፥ ሐ) ነፃነት ለሥጋዊ ድርጊት ምክንያት አለመሆኑን (5፥13-15)፥ መ) በመንፈስ የሚመላለሱ ሥጋን መስቀላቸውን (5፥16-26)፥ ሠ) ነፃነት፥ ርኅራኄን፥ ልግስናንና በረከትን የሚያስገኝ መሆኑን (6፥1-10) አስተማረ።

5. መደምደሚያ፤ የጳውሎስ ትግል፥ ትምክህትና ቡራኬ።

**ገል**፤ የሸክላ ዕቃ ስባሪ። ለእሳት መጫሪያ የሚያገለግል ነው፤ ኢዮብ 2፥8፤ ኢሳ. 30፥14። የድካም ምሳሌ ነው፤ መዝ. 22፥15።

**ገመድ**፤ ማሰሪያ። ከእንስሳት ጠጕር፥ ከቆዳ፥ ከልጥና ከልዩ ልዩ ተክል ቃጫ ይገመዳል፤ ለብዙ ሥራ ያገለግላል፤ ኢያሱ 2፥15፤ 1ነገ. 21፥31:32፤ ዮሐ. 2፥15፤ ሐ.ሥ. 27፥32።

**ገማልያል**፤ የታወቀ ፈሪሳዊና የሕግ መምህር። ጳውሎስ የተማረው ከገማልያል ዘንድ ነው። ሐዋርያትን እንዲታገሡአቸውና እንዳይነኩአቸው ለሸንጎው ምክር አቀረበ፤ ሐ.ሥ. 5፥34-39፤ 22፥3።

**ገማዳውያን**፤ የያፌት ዘሮች። በግእዝ ገማዲም ይባላሉ። ኀይለኞችና ቈራጦች ናቸው፤ ሕዝ. 27፥11።

**ገምባሌ**፤ ከእግር እንገት እስከ ቋንጃ(ጂ) የሚለበስ። እንደ ረዥም ጫማ ያለ ነው፤ 1ሳሙ. 17፥6። «የጦር መጫሚያ» ይመ.

**ገሞራ**፤ «ሰዶም» ይመ.

**ገሪዛንና ጌባል**፤ በሴኬም አቅራቢያ ያሉ ሁለት ተራራዎች። ገሪዛን የበረከት፥ ጌባል የመርገም ተራራዎች ናቸው፤ ዘዳ. 11፥29። ኢያሱ በሁለቱ ተራራዎች መካከል መሠዊያ ሠራ፤ ሕጉንም በዚያ አነበበ፤ ዘዳ. 27፥4-8፤ ኢያሱ 8፥30-35። የጌዴዎን ልጅ ኢዮአታም በገሪዛን ራስ ላይ ሆኖ ለአቤሜሌክ ተከታዮች ጮኸ፤ መሳ. 9፥7-21። ሳምራውያን በገሪዛን ተራራ ቤተ መቅደስን ሠሩ፤ ዮሐ. 4፥20። ካ. 3መ 3ሰ።

**ገርነት**፤ ስለ ሌላ ሰው ማሰብ፥ በቃልም ሆነ በድርጊት ሰውን አለመጕዳትና አለመጨከን፤ 1ጴጥ. 2፥18። ክርስቶስን የሚከተሉ በሰው መካከል ገርነት እንዲያሳዩ ይጠበቅባቸዋል፤ ፊል. 4፥5፤ 2ጢሞ. 2፥24፤ ቲቶ 3፥1:2፤ ያዕ. 3፥17።

**ገበሎ**፤ የእንሽላሊት ዓይነት፥ ዝንብን የምትበላ፥ በግድግዳ የምትኖር ተንቀሳቃሽ እንስሳ፤ ዘሌ. 11፥30።

**ገበታ**፤ ምግብ የሚቀመጥበት ጠረጴዛ፤ መሳ. 1፥7። በእግዚአብሔር ማደሪያ ውስጥ ከግራር እንጨት የተሠራ ልዩ ገበታ ነበር፤ በወርቅም የተለበጠ ነበር። በዚህ ገበታ ላይ ካህናት ሁልጊዜ የገጹን ኅብስት ያስቀምጡ ነበር፤ ዘጸ. 25፥23-30፤ ዘሌ. 24፥5-9።



የመገኘቱ ኅብስት በወርቅ ገበታ ላይ.

**ገበያ**፤ ማንኛውም ዕቃ የሚነገድበት፥ ሰዎች የሚገናኙበት፥ ልጆች የሚጫወቱበት፥ ጉዳይ የሚፈጸምበት ቦታ። ክርስቶስ በምድር ሳለ ሰዎች ድውያንን በገበያ ያስቀምጡ ነበር፤ ማቴ. 11፥16:17፤ ማር. 6፥56፤ 12፥38፤ 1ቆሮ. 10፥25። ብዙ ጊዜ ዳኞች ገበያ አጠገብ ይገኙ ነበር፤ ሐ.ሥ. 16፥19፤ 17፥17።

**ገባር**፤ ያለ ደመወዝ መንግሥትን ለማገልገል የተገደደ ሰው ወይም ሕዝብ፤ 1ነገ. 5፥13:14፤ 9፥21።

**ገባዖን**፤ በኢያሱ ዘመን የነበረ የኤዊያውያን ከተማ፤ ኢያሱ 9፥7። የገባዖን ሰዎች እስራኤልን አታለሉና ከእስራኤል ጋር ተማማሉ፤ ኢያሱ 9፥1-27። ሳኦል የገባዖንን ሰዎች ገደለ፤ 2ሳሙ. 21፥1-9። የዳዊትና የአበኔር ጆግኖች በገባዖን ውሃ አጠገብ ተቈራቈሱ፤ 2ሳሙ. 2፥12-17። ሰሎሞን በመጀመሪያ ሲነግሥ መሥዋዕትን በገባዖን አቀረበ፤ 1ነገ. 3፥4-15። ካ. 3ሰ።

**ገብርኤል**፤ ገብርኤል ማለት የእግዚአብሔር ሰው ማለት ነው። በሰው ምሳሌ ለሰዎች የተገለጠ የእግዚአብሔር መልአክ። ለዳንኤል የእግዚአብሔርን ቃል ለመተርጐምና የሚመጣውን ለመግለጥ ተላከ፤ ዳን. 8፥15-26፤ 9፥21-27። ለዘካርያስ ስለ ዮሐንስ፥ ለማርያምም ስለ ክርስቶስ ልደት የምሥራችን ቃል አቀረበ፤ ሉቃ. 1፥11-38።

**የገበ**፤ ቃሉ የግእዝ ቃል ነው። ጎን፥ አጠገብ ማለት ነው። እህል ከታጨደ ወይም ከተቈረጠ በኋላ በጎኑ የሚያቈጠቍጠውና የሚወጣው ቡቃያ የገበ እህል ይባላል፤ አሞጽ 7፥1።

**ገነት**፤ ቃሉ ሁለት ነገሮችን ይተረጕማል።

1. አትክልት ማለት ነው፤ ዘፍ. 2፥8፤ 3፥8።

2. በቅጥር የተከለለ የአትክልት ስፍራ ማለት ነው፤ መ.መ. 4፥13-16።

እግዚአብሔር አዳምን በዔድን በተከለው ገነት አኖረው። በገነት ብዙ መንገዶችና ዛፎች ነበሩ፤ በተለይም የሕይወት ዛፍና መልካምንና ክፉን የምታስታውቅ ዛፍ ነበሩበት፤ ዘፍ. 2፥8-17። በዚያ እግዚአብሔር ከአዳም ጋር ይገናኝ ነበር፤ ዘፍ. 2፥16፤ 3፥8። እግዚአብሔር በኃጢአት ምክንያት አዳምን ከገነት አስወጣው፤ ዘፍ. 3፥22-24። አዳም የነበረበት ገነት በጥፋት ውሃ ጊዜ የጠፋ ይመስላል። ዋናው የገነት አሳብ ግን ሰው ከእግዚአብሔር ጋር በደስታና በፍቅር የሚገናኝበት ሁኔታ ነውና፥ ጻድቃን ሲሞቱ የሚሄዱበት ገነት ይባላል፤ ይህም አዳም በነበረበት የመጀመሪያው ገነት ሁኔታና ደስታ ተገልጧል፤ ኢሳ. 58፥11፤ ኤር. 31፥12፤ ራእ. 2፥7፤ 22፥1-5። ገነት በልዕልናው ምክንያት ሰማይ ተብሏል፤ 2ቆሮ. 12፥4። ገነት ማለት እግዚአብሔር ራሱ ያለበት ማለት እንደሆነ ክርስቶስ ተናግሯል፤ ሉቃ. 23፥43። «የአትክልት ስፍራ» ይመ.

**ገና**፤ የክርስቶስ ልደት የሚታሰብበት ዓመታዊ በዓል። ቃሉ ከግሪክ የተገኘ ነው። በዓሉ በምሥራቃውያን ታኅሣሥ 29፥ በምዕራባውያን ታኅሣሥ 15፥ በአርመን ቤ.ክ. ጥር 12 ቀን ይከበራል። በዓሉ በቈስጠንጢኖስ ጊዜ በ325 ዓ.ም እንደተከበረ በዓለም ታሪክ እናነባለን። ከዚያ በፊት ግን ይከበር እንደነበር ማረጋገጫ አልተገኘም። መ.ቅ. ስለ በዓሉ አይናገርም፥ ጊዜውንም ለመወሰን በቂ ማስረጃ አይሰጥም፤ «ዓመት» ይመ.። ሆኖም ምእመናን ሁሉ ከዘለዓለም የነበረ ቃል ከቅድስት ድንግል ማርያም ሥጋንና ነፍስን ነሥቶ እንደተወለደ አምነው ያከብሩታል።

**ገንዘብ**፤ እስከ 700 ከክ. ል. ምንዛሬ አልነበረም። ብርና ወርቅ እየመዘኑ ይገዙና ይሸጡ ነበር። አብርሃም በአራት መቶ ሰቅል ብር መሬት ገዛ፤ ዘፍ. 23፥15:16። ሰሎሞን ያገኘው የነበረው ግብር በወርቅ መክሊት ተመዘነ፤ 1ነገ. 10፥14:15። በኋላ ግን ልዩ ልዩ መንግሥታት የንጉሣቸውን ወይም የሌላውን ምልክት በወርቅና በብር ወይም በናስ አትመው ገንዘብ አበጁ፤ ማቴ. 10፥9፤ 22፥20፤ ብዙ አገሮች ገንዘብ ስላሳተሙ ገንዘብ ለዋጮች አስፈላጊ ሆኑ። እነርሱም ከመጠን በላይ አትራፊዎች ሆነው ተገኙ፤ ማቴ. 21፥12:13። ክርስቶስ በምድር ሳለ በልዩ ልዩ ገንዘብ ይጠቀሙ ነበር። የእያንዳንዱን ዋጋ ለመወሰን ያስቸግራል። ሆኖም አንድ ዲናር ለቀን ሠራተኛ ያንድ ቀን ደመወዝ ነበረ፤ ማቴ. 20፥2። ዲናር ከሁሉ ያነሰ የናስ ሳንቲም ነበር። በዲናር ዐሥራ ስድስት ሳንቲሞች ነበሩ። በእስታቴር አራት ዲናሮች ነበሩ። ምናንና መክሊት በመጀመሪያ የክብደት መለኪያዎች ነበሩ። የምናን ብር መቶ ዲናር፥ የመክሊት ብር ስድስት ሺህ ዲናር ያህል ነበረ። ሐዋርያት ገንዘብ እንዳይዙ ተከለከሉ (ማቴ. 10፥9)፥ በኋላ ግን ተፈቀደላቸው፤ ሉቃ. 22፥35:36።

ገንዘብ ማናቸውንም ዓይነት ሀብት ሊያመለክት ይችላል፤ ገንዘብ አንቅፋት እንዳይሆን መጠንቀቅ ያስፈልጋል፤ ማቴ. 6፥24። የሰው ጠባይ በገንዘብ አጠቃቀሙ ይገለጣል፤ ሉቃ. 16፥10-13። ገንዘብን መውደድ የክፋት ሁሉ ሥር ነው ተብሏል፤ 1ጢሞ. 6፥10።

**ገውዝ**፤ ፍሬው ጣፋጭ የሆነ ተክል፤ መ.መ. 6፥11።

**ገዥ፥ አገረ ገዥ**፤ ከዋናው ባለ ሥልጣን በታች አንድን አገር የሚያስተዳድር። በብ.ኪ. ዮሴፍ (ዘፍ. 42፥6) ሌሎችም ገዦች ተባሉ።

በሮም መንግሥት ሁለት ዓይነት ገዦች ነበሩ። ሰላም በሚገኝባቸው አገሮች በሮም ምክር ቤት በየዓመቱ የሚሾሙ እንደ ሰርግዮስ ጳውሎስና እንደ ጋልዮስ ያሉ አገረ ገዦች ነበሩ፤ ሐ.ሥ. 13፥7፤ 18፥12። ሰላም በማይገኝባቸው የጦር ሠራዊት በሚያስፈልግባቸው አገሮች በቄሣር የሚሾሙ እንደ ጲላጦስ፥ እንደ ፊልክስ፥ እንደ ፊስጦስም ያሉ ገዦች ነበሩ፤ ማቴ. 27፥2፤ ሐ.ሥ. 23፥24፤ 24፥27። የገዥው ሥራዎች በተለይ ሦስት ነበሩ፤ እነርሱም ጸጥታን መጠበቅ (ሐ.ሥ. 19፥40)፥ ግብርን መሰብሰብ (ሉቃ. 2፥1፤ 20፥22-25)፥ ፍርድንም መፍረድ ናቸው፤ ሉቃ. 23፥1:2።

**ገደለ**፤ 1. ሕይወትን አጠፋ፤ ዘፍ. 4፥8። 2. ፈቃድን ተወ፥ ክፉ ፍላጎትን ከልብና ከመንፈሳዊ ሕይወት አራቀና ለየ፤ ሮም 8፥13፤ ቆላ. 3፥5።

**ገዲ**፤ ጥፍሩ ቆላፋ፥ ጭልፊትን የሚመስል አይጥንና እባብን የሚበላ ደፋር አሞራ (ዘሌ. 11፥14)። «ወፎች» ይመ.

**ገፈራ**፤ የእንስሳት ምግብ። አብዛኛውን ጊዜ ገለባ የተቀላቀለበት እህል ነው፤ ዘፍ. 24፥32፤ 42፥27።

**ጉማሬ**፤ ቀን በውሃ ውስጥ የሚተኛ፥ ሌሊት በመሬት ላይ የሚሰማራ፥ በጣም ትልቅ የሆነ አውሬ፤ ኢዮብ 40፥15-24።

**ጉም**፤ በክረምት ወራት ከመሬት የሚተን፥ መሬትን የሚሸፍን ጭጋግ መሳይ ብትን ደመና። ጉም ለምድር ርጥበትን ይሰጣል፤ (ዘፍ. 2፥6)፥ ጉም ብዙ ጊዜ ሳይቆይ ይበተናል፤ መዝ. 147፥5።

**ጉርጅ**፤ «ጉርጅ» ይመ.

**ጉበት**፤ ደም ያለበት በሆድ ውስጥ ያለ ብልት። በጥንት ዘመን በብዙ አገር ለምዋርት ይጠቀሙበት ነበር። በባቢሎን የጉበት ምስል በሸክላ ዕቃ ላይ ቀርጸው አምሳ ስድስት ክፍል አደረጉለት፤ ለየክፍሉም ትርጕም ሰጡት። እንስሳ ገድለው ጉበቱን በመመልከት እንደ አተረጓጐማቸው የሚመጣውን ይናገሩ ነበር፤ ሕዝ. 21፥21።

**ጉበን**፤ ከመድረክ በላይ ያለ ከግራ እስከ ቀኝ የሚሻገር፥ በመቃን የተደገፈ እንጨት ወይም ድንጋይ፤ ዘጸ. 12፥22:23። ገጽ 242 ይመ.



የበር መቃኖችና ጉበን

**ጉባኤ፤** ሕዝብ ወይም ማኅበር በምክንያት የሚያደርገው ስብሰባ፤ ዘጸ. 12፥6፤ ዘኁ. 16፥3፤ 1ነገ. 8፥65፤ ሐ.ሥ. 13፥43፤ 19፥32:41። በኢየሩሳሌም አሕዛብ ስለመገረዛቸውና ሕግን ስለመጠበቃቸው የተካሄደ ስብሰባ የሐዋርያት ጉባኤ ይባላል፤ ሐ.ሥ. 15፥1-29።

**ጉቦ፤** ዳኛ ፍርድ እንዲያጣምም፥ ቀጠሮ እንዲያስረዝም የሚሰጠው መማለጃ። ጉቦ እውነትን ይሸፍናል፤ ሰዎችን ያበላሻል፤ ትክክለኛነትን ያስቀራል፤ ዳኞችንም ያስነውራል፤ ዘዳ. 16፥19፤ 1ሳሙ. 8፥3፤ 12፥3፤ መዝ. 26፥10፤ ኢሳ. 33፥15፤ አሞጽ 5፥12።

**ጉቶ፤** ግንዱና ቅርንጫፉ ከተቈረጠ በኋላ ከመሬት ላይ የሚቀር የዛፍ ጉራጅ። ከደከመ በኋላ እንደገና ኃይል የሚያገኝ ሕዝብን ሊያመለክት ይችላል፤ ኢሳ. 6፥13።

**ጊልቦዓ፤** ኃይለኛ ምንጭ ማለት ነው። በይሳኮር ርስት ያለ ተራራማ አገር። ሳኦልና ዮናታን በጊልቦዓ ተገደሉ፤ 1ሳሙ. 31፤ 2ሳሙ. 1፥21።

**ጊብዓ፤** ጉብታ ወይም ኮረብታ ማለት ነው። 1. በይሁዳ የነበረ ከተማ። ዛሬ ቦታውን ለመወሰን አይቻልም፤ ኢያሱ 15፥57። 2. ከኢየሩሳሌም ወደ ሰሜን አምስት ኪ.ሜ. ያህል ርቆ የሚገኝ የብንያም አገር ከተማ። የጊብዓ ሰዎች አስጸያፊ ብልግና ስላደረጉ እስራኤላውያን የብንያምን ወገን ለማጥፋት ተነሡ፤ ሆኖም 600 ሰዎች አምልጠዋል፤ መሳ. 19፥11-20፥48። ግን ንጉሥ ሳኦል የጊብዓ ሰው ነበረና መናገሻ ከተማውን በጊብዓ አደረገ፤ 1ሳሙ. 10፥26፤ 22፥6። በብ.ኪ. ዘመን ጊብዓ ምሽግ ከተማ ነበረ፤ ከክርስቶስ ልደት ወዲህ ግን ባድማ ሆኗል።

**ጊንጥ፤** በቆላና በበረሃ የምትኖር፥ መጠኗ የሰውን ጣት የሚያህል ተንቀሳቃሽ። ጅራቷ ላይ የሚናደፍ መውጊያ አላት። ሰው በእርሷ ከተነደፈ ይታመማል፤ ሊሞትም ይችላል፤ 1ነገ. 12፥11፤ ሉቃ. 11፥12፤ ራእ. 9፥3-5።

**ጊዜ፤** ዓለም ከተፈጠረ ጀምሮ ጊዜ ይታሰባል፤ ዘፍ. 1፥1። ከአዳም ጀምሮ ዓመት ይቈጠራል፤ ዘፍ.



ጊንጥ

5፥1-5። ስለ አቈጣጠሩ ግን በሊቃውንት ዘንድ ልዩ ልዩ አሳብ አለ። እግዚአብሔር እንደ ሰው በጊዜ አይወሰንም (2ጴጥ. 3፥8)፥ ዳሩ ግን ሥጋ ነሥቶ ሰው በመሆኑ ጊዜ ተቈጠረለት፤ ገላ. 4፥4። ይህንም በማድረጉ የደኅንነትን ጊዜ ጀመረ (ማር. 1፥15)፥ ኢየሱስም እስኪመለስ ድረስ ያለው ጊዜ የመዳን ጊዜ ነው፤ 2ቆሮ. 6፥2። «ሰዓት»፥ «ቀን»፥ «ዓመት» ወዘተ. ይመ.

**ጊጤ፤** የጦርና የቀስት ውርወራ ጨዋታ። በሰ.ኤ. 3፥12 ጊጤ ማለት ኢላማ (ዒላማ) ማለት ነው።

**ጋለሞታ፤** ባል ፈትታ የምትኖር ሴት ወይም ሚስት ፈትቶ የሚኖር ወንድ። በመ.ቅ. ትርጉም ግን ዘማዊነትን ያመለክታል፤ ዘፍ. 38፥15፤ ዘዳ. 23፥17። እስራኤላውያን ጣዖትን ማምለካቸው በግልሙትና ተመስሏል፤ ሚክ. 1፥7።

**ጋሻ፤** በእጅ የሚያዝ የጦር መሣሪያ መከላከያ፤ ኢሳ. 21፥5። የእምነትና የእግዚአብሔር ረድኤት ምሳሌ ነው፤ መዝ. 35፥2፤ ኤፌ. 6፥16። «የጦር መሣሪያ» ይመ.



ጋሻ፥ ጦርና ጐራዴ የያዘ ወታደር

**ጋሻ ጃግሬ፤** የጦር መሪ የጦር ዕቃ አንጋች፤ መሳ. 9፥54፤ 1ሳሙ. 14፥6-14፤ 16፥21፤ 31፥4።

**ጋብቻ፤** ወንድና ሴት በቃል ኪዳን በአንድነት ተሳስረው እንዲኖሩ በማንኛውም ኅብረተሰብ የተፈቀደና የተከበረ ሥነ ሥርዓት ነው። ጋብቻ በእግዚአብሔር እንደተመሠረተ በዘፍ. 2፥18-25 እናነባለን። ጌታችንም የጋብቻን ሥርዓት በቃሉ አጽድቆታል፤ ማቴ. 19፥3-6። በዘፍ. 2፥18-25 ካለው ክፍል የሚከተሉትን ነገሮች እናገኛለን።

1. ወንድና ሴት ተፈላላጊዎች ናቸው (ዘፍ. 2፥18-21)፥ ሆኖም በወንጌልና በሌላም ምክንያት አንዳንዶች እንዳያገቡ ተጠርተዋል፤ ማቴ. 19፥7-12፤ 1ቆሮ. 7።

2. የሴቲቱ ኀላፊ የሆነው ሰው ካላቀረበለት በስተቀር ወንዱ ሊወስዳትና ሊያውቃት አይፈቀድለትም፤ ይህም ተቀባይነት ካለው ጋብቻ ውጭ የግብረ ሥጋ ግንኙነት ማድረግ በእግዚአብሔር የተከለከለ መሆኑን የሚያሳይ ነው፤ ዘፍ. 2፥22፤ ዘጸ. 20፥14:17፤ ዕብ. 13፥4።

3. እግዚአብሔር ሴትን ፈጥሮ ለአዳም በማቅረብ፥ በጋብቻ ሥርዓት የአባትንና የካህንን ድርሻዎች ፈጸመ፤ ዘፍ. 2፥21:22።

4. ወንድ ሚስት ሲያገባ ለራሱ ቤት መርቶ ወላጆቹን ትቶ መሄድ አለበት፤ ዘፍ. 2፥24።

5. ባልና ሚስት ሞት እስኪለያያቸው ድረስ ወደ ሌላ መመልከት የለባቸውም፤ ዘፍ. 2፥24።

6. «ሁለቱ አንድ ሥጋ ይሆናሉ»፤ ሥጋዊ ግንኙነታቸው የአንድነታቸው ምልክትና ማኅተም ነውና። «ዐወቀ» በሚል ግሥም ብዙ ጊዜ ይገለጣል፤ ዘፍ. 2፥24፤ 4፥1።

7. ጋብቻ አስደሳችና የማያሳፍር ሊሆን የሚችለው ወንዱና ሴቲቱ በአንድነት እግዚአብሔርን ሲከተሉ ነው፤ ዘፍ. 2፥25፤ ዘዳ. 7፥1-4፤ 1ቆሮ. 7፥39።

በተራ ቍጥር 1-7 መሠረት፥ ከሰው ውድቀት የተነሣ የተከሠቱ ሦስት ተጨማሪ ነጥቦችን መመልከት አለብን ፦

8. ጌታ ኢየሱስ «እንግዲህ እግዚአብሔር አንድ ያደረገውን ሰው አይለየው» ብሎ ስላስተማረ፥ በዝሙት ምክንያት ካልሆነ በቀር ፍች አይፈቀድም፤ ማቴ. 19፥1-6። «መፋታት» ይመ.

9. ክርስትናን ሳይቀበሉ በአረማዊ ባህል ሲኖሩ ከአንድ በላይ ሚስቶችን ያገቡ ክርስትናን ሲቀበሉ፥ ስለ ሚስቶቻቸው ምን ማድረግ እንደሚገባቸው ሁለት ዓይነት አስተሳሰብ አለ ፦

አንዳንዶች፥ «ከአንዲቱ በስተቀር ሌሎችን ፍቱ» በማለት የጋብቻ ቅድስና እንዲጠበቅ ትኵረት ይሰጣሉ። ይህም በብዙዎች ዘንድ ተቀባይነት ያለው ውሳኔ ነው።

ሌሎች ደግሞ «ሚስቶችን ማባረር ትልቅ ግፍ ነው፤ እንደ ዳዊት ብዙ ሚስቶችን ቢያገቡም፥ እንዲፈቱአቸው አልታዘዙም። ስለዚህ ቤ.ክ. ከማመኑ በፊት ከአንድ በላይ ሚስቶች የነበሩትን ሰው ከሚስቶቹ ጋር መቀበል አለባት» ይላሉ። ከዚህም ጋር ይህ ዐይነቱ ሰው በቤ.ክ. ውስጥ ኀላፊነት ወይም ሹመት ሊሰጠው እንደማይገባ (1ጢሞ. 3፥2፤ ቲቶ 1፥6)፤ አዲሱን ትውልድም በአንድ ሚስት ተወስኖ ይኖር ዘንድ ማስተማር አስፈላጊ መሆኑን በትኵረት ይገልጣሉ።

10. ጋብቻ የእግዚአብሔርና የቤተ እስራኤል (ሆሴዕ 2፥21፤ ኤር. 3፥14)፥ የክርስቶስና የቤ.ክ. ምሳሌ ነው፤ 2ቆሮ. 11፥2፤ ኤፌ. 5፥23-33። አዳም በሴቲቱ እንደተደሰተ ሁሉ (ዘፍ. 2፥23)፥ ባልም በሚስቱ ሊደሰትና ራሱን ለእርሷ መሥዋዕት አድርጎ እስኪሰጥ ድረስ ሊወድዳት ይገባዋል፤ ኤፌ. 5፥25-26። ባልና ሚስት በእግዚአብሔር መልክ በመፈጠራቸው፥ በማንነታቸው (ዘፍ. 1፥27)፥ በክርስቶስ ከሆኑም በመዳናቸው እኩል ናቸው፤ ገላ. 3፥28፤ 1ጴጥ. 3፥7። ቤ.ክ. ለክርስቶስ መታዘዝ እንደሚገባት ሁሉ፥ ሚስት በባሏ ፍቅር እንደተደሰተች ባሏን እንደ ራሷ አክብራ ልትገዛለት ታገዛለች፤ ዘፍ. 3፥16፤ መክ. 9፥9፤ 1ቆሮ. 11፥3:9፤ ኤፌ. 5፥22-33፤ ቆላ. 3፥18-19፤ ቲቶ 2፥4-5፤ 1ጴጥ. 3፥1-7።

**ጋት፤** የአራት ጣት ስፋት። ለመለኪያ ሲሆን፥ 7.4 ሳንቲሜትር ያህል ነው፤ ዘጸ. 25፥25፤ 1ነገ. 7፥26። «ርዝመት» ይመ.

**ጋኔን፤** አጋንንት፤ ሰይጣንን የሚከተሉ ርኩሳን መናፍስት፤ ሉቃ.10፥17-20። ደረጃቸውና ዓይነታቸው ብዙ ነው፤ ኤፌ. 6፥12። ሰውን ፦ ዕውር፥ ዲዳ፥ ደንቆሮ፥ ዕብድ፥ ጎባጣ ሊያደርጉ፥ ራስንም እስከ መግደል ሊያደርሱ ይችላሉ፤ ማቴ. 12፥22፤ ሉቃ. 8፥22-36፤ 13፥11፤ ማር. 9፥22። አጋንንት ክርስቶስን ያውቃሉ። እውነትንም አስተውለው ይንቀጠቀጣሉ፤ ማቴ. 8፥29፤ ያዕ. 2፥19። ብዙ መናፍስት በአንድ ሰው ሊያድሩ፥ በእንስሳትም ሊገቡ ይችላሉ፤ ማር. 5፥9-13። አጋንንት በጣዖት ዘንድ ይገኛሉ፤ 1ቆሮ. 10፥20-22፤ ራእ. 9፥20። በቤ.ክ. ገብተው ሰዎችን ሊያታልሉ ይሞክራሉ፤ 1ጢሞ. 4፥1-2። አጋንንት በቀትር ሰዓት ይሠለጥናሉ፤ መዝ. 91፥6። በአይሁድ ዘንድ አጋንንትን የሚያወጡ ይገኙ ነበር፤ ማቴ. 12፥27፤ 7፥22፤ ሐ.ሥ. 19፥13-16። ክርስቶስ ሰይጣንን አሸንፎ (አስሮ) ከብዙ ሰዎች አጋንንትን አወጣ፤ ማቴ. 12፥28-30። ክርስቶስ ለዐሥራ ሁለቱ ደቀ መዛሙርት በአጋንንት ላይ ሥልጣን ሰጣቸው፤ ሰባ ተከታዮቹም በኢየሱስ ስም አጋንንትን አወጡ፤ ሉቃ. 9፥1፤ 10፥17። ምእመናን በመንፈስ ቅዱስ እየተመሩ አጋንንትን ሊያውቁአቸውና ሊያወጡአቸው ይችላሉ፤ 1ቆሮ. 12፥10፤ 1ዮሐ. 4፥1-3፤ ማር. 16፥17። ሰው ከጋኔን ቁራኛ ከዳነ፥ ሕይወቱ በእግዚአብሔር መንፈስ እንዲሞላ ያስፈልጋል። አለበለዚያ አጋንንት ተመልሰው ሊያድሩበት ይችላሉ፤ ማቴ. 12፥43-45።

**ጋዛ፤** ምሽግ ማለት ነው። ከአስቀሎና 20 ኪ.ሜ. ርቀት ላይ በስተደቡብ የሚገኝ ከተማ። ከአምስቱ የፍልስጥኤማውያን ከተሞች አንዱ ነበረ፤ ኢያሱ 15፥47። ሶምሶን የዚህን ከተማ በር መዝጊያ ነቅሎ በኬብሮን አንጻር ጣለው፤ መሳ. 16፥1-3። በመጨረሻም ሶምሶን በጋዛ ሞተ፤ መሳ. 16፥21:30። አሞጽ የጋዛን መፍረስ ተነበየ፤ አሞጽ 1፥6-8። ካ. 3ቀ።

**ጋይ፤** ክምር ማለት ነው። ከቤቴል በስተምሥራቅ የነበረ ከተማ። አብርሃም ድንኳኑን በዚያ ተከለ፤ ዘፍ. 12፥8። በኢያሱ ተይዘው ከነበሩት የከነዓናውያን ከተሞች ይህ ሁለተኛው ነው፤ ኢያሱ 7፥2-5፤ 8፥1-29።

**ጋድ፤** ጋድ ማለት መልካም ዕድል ማለት ነው። በዚህ ስም የተጠሩ ሁለት የታወቁ ሰዎች አሉ። 1. የያዕቆብ ሰባተኛ ልጅ፥ የልያ ባሪያ ዘለፋ ለያዕቆብ ከወለደችለት ከሁለቱ ልጆቿ የመጀመሪያው፤ ዘፍ. 30፥9-11። ከእስራኤል ነገዶች የአንዱ አባት ሆነ፥ በስሙም ነገደ ጋድ ተብሎ ተሰየመ፤ ዘፍ. 46፥16፤ 49፥19። የጋድ ነገድ እንደ ሮቤል ነገድና እንደ ምናሴ ነገድ እኩሌታ ከሙሴ በለመኑት መሠረት ከዮርዳኖስ በስተምሥራቅ ርስትን ተቀብለው ኖሩ፤ ዘኁ. 32፤ ኢያሱ 22። ካ. 3ሸ።

2. በሳኦልና በዳዊት ዘመነ መንግሥት የነበረ ነቢይ። ይህ ነቢይ ዳዊትን መከረው፤ 1ሳሙ. 22፥5፤ 2ሳሙ. 24፥11-19፤ 1ዜ.መ. 21። የዳዊትን ታሪክ ጻፈ፤ 1ዜ.መ. 29፥29። የቤተ መቅደስን ሥነ ሥርዓት አስከበረ፤ 2ዜ.መ. 29፥25።

**ጋጋኖ፤** ድምፁ ወፍራም የሆነ፥ ምግብን ከረገረግ የሚፈልግ አሞራ፤ ዘሌ. 11፥18። «ወፎች» ይመ.

**ጋጣ፤** ጋጥ፤ በቤት ውስጥ የሚሠራ የከብት ማደሪያ፤ ኢሳ. 1፥3፤ ዕን. 3፥17።

**ጌልገላ፤** በኢያሪኮና በዮርዳኖስ መካከል ያለው ስፍራ። ማንከባለያ ማለት ነው፤ ኢያሱ 5፥9። እስራኤላውያን ዮርዳኖስን ከተሻገሩ በኋላ ለመጀመሪያ ጊዜ በጌልገላ ሰፈሩ፤ የማደሪያ ድንኳንም ተከሉ፤ ኢያሱ 4፥19:20። በጌልገላም ሳኦልን አነገሡ፤ 1ሳሙ. 11፥15። ሳሙኤል ሳኦልን በጌልገላ ወቀሰ፤ የአማሌቅንም ንጉሥ አጋግን ገደለ፤ 1ሳሙ. 15፥10-33። ከዚህም ውጭ ጌልገላ ተብሎ የሚጠራ ሌላ ቦታ ነበር፤ ዘዳ. 11፥30፤ ኢያሱ 12፥23። ካ. 3ሸ።

**ጌልጌል፤** የሠረገላ መንኰራኩር፤ ሕዝ. 10፥13።

**ጌሤም፤** በግብጽ ውስጥ በስተሰሜን ምሥራቅ ጠረፍ፥ ወደ ከነዓን የሚቀርብና በራምሴ አቅራቢያ የእስራኤል ልጆች የተቀመጡበት ለም ምድር፤ ዘፍ. 45፥10፤ 46፥28፤ 47፥11:27፤ ዘጸ. 8፥22፤ 9፥26።

**ጌራራ፤** ከጋዛ ወደ ደቡብ ዐሥር ኪ.ሜ. ርቆ የሚገኝ ከተማ። አብርሃምና ይስሐቅ በረሃብ ምክንያት ተሰድደው በጌራራ ይኖሩ ነበር፤ ዘፍ. 20፤ 26። የይሁዳ ንጉሥ አሳ በጌራራ ኢትዮጵያውያንን አሸነፈ፤ 2ዜ.መ. 14፥13።

**ጌርጌሳውያን (ጌርጌሴዎን)፤** ከከነዓን የተገኘ ወገን፤ ዘፍ. 10፥15-18። ኢያሱ ድል አድርጓቸዋል፤ ኢያሱ 24፥11።

**ጌርጌሴኖን፤** ከገሊላ ባሕር በስተደቡብ ምሥራቅ በኩል በሳዳራ ከተማ አቅራቢያ የኖረ ሕዝብ፤ ማቴ. 8፥28። ካ. 5ለ።

**ጌባ፤** ከኢየሩሳሌም በስተሰሜን 12 ኪ.ሜ.፥ ከገባዖንም 5 ኪ.ሜ. ርቆ የሚገኝ ምሽግ። ለይሁዳ መንግሥት ሰሜናዊ የድንበር ከተማ ነበረ፤ 2ነገ. 23፥8። በ1ሳሙ. 13፥2:3 ናሲብና ጌባ ተብሎ የተጠቀሰው አንድ ይመስላል።

**ጌባል፤** «ገሪዛን» ይመ.

**ጌታ፤** በላይ ያለ፥ የሚከበር፥ ኀላፊነት ያለው፤ ሌሎች የሚታዘዙለት፤ አክብሮትን (ዘፍ. 23፥6)፥ ሥልጣንን (ዘፍ. 44፥18)፥ ገዥነትን (ዘፍ. 42፥33)፥ ባለቤትነትን (ዘፍ. 39፥16) እና መምህርነትን ያሳያል፤ 2ነገ. 4፥16። ቃሉ በቅጽልነትም ሆነ ለብቻ ለእግዚአብሔር ይነገራል፤ ሉቃ. 1፥68፤ 2፥9፤ ሐ.ሥ. 4፥26:29። በተለይም ኢየሱስ ክርስቶስ በዚህ ስም ብዙ ጊዜ ይጠራል። «ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ» ብለን እንጠራዋለንና ስለ እግዚአብሔር የተጻፈው በጌታ በኢየሱስ ክርስቶስ ተፈጽሟል፤ ኢየሱስ እግዚአብሔር መሆኑን ያስረዳል፤ ኢሳ. 40፥3 እና ሉቃ. 3፥3-6 ያስተያዩ። ደቀ መዛሙርት ኢየሱስን «ጌታ» ሲሉት ማንነቱን አልተረዱም ነበር። ከትንሣኤ በኋላ ግን የኢየሱስ ጌትነት እንዴት እንደሆነ ተረዱ፤ ዮሐ. 20፥28። ከሁሉ በላይ መሆኑንም ዐወቁ፤ ሐ.ሥ. 2፥36፤ ሮም 14፥7-10።

**የጌታ ቀን፤** «ሰንበት» ይመ.

**የጌታ እራት፤** «ቅዱስ ቍርባን» ይመ.

**የጌታ ወንድሞች፤** ያዕቆብ፥ ዮሳ፥ ስምዖን፥ ይሁዳ፥ እኅቶቹም አብረው በናዝሬት ከኢየሱስ ጋር እንዳደጉና እንደኖሩ ተገልጧል፤ ማቴ. 13፥55-56። ሆኖም አላመኑበትም፤ ዮሐ. 7፥1-10። ያዕቆብ ከትንሣኤ በኋላ ኢየሱስን አይቶ አመነ፤ 1ቆሮ. 15፥7፤ ገላ. 2፥9። ከኢየሱስ ጋር ወንድምነታቸው በምን በኩልና እንዴት እንደሆነ መ.ቅ. አይገልጥም። ኢየሱስ ከሥጋዊ ዝምድና ይልቅ መንፈሳዊ ዝምድናን ከፍ ያደርግ ነበር፤ ማር. 3፥35። ከአ.ኪ. መልእክቶች መካከል ሁለቱ በያዕቆብና በይሁዳ ተጽፈዋል፤ ይሁዳ 1፤ ገላ. 1፥19።

**ጌቴሴማኒ፤** ከኢየሩሳሌም በቄድሮን ወንዝ ማዶ በደብረ ዘይት ግርጌ ያለ የአትክልት ስፍራ። ስሙ በአራም ቋንቋ (በአራማይክ) የዘይት መጥመቂያ ማለት ነው። ኢየሱስ በጌቴሴማኒ ከጸለየ በኋላ ተያዘ፤ ማር. 14፥32-42፤ ዮሐ. 18፥1-12።

**ጌት፤** ከ5 የፍልስጥኤም ከተሞች ጌት አንዱ ነበረ። የኤላ ሸለቆ ምሽግ፥ የጎልያድም አገር ነበረ።

ዳዊት ከጌት ንጉሥ ከአንኩስ ለማምለጥ ዕብድ መስሎ ታየ (1ሳሙ. 21፥10-15)፤ በኋላም አንኩስን እታልሎ በጌት ኖረ፤ 1ሳሙ. 27፥4-12። ንጉሥ በሆነ ጊዜም ስድስት መቶ የጌትን ሰዎች አስከተለ፤ 2ሳሙ. 15፥18። ከብዙ ዘመን በኋላ ግን ከተማው ጠፋ፤ አሞጽ 6፥2። ካ. 30በ።

**ጌንሳሬጥ**፤ «ኪኔሬት»፥ «የገሊላ ባሕር» ይመ.

**ጌዝር**፤ ከኢየሩሳሌም በሰሜናዊ ምዕራብ በኩል 30 ኪ.ሜ. ርቆ ወደ ኢዮጴ በሚወስደው መንገድ ላይ የነበረ ምሽግ። ኢያሱ የጌዝርን ንጉሥ አሸነፈ፤ ኢያሱ 10፥33። ነገር ግን ከነዓናውያን ተቀመጡበት፤ በኋላም ግብጻውያን ያዙት። ፈርዖን ለልጁ ለሰሎሞን ሚስት ጌዝርን ግጫ አድርጎ ሰጠው፤ ሰሎሞንም የሠረገላ ከተማ አደረገውና ትልቅ ምሽግ ሆነ፤ 1ነገ. 9፥15-19፤ 10፥26።

**ጌዴዎን**፤ ከእስራኤላውያን መሳፍንት አንዱ። ታሪኩ በመሳ. 6፥1-9፥6 ተጽፏል። እስራኤልን ከምድያማውያን ሊያድን ተጠራ፤ መሳ. 6፥11-24። የበአልን መሠዊያ ካፈረሰ በኋላ ይሩበአል ተብሎ ተጠራ፤ መሳ. 6፥25-32። 32,000 ሰዎች ሲወጡለት በእግዚአብሔር ትእዛዝ 300 ሰዎችን ብቻ አስከትሎ ምድያማውያንን በማባረር አሸነፋቸው፤ መሳ. 6፥33-8፥21። ሕዝቡ ንገሥልን ቢሉት እምቢ አለ። አርባ ዓመት በእስራኤል ላይ ፈራጅ ሆነ፤ መሳ. 8፥22-35። የጌዴዎን እምነት በዕብ. 11፥32 ተመስክሮለታል። በምድያም ላይ የተቀዳጀው ድል ለእግዚአብሔር የመታደግ ተግባር በምሳሌነት ይጠቀሳል፤ ኢሳ. 9፥4፤ 10፥26።

**ጌድሶን**፤ ከሦስቱ የሌዊ ልጆች ታላቁ፤ ዘፍ. 46፥11። እስራኤላውያን በምድረ በዳ ሲጓዙ ጌድሶናውያን የማኅበሩን የድንኳን መጋረጃዎች ይጠብቁና ይሸከሙ ነበር፤ ዘኁ. 3፥21-26፤ 7፥7። ዳዊት ታቦቱን ወደ ጽዮን ሲያወጣ ያገለግሉ ነበር፤ 1ዜ.መ. 15፥7።

**ግመል**፤ በጀርባው ላይ አንድ ወይም ሁለት ሻኛ ያለው የጭነት እንስሳ፤ ዘፍ. 24፥10፤ 2ነገ. 8፥9። ጠጕሩ ልብስ ይሆናል፤ ማቴ. 3፥4። ግመል ያመሰኳል፤ ግን ሰኰናው ስንጥቅ አይደለም።



ስለዚህም በእስራኤል ዘንድ ለመብል አልተፈቀደም፤ ዘሌ. 11፥4። ግመል ለትልቅ ነገር ምሳሌ ሆኖ ተጠቅሷል፤ ማቴ. 19፥24፤ 23፥24። «እንስሳት» ይመ.

**ግምባር**፤ (ግንባር) ከዐይን በላይ ያለው የራስ ክፍል፥ የሰው ጠባይ በተለይም ቊራጥነት በግምባሩ ሊገለጥ ይችላል፤ ሕዝ. 3፥8:9። ግምባር በግልጥ ስለሚታይ፥ ሰዎች በግምባራቸው ላይ የጽሑፍ ወይም የማኅተም ምልክት ያደርጉ ነበር፤ ዘጸ. 28፥38፤ ሕዝ. 9፥4፤ ራእ. 7፥3።

**ግምጃ**፤ ከልዩ ልዩ ሐርና ወርቅ የሚሠራ ልብስ፤ ወይም የተቀለመ በፍታ፤ ምሳ. 31፥22።

**ግምጋሜ**፤ የግምት ሂሳብ። በብ.ኪ. ዘመን ሰዎች ባለማወቅና በስሕተት ሲበድሉ፥ በካህኑ ግምት ወይም ግምጋሜ መጠን መሥዋዕት ያቀርቡ ነበር፤ ዘሌ. 5፥15፤ 6፥6።

**ግሪክ**፤ ከጥንት የተገኘ ከፍ ያለ ሕዝብና መንግሥት። አገሩ በመጀመሪያ በብ.ኪ. «ያዋን»፥ በአ.ኪ. «አካይያ» ተባለ። በታላቁ እስክንድር ጊዜ (እስክንድር 333 ከክ.በ. ሞተ) የግሪክ ሰዎች እስከ ሕንድ ድረስ ዘመቱ፤ ዳን. 8፥21። በየአገሩ ሲኖሩ ታላላቅ ሕንጻዎችን ሠሩ። ሥልጣኔአቸውን፥ ትምህርታቸውንና ቋንቋቸውን አስፋፉ። አንድ መቶ ዓመት ያህል ከክርስቶስ በፊት የሮም መንግሥት የግሪክን መንግሥት አሸነፈ። ቢሆንም በግብጽ፥ በእስያ፥ በጠቅላላው ከታላቁ ባሕር በስተምሥራቅ በኩል በሚገኙት አገሮች የግሪክ ትምህርት፥ ባህልና ቋንቋ የታወቀ ነበር። ስለዚህ በሐዋርያት ዘመን ማናቸውም ሰው የሠለጠነ ከሆነ ግሪክ ይባል ነበር፤ ማር. 7፥26፤ ሐ.ሥ. 21፥37-39፤ ሮም 1፥14።

አዲስ ኪዳን ግሪክ ሲል ብዙ ጊዜ ከአይሁድ ወገን ያልሆነውን ያመለክታል፤ ሐ.ሥ. 11፥20። ብዙ የግሪክ ሰዎች ሳይገረዙ በምኵራቦች ያመልኩ ነበር፤ ዮሐ. 12፥20፤ ሐ.ሥ. 14፥1፤ 17፥4፤ 18፥4። በአ.ኪ. ዘመን ዋናው የግሪክ አገር መቄዶንያና አካይያ የሚገኙበት ነበረ (ሐ.ሥ. 20፥2)፤ የአሁኑም የግሪክ አገር ያው ነው።

**ግሪክ**፤ የግሪካውያን ቋንቋ ማለት ነው። በግእዝ መ.ቅ. ጽርእ፥ በአማርኛም ግሪክ ተብሎ ይጠራል፤ ዮሐ. 19፥20፤ ሐ.ሥ. 21፥37። ከክርስቶስ ዘመን በፊት የግሪክ ሥልጣኔ በብዙ አገሮች ተስፋፍቶ ነበረና የግሪክ ቋንቋ በሜዲቴራንያን ባሕር ዙሪያ ላሉት ሕዝቦች የጋራ መገናኛ ቋንቋ ሆነ።

የአ.ኪ. መጻሕፍት በግሪክ ቋንቋ ተጻፉ። የጌታና የሐዋርያት ቋንቋ አራማይክ ስለሆነ አራቱ ወንጌላውያን ጌታ በአራማይክ የተናገረውን ቃል ወደ ግሪክ ተርጕመው ጽፈውታል፤ ይህን ከማድረጋቸው በፊት ግን ልዩ ልዩ ማስታወሻ በአራማይክ ሳይጽፉ አልቀሩም።

የብ.ኪ. መጻሕፍት ከዕብራይስጥ ወደ ግሪክ ተተረጐሙ፤ «የቅዱሳት መጻሕፍት ትርጓሜ» ይመ.


የግሪክ አማልክት

በአክሱም መንግሥት የግሪክ ሥልጣኔ ተስፋፍቶ ነበረና አያሌ የግሪክ ቃላት ወደ ግእዝና ወደ አማርኛ ገብተዋል፤ ለምሳሌ ጠረጴዛ፥ ጳጳስ፥ ጰራቅሊጦስ፥ ኢትዮጵያ የግሪክ ቃላት ናቸው።

የግሪክ ፊደሎችም የሚከተሉት ናቸው ፡-

| | | | |
|---|---|---|---|
| α | አልፋ | ν | ኑ |
| β | ቤታ | ξ | ክሳይ |
| γ | ጋማ | ο | አሚክሮን |
| δ | ደልታ | π | ፓይ |
| ε | እፕሲሎን | ρ | ሮ |
| ζ | ዜታ | σ | ስግማ |
| η | ኢታ | τ | ታው |
| θ | ቴታ | υ | ኡፕሲሎን |
| ι | እኦታ | φ | ፋይ |
| κ | ካፓ | χ | ካይ |
| λ | ላምብዳ | ψ | ፕሳይ |
| μ | ሙ | ω | ዖሜጋ |

**ግራ**፤ የቀኝ ተቃራኒ፤ ምሳ. 4፥27፤ ማቴ. 25፥33:41። አንዳንድ ጊዜ ግራ የክብር ምሳሌነት ቢኖረውም እንደ ቀኝ አይሆንም፤ ምሳ. 3፥16፤ መ.መ. 2፥6፤ ማቴ. 6፥3፤ 20፥21:23።

**ግርግም**፤ በቤት ወይም በበረት ውስጥ የሚገኝ የከብት ምግብ መስጫ፥ እንደ ገንዳ ያለ ቋት፤ ኢዮብ 39፥9፤ ሉቃ. 2፥7። አንዳንዴም በረት ግርግም ይባላል፤ ሉቃ. 13፥15።

[illegible] ይፈጸም የነበረ ቅጣት። በሙሴ ሕግ እስከ አርባ ጊዜ በበትር ወይም በአለንጋ መምታት ተፈቅዶ ነበር፤ ዘዳ. 25፥3፤ 2ቆሮ. 11፥24። የምኵራብ አለቆች ጥፋተኞችን ይገርፉ ነበር፤ ማቴ. 10፥17፤ ሐ.ሥ. 5፥40።

በሮማውያን ዘንድም ተደረገ፤ ማቴ. 27፥26። ነገር ግን የሮም ዜግነት ያለው ያለ ፍርድ እንዲገረፍ አልተፈቀደም ነበር፤ ሐ.ሥ. 22፥24:25። እነርሱ የተጠቀሙት በበትር ወይም በጅራፍ ነበር። የግርፋት ቍጥርም አልተወሰነም።


ብረታ ብረትና አጥንት የተሰካበት የሮም ጅራፍ

**ግብር**፤ በበላይ ላለው የሚሰጥ ንብረት ወይም አገልግሎት። አንድ መንግሥት ግብርን በማስገበር ለማስተዳደር አስፈላጊውንና የሚመቸውን ነገር ያደርጋል። የእስራኤል ሕዝብ በየዓመቱ ለመቅደስ ግማሽ ሰቅል ይከፍሉ ነበር፤ ዘጸ. 30፥13፤ 38፥25:26፤ ማቴ. 17፥24-27። እስራኤል ከነዓናውያንን የጕልበት ግብር አስገበሩ፤ ኢያሱ 16፥10፤ 2ዜ.መ. 8፥8። ኢዮሣፍጥ ከፍልስጥኤማውያንና ከዐረባውያን ብርንና ከብትን አስገበረ፤ 2ዜ.መ. 17፥11። በብ.ኪ. ዘመን አንድ መንግሥት ሌላውን ሲያሸንፍ ያስገብረው ነበር፤ 2ነገ. 23፥33፤ ዕዝ. 4፥13፤ አስ. 10፥1። ሮማውያን ግብርን እንዲቀበሉ በየዐሥራ አራት ዓመቱ ዓለሙን ሁሉ ይመዘግቡ ነበር፤ ሉቃ. 2፥1:2። በየአገሩም ቀራጮችን መድበው ነበር። አይሁድ ለቄሣር ገበሩ። ምእመናን ግብርንና ቀረጥን መክፈል ይገባቸዋል፤ ማቴ. 17፥24፤ ሮም 13፥6:7። «ቀራጭ» ይመ.

**ግብር**፤ የንጉሥ ወይም የማንኛውም ሰው ሰፊ ግብዣ፤ 1ሳሙ. 20፥24:27:34።

**ግብርና፤** በመጀመሪያ እግዚአብሔር ሰው ምድርን እንዲያርስና እንዲጠብቃት፡ ፍሬዎቹንም እንዲበላ አዘዘው፤ ዘፍ. 2፥15፤ 3፥19:23። ቀጥሎም ሌሎቹ ሁሉ ግብርናን ወረሱ፤ ዘፍ. 4፥3:4። ግብርና በእስራኤል አገር ዋና ሥራ ነበረ። እያንዳንዱ ቤተሰብ በድንበር ምልክት የተወሰነ መሬት ነበረው፤ ዘዳ. 19፥14። ዝናብ መሬቱን ካራሰው በኋላ በኅዳርና በታኅሣሥ እርሻ ይጀምራሉ። መከር ከፋሲካ እስከ በዓለ ኀምሳ ነበረ። እህል ሲያጭዱ ለድሆች ቃርሚያ ይተዉ ነበር፤ ድሆችም እየተከተሉ ይቃርማሉ፤ ዘሌ. 19፥10፤ ሩት 2፥2። እህላቸውን በአውድማ አከማችተው በከብት እያሄዱ ይወቃሉ፤ ዘዳ. 25፥4። ከዚያም በኋላ በመንሽ ያበጥሩታል፤ በወንፊትም ያንጠረጥሩታል፤ ኢሳ. 30፥24፤ 41፥16። ዋና እህላቸው ስንዴና ገብስ ሲሆን፥ ሌላም ልዩ ልዩ እህልና አትክልት ነበራቸው። «ምግብ» ይመ.

**ግብዝነት፤** ያልሆነውን ወይም የማያውቁትን ለመምሰል መመጻደቅ ማለት ነው። በተለይ በሃይማኖት በሙሉ ልብ ከእግዚአብሔር የራቀ ሲሆን፥ በሰው ፊት ራስን ጻድቅ ማድረግ ነው፤ ማር. 7፥6:7፤ 2ጢሞ. 3፥5። ኢየሱስ ፈሪሳውያንንና ጻፎችን ስለ ግብዝነታቸው አጥብቆ ወቀሳቸው፤ ማቴ. 6፥2:5:16፤ 7፥5፤ 15፥7፤ 22፥18፤ 23፤ ማር. 12፥15፤ ሉቃ. 12፥1:56፤ 13፥15። ፍቅራችንና እምነታችን እውነተኛና ያለ ግብዝነት እንዲሆን ያስፈልጋል፤ ሮም 12፥9፤ 2ቆሮ. 6፥6፤ 1ጴጥ. 1፥22፤ 1ጢሞ. 1፥5፤ 2ጢሞ. 1፥5፤ ገላ. 2፥11-14።

**ግብዣ፤** በአይሁድ ኅብረተሰብ ዘንድ አብሮ መብላትና መጠጣት፥ መዘመር፥ በጠቅላላም መደሰት የተለመደ ነበር፤ ሉቃ. 15፥23-25። ግብዣ ለተወለዱበት ዕለት መታሰቢያ (ዘፍ. 40፥20)፥ ለሰርግ ቀን (ዘፍ. 29፥22)፥ ለወይን ለቀማ (መሳ. 9፥27)፥ ለበግ ሸለታ (1ሳሙ. 25፥2:36) ለሌላም ጉዳይ ይደረግ ነበር፤ ለተጋባዦች 2ኛ የማሳሰቢያ ጥሪ ይደረጋል፤ ሉቃ. 14፥17። ተጋባዦች ሲደርሱ ይሳሙ፥ እግራቸውን ይታጠቡ፥ ራሳቸውንም በዘይት ይቀቡ ነበር፤ ሉቃ. 7፥44-46።

**ግብጽ፤** በሰሜን አፍሪካ የሚገኝ አገር። ካ. 1መ።

በመ.ቅ. ምጽራይም የሚለው ቃል (ዘፍ. 10፥6)፥ በዐረብኛ ምስር ይባላል። ደግሞም የካም አገር ይባላል፤ መዝ. 105፥23:27። ዝናብ በግብጽ ብዙ ጊዜ ስለማይገኝ ሕዝቡ ከዓለም ወንዞች በታላቅነቱ በታወቀው በዓባይ ወንዝ ይጠቀማሉ። የግብጽ ነገሥታት ፈርዖን ይባሉ ነበር። ከአብርሃም ዘመን በፊት ጀምሮ ግብጽ የሠለጠነ አገር ነበር። ነገሥታት ለመቃብሮቻቸው ታላላቅ ግንቦችን (ፒራሚዶች) ይሠሩ ነበር። በግብጽ ብዙ ዓይነት ኪነ ጥበብና ጌጣጌጥ ነበረ፤ የመንግሥት ሕግና አስተዳደር የታወቀ ነበር። እንዲያገለግሉአቸው እንደ እስራኤል ያሉ ልዩ ልዩ ሕዝቦችን አስገደዱ። ከእነዚህም ነገዶች ውስጥ እንደ ሙሴና እንደ ዮሴፍ ያሉት በቤተ መንግሥት ተሾሙ።

አብርሃም በራብ ምክንያት ወደ ግብጽ ወረደ፤ ዘፍ. 12፥10። ዮሴፍ ወደ ግብጽ ተሸጠ፤ ታላቅ ሰው ሲሆን አባቱንና ወንድሞቹን ወደዚያ ወሰደ፤ መሬትም ሰጣቸው፤ ዘፍ. 47፥27። በኋላም ግብጻውያን እስራኤላውያንን ለ400 ዓመት ያህል ባሪያዎች አደረጉአቸው (ሐ.ሥ. 7፥6)፤ ከተማዎችን እንዲሠሩላቸው አስገደዱአቸው፤ ዘጸ. 1፥8-14። እግዚአብሔር ግብጻውያንን ቀሠፈ፤ እስራኤል በሙሴ መሪነትና በእግዚአብሔር ኃይል ቀይ ባሕርን ተሻግረው ከግብጽ ወጡ።

እስራኤል ከነዓንን ከያዙ በኋላ ከግብጽ ጋር በንግድ ተገናኙ። ሰሎሞን የፈርዖንን ልጅ አገባ፤ 1ነገ. 3፥1፤ 10፥28:29። ኢዮርብዓም ከሰሎሞን ወደ ግብጽ ሸሸ። የግብጽ ንጉሥ ሺሻቅ በሰሎሞን ልጅ በሮብዓም ላይ ዘመተ፤ 1ነገ. 12፥2፤ 14፥25። ከሰሎሞን ጊዜ ጀምሮ የግብጽ መንግሥት እየደከመ ሄደ፤ እስራኤላውያን አሦርን ለመቃወም በግብጽ እንደተማመኑ ብለው ተስፋ አደረጉ፥ ተስፋቸው ግን ከንቱ ሆነ፤ 2ነገ. 17፥1-6። እንደዚሁም አንዳንድ የይሁዳ ሕዝብ በግብጽ ተስፋ አደረጉ፤ ኢሳ. 20። በኋላም የግብጽ ንጉሥ ኒካው የይሁዳን ንጉሥ ኢዮስያስን በመጊዶ ገደለው፤ ኤልያቄምን በኢዮአቄምም አነገሠ፤ 2ነገ. 23፥28-35። ኒካው ግን ከርከሚሽ ላይ በናቡከደነፆር ተሸነፈ፥ እንደ ገናም ግብጻውያን ወደ ይሁዳ አልዘመቱም፤ 2ነገ. 24፥7፤ ኤር. 46፥2። በይሁዳ መንግሥት መጨረሻ ከባቢሎን ኃይል ለማምለጥ ብዙ አይሁድ ኤርምያስን ይዘው ወደ ግብጽ ወረዱ (ኤር. 43)፤ ብዙ አይሁድ በግብጽ አገር ኖሩ።

ከዚያም በኋላ ግብጽ መጀመሪያ በግሪክ፥ በኋላም በሮም መንግሥት ተገዛ። ብ.ኪ. ከዕብራይስጥ ወደ ግሪክ በ70 ሊቃናት በግብጽ አገር ለመጀመሪያ ጊዜ ከክርስቶስ ልደት በፊት ከመቶ ዓመት በላይ ተተረጐመ። ኢየሱስ ከሄሮድስ ለመዳን ወደ ግብጽ ተወሰደ፤ ከዚያም ወደ ናዝሬት መጣ፤ ማቴ. 2፥13-15:19-21። ከብዙ ዓመታት በፊት ኢሳይያስ «እግዚአብሔር በግብጽ የታወቀ ይሆናል» የሚል ትንቢት ተናግሮ ነበር፤ ኢሳ. 19፥19-25። ግብጻውያን በጰንጠቆስጤ ቀን በኢየሩሳሌም ነበሩ፤ ሐ.ሥ. 2፥10። አጵሎስ የእስክንድርያ ሰው ነበረ፤ ማርቆስ በግብጽ ወንጌልን እንደሰበከ በቤ.ክ. ታሪክ ይተረካል።

**የግብጽ ወንዝ፤** በግብጽና በከነዓን፥ በኋላም በግብጽና በይሁዳ መካከል ድንበር ነበረ፤ ዘፍ. 15፥18፤ ዘኍ. 34፥5፤ ኢያሱ 15፥4:47። ዋናው የግብጽ ወንዝ ዓባይ ነው። ብዙ ገባር ወንዞች አሉት። ሆኖም ድንበሩ የአሁኑ የስዌዝ መስና የሚገነባበትን ልሳነ ባሕር የሚያመለክት ይመስላል። «ዓባይ» ይመ.

**ግንብ፤** ጠላት ሲመጣ ሕዝብ የሚሸሸበት፥ በከተማ ቅጥር ላይም ጠላትን የሚከላከልበት፤ 2ዜ.መ. 14፥7፤ 26፥9፤ ማቴ. 21፥33። አሠራሩ አንዳንድ ጊዜ ክብ፥ አንዳንድ ጊዜም ባለ ማዕዘን ይሆናል።

**ግንኙነት፤** ተራርቀው የነበሩ ሰዎች ሲቀራረቡ፤ ዘፍ. 33፥4። ሁለት ተቃራኒ ጾታዎች በግብር ሲገናኙ፤ ዘፍ. 19፥31። ሰው ከፈጣሪው ጋር በመንፈስ ሲገናኝ፤ አሞጽ 4፥12።

**ግንድ (የእግር)፤** ቀዳዳ ያለው ሆኖ ከእንጨት የሚሠራ መንቁር፥ የወንጀለኛ ማሰሪያ፤ ኤር. 20፥2፤ ሐ.ሥ. 16፥24።



የሰዎች እግር በግንድ እንደተጠረቀ

**ግኖስቲክ፤** ቃሉ ዕውቀት ተብሎ ከሚተረጐም የግሪክ ቃል የመጣ ነው። ከግሪክ ዓለም ብዙ ሰዎች ደኅንነት የሚገኘው ዕውቀትን በማግኘት ነው ብለው ያምኑ ነበር። የግኖስቲክ አስተሳሰብ ወደ ቤ.ክ. በልዩ ልዩ ዓይነት ይገባ ነበርና ሐዋርያት ተቃወሙት።

የግኖስቲክ አሳብ ብዙና የተለያየ ነበር። ዋና ዋና ትምህርታቸው እንደሚከተለው ነው። (ሐዋርያት ትምህርቱን የተቃወሙባቸው አንቀጾች በቅንፍ ውስጥ ተጽፈዋል)።

1. ሰው በዕውቀት እግዚአብሔርን ያገኛል። ይህ ዓይነት አስተሳሰብ ግን ኩራትንና ብዙ ዓይነት የማይረባ መለፍለፍን ያስከትላል (1ጢሞ. 1፥3:4፤ 6፥20)።

2. እውነተኛው ዓለም መንፈሳዊ ነው። ይህ ዓለም የእውነተኛው ጥላ ብቻ ነው። ስለዚህ ክርስቶስ በሥጋ እንደመጣ አያምኑም (1ዮሐ. 4፥3፤ 2ዮሐ. 7)።

3. ሰው የሚድነው ከተፈጠረው ዓለም በመለየት ነው። አንዳንዶች ይህ የሚፈጸመው ሥጋን በመግዛትና በማድከም እንደሆነ አስተማሩ። ይህንም አምነው ጋብቻን፥ ልዩ ልዩ ዓይነት ምግብንም ከለከሉ (1ጢሞ. 4፥3-5)። ትንሣኤም በመንፈስ እንደሆነ ተረጐሙ (2ጢሞ. 2፥18)። ሌሎች ግን እውነተኛው ዓለም መንፈሳዊ በመሆኑ ሥጋዊ ድርጊት ለውጥ እንደማያመጣ አስበው የፈለጉትን አደረጉ (2ጢሞ. 3፥6:7)።

4. እግዚአብሔር መሠረታዊ የሆነ አንድ ነገርን ፈጠረ፤ ቀጥሎም ሌላ ነገር ከዚያ ወጣ፥ በኋላም ከዚህ የተለያዩ ነገሮች እየወጡ በመጨረሻ ይህ የሚታየው ዓለም ተገኘ። ስለዚህ በዓለምና በእግዚአብሔር መካከል ብዙ ደረጃዎች ይገኛሉ (ቆላ. 1፥19:20፤ 2፥8-15)።

5. ሰው የሚድነው በዐዋቂዎች መካከል በሚደረግ ሥርዓትና ወግ ነው ይሉ ነበር (ቆላ. 2:16-23)።

**ግእዝ፤** የቋንቋ ስም። የግእዝ ቋንቋ በአማርኛ መ.ቅ. ውስጥ ተጠቅሶ አይገኝም። በግእዝ አ.ኪ. ግን በአንዳንድ ግልባጮች በዮሐንስ ራእይ 9፥11 በዕብራይስጥ አብዶን የተባለው የጥልቅ መልአክ በግእዝ ማሕጐሊ ይባላል ይላል። የግእዝ ዘርና የአማርኛ መ.ቅ. ቃል አልፎ አልፎ የሚለያዩበትን ስፍራ ለማመልከት የአማርኛ ተርጓሚዎች አንዳንድ ማስታወሻዎችን ጨምረዋል፤ ዘፍ. 15፥2፤ ምሳ. 25፤ 1ጴጥ. 2፥24።

**ግዝረት (ግርዛት)፤** የዘር ብልትን ሸለፈት መቍረጥ። ለአብርሃም የተሰጠ የቃል ኪዳን ምልክት ነው። ይህም ለወንድ ልጅ ብቻ ነበረ፤ ዘፍ. 17፥7-14። በሙሴ ዘመን ለእስራኤል ሕዝብ ምልክትና መለያ ሆነ፤ ዘጸ. 12፥43-45፤ 1ሳሙ. 17፥36። ፈሪሳውያን በተለይ በሙሴ እንደተሰጠ፥ እንደ ሕዝባዊና ሕጋዊ ምልክት አድርገው ቈጥረውት ነበር፤ ሐ.ሥ. 15፥1-5፤ ገላ. 5፥2-6። ክርስቶስ እንዳስታወሳቸው በመጀመሪያ የተሰጠው ለአብርሃም ነበርና መንፈሳዊ ምልክት ነው፤ ዮሐ. 7፥22።

ግዝረት የሚከተሉትን ሦስት ነገሮች ያመለክታል።

1. እግዚአብሔር የተገረዘውን ሰው ለራሱ መርጧልና አምላኩ ነው፤ ዘፍ. 17፥8:11።

2. የተገረዙት የእግዚአብሔር ሕዝብ ናቸውና ክፋትን ከሕይወታቸው ማስወገድ አለባቸው፤ ዘዳ. 10፥16፤ ኤር. 4፥4።

3. እግዚአብሔር በእምነት መሠረት ስለተቀበላቸው የጽድቃቸው ማኅተም ነው፤ ሮም 4፥11። ሥርዓት ራሱ አያድንም። ስለዚህ ሰዎች የእግዚአብሔርን ፈቃድ ማድረግ አለባቸው፤ ሮም 2፥25-29። ዋናው ነገር የልብ መለወጥ ነውና ምእመናን በመንፈስ የተገረዙ ናቸው፤ ፊል. 3፥3። በአ.ኪ. ዘመን ጥምቀት በግዝረት ተተክቷል (ቆላ. 2፥11:12)፥ ግዝረትም አሁን አይጠቅምም፤ ገላ. 5፥6፤ 6፥15። ወንድ ልጅ ተወልዶ በስምንተኛው ቀን ሲገረዝ ስም ይወጣለት ነበር፤ ሉቃ. 1፥59-63፤ 2፥21።

ግዝረት ከእስራኤል ሌላ በአንዳንድ ሕዝብም ዘንድ እንደነበረ ይታመናል። ያልተገረዘ በእስራኤል ኅብረተሰብ ዘንድ ተቀባይነት አልነበረውምና የተከለከለ ነገር ሁሉ ባልተገረዘ ሰው ተመስሏል፤ ዘሌ. 19፥23።

**ግዝት፥ ውግዘት፤** ከምእመናን አንድነት መለየት። የቤ.ክ. መሪዎች አስተዳዳሪነት የሚገለጠው የእግዚአብሔርን ቃል በማስተማር ነው፤ ሐ.ሥ.

6፥2፤ 1ጢሞ. 3፥2፤ ቲቶ 1፥9። ሆኖም ሰዎች ማስጠንቀቂያዎች ከተሰጡአቸው በኋላ ንስሓ ገብተው ባይመለሱ ከማኅበር ልታስወጣቸው የቤ.ክ. ኀላፊነት ነው፤ ማቴ. 18፥15-18፤ 2ተሰ. 3፥14:15፤ ቲቶ 3፥10፤ ራእ. 2፥14:15:20። ሐዋርያት ስለ ትምህርት (1ጢሞ. 1፥19:20፤ 2ጢሞ. 2፥17:18)፥ ስለ ክርስቲያናዊ አካሄድ ሲገዝቱ (ሲያወግዙ) እናነባለን፤ 1ቆሮ. 5፥1-5። የውግዘት ዓላማዎች 3 ናቸው። እነርሱም ቤ.ክ. ቅድስት እንድትሆን፥ ክፋቱ ወደ ሌሎች እንዳይተላለፍ፥ ሰውዬው ከኃጢአቱ እንዲመለስ ናቸው፤ 1ቆሮ. 5፥5-7፤ 2ቆሮ. 2፥6-8። ሐዋርያት በልዩ ሥልጣናቸው ገዘቱ። ሆኖም አብ.ክ. እንዲስማሙበትና እንዲተባበሩበት ምክንያት ገለጡ።

**ግዞት ቤት**፤ ፍርድ እስኪሰጥ ድረስ ወይም ያለ ፍርድ ሰው ተገልሎ የሚቈይበት ቦታ። ዮሴፍ (ዘፍ. 39፥20)፥ ሶምሶን (መሳ. 16፥21:25)፥ ነቢያትም በግዞት ቤት ተጠበቁ፤ 1ነገ. 22፥27፤ 2ዜ.መ. 16፥10፤ ኤር. 32፥2:8:12። «ወኅኒ» ይመ.

**ግያዝ**፤ የነቢዩ የኤልሳዕ ሎሌ። በመዋሸት ገንዘብ ለራሱ ስለወሰደ በለምጽ ተቀጣ፤ 2ነገ. 4፥8-37፤ 5፥1-27፤ 8፥1-6። «ለምጽ» ይመ.

**ግዮን**፤

1. ከዔድን የሚወጣ የኢትዮጵያን ምድር ሁሉ የሚከብብ ወንዝ፤ ዘፍ. 2፥13። ብዙዎች ግዮን ዓባይ ነው ይላሉ። ሌሎችም ኢትዮጵያ የኩሽ አገር ነው፤ የኩሽም መጀመሪያ አገሩ በመስጴጦምያ ነበረና ግዮን ከመስጴጦምያ ወንዞች አንዱ ሊሆን ይችላል ይላሉ፤ ዘፍ. 10፥5-8።

2. ከኢየሩሳሌም በስተምሥራቅ በቄድሮን ሸለቆ ያለው ምንጭ። ከጥንት ጀምሮ የኢየሩሳሌም ሰዎች ከግዮን ውሃ ያመጡ ነበር። ኢዮአብ በግዮን ውሃ መሄጃ ገብቶ ከተማውን ያዘ፤ 2ሳሙ. 5፥6-8። ሰሎሞን በግዮን አጠገብ ተቀብቶ ነገሠ፤ 1ነገ. 1፥33-40። ሕዝቅያስ ዓለቱን አስቆፍሮ የግዮንን ውሃ በመስና ወደ ከተማ እንዲፈስስ አደረገ፤ እስከ ዛሬም ድረስ ይፈስሳል። የመስናው ዋሻ ርዝመት 530 ሜትር፥ ቁመቱ 2ሜትር፥ ስፋቱ ደግሞ ግማሽ ሜትር ነው (2ዜ.መ. 32፥3:4:30፤ 33፥14)፤ ራፋስቂስ በቅጥር ላይ ለነበሩት አይሁድ ከግዮን አጠገብ ቆሞ ጮኸ፤ ኢሳ. 36፥2።

**ግድግዳ**፤ በብ.ኪ. ዘመን የቤት ግድግዳ አንዳንድ ጊዜ ከድንጋይ፥ ብዙ ጊዜ ከጭቃ፥ ከእንጨትና ከጡብ ይሠራ ነበር። አሕዛብ ወደ አይሁድ አደባባይ እንዳይገቡ በቤተ መቅደስ አደባባይ ግድግዳ ነበረ። ይህም በምሳሌ የጥል ግድግዳ ተባለ፤ ኤፌ. 2፥14:15።

**ግጥም**፤ የዕብራይስጥ ግጥም ከልዩ ልዩ ቃላቱና ሰዋስዉ የተነሣ ከተራ አነጋገር የተለየ ነበር፥ ብዙ ጊዜ ግን ቤት አይመታም። ዋናው ስልቱ እንደሚከተለው ነው። በእያንዳንዱ ግጥም ሁለት ክፍሎች (ስንኞች) አሉ። የሁለቱም ክፍሎች ምሥጢር በአሳብ ወይም በአቀራረብ ይገናኛል። ይህም በሦስት ዓይነት ይታያል። 1. የሁለተኛው ክፍል አሳብ የአንደኛውን ይደግፋል፤ ሁለተኛው ለመጀመሪያው አስረጅ ነው ማለት ነው፤ መዝ. 15፥1፤ 24፥1-3። 2. የሁለተኛው አሳብ የአንደኛው ተቃራኒ ነው፤ አፍራሽ ቅኔ እንደ ማለት ነው፤ መዝ. 37፥9፤ ምሳ. 10፥1። 3. ከሁለቱም ክፍሎች ያሉ ባለቤቶችና ተሳቢዎች፥ ግሦችና ሌሎችም ይገናኛሉ፤ እያንዳንዱ ምሥጢሩን ያብራራል፤ መዝ. 19፥8። በብ.ኪ. ታሪክ መጻሕፍት ውስጥ ልዩ ልዩ ግጥም ይገኛል (ዘጸ. 15፥1-18፤ መሳ. 15፥16፤ 2ሳሙ. 18፥33፤ 2ዜ.መ. 35፥25-27)፤ በሉቃስ ወንጌልም የግጥም ዓይነት ይታያል፤ ሉቃ. 1፥46-56:68-79፤ 2፥14:29-32። «አሌፋት» ይመ.

**ግጽው**፤ 56 ወይም 57 ቀናና (አንቀጽ) ያለበት የሲኖዶስ መጽሐፍ ክፍል። «ሲኖዶስ» ይመ.

**ጎላን**፤ ከገሊላ አገር በስተምሥራቅ በባሳን አገር ለምናሴ ነገድ የተለየ መማፀኛ ተራራማ ከተማ፤ ዘዳ. 4፥43፤ ኢያሱ 20፥8። ካ. 3ለ።

**ጎልያድ**፤ የእስራኤልን ጭፍራዎች የተገዳደራቸው፥ ቁመተ ረጅም የፍልስጥኤማውያን ጀግና፤ 1ሳሙ. 17፥4-11። ዳዊት በወንጭፍና በድንጋይ አሸነፈው፤ 1ሳሙ. 17፥12-53። በ2ሳሙ. 21፥19 የተጠቀሰው ጎልያድ የፊተኛው ጎልያድ ልጅ ይሆናል የሚል ግምት አለ። «ኤሌልም» ይመ.

**ጎልጎታ**፤ ቀራንዮ፥ ክርስቶስ የተሰቀለበት ቦታ። በአራማይክ ጎልጎታ፥ በግሪክ ቀራንዮ ማለት የራስ ቅል ማለት ነው። ቦታው ከኢየሩሳሌም ቅጥር ውጭ በመንገድ አጠገብ ነበረ፥ ዛሬ ግን ቦታው የት እንደሆነ ሰዎች ይከራከሩበታል። አብዛኞቹ ግን ቆስጠንጢኖስ ያሠራው ቤተ መቅደስ ያለበት እንደሆነ ያምናሉ፤ ማቴ. 27፥33፤ ማር. 15፥22፤ ሉቃ. 23፥33፤ ዮሐ. 19፥17-20። ካ. 8ለ። «ኢየሩሳሌም» ይመ.

**ጐመድ**፤ ራሳም መምቻ ዱላ። ክብደት እንዲያገኝ የብረት ጅንፎ ወይም አጥንት ይጨመርበታል፤ ሕዝ. 39፥9፤ ማቴ. 26፥55። «የጦር መሣሪያ» ይመ.

**ጎሜር**፤ ነቢዩ ሆሴዕ ያገባት የዲብላይም ልጅ፥ የኢይዝራኤልና የሎሩሃማ የሎዓሚም እናት። ውሽሞቿን ተከትላ በባርነት ተሸጠች። ግን ሆሴዕ መለሳት፤ ሆሴዕ 1፥3-9፤ 3፥1-3። «የሆሴዕ ትንቢት» ይመ.

**ጎሞር**፤ መስፈሪያ፤ ዘጸ. 16፥16-36። «መስፈሪያ» ይመ.

**ጎረቤት**፤ በቅርብ የሚኖር ሰው ወይም ድንበርተኛ አገር። ጎረቤቶች በሕይወት ጉዳይ ሁሉ መሳተፍና መተባበር ይገባቸዋል፤ ዘጸ. 3፥22፤ 12፥4፤ ሩት 4፥17፤ 2ነገ. 4፥3፤ ሉቃ. 15፥6:9። ጎረቤቶች ሲለያዩ ኑሮ ይከፋል፤ መዝ. 31፥11፤ 44፥13፤ 79፥4:12።

**ጎተራ (ጐተራ)**፦ የእህል መከተቻ፤ ኢዩ. 1፥17፤ ሚል. 3፥10፤ ማቴ. 6፥26፤ ሉቃ. 12፥18። በምሳሌነት በፍርድ ቀን የእግዚአብሔር ሕዝብ የሚሰበሰብበት፤ ማቴ. 3፥12።

**ጎቶልያ**፦ የንጉሥ አክዓብ ሴት ልጅ። የይሁዳን ንጉሥ ኢዮራምን አግብታ ነበር። እርሱም ከሞተ በኋላ ልጁ አካዝያስ አንድ ዓመት ነገሠ። አካዝያስ በኢዩ እጅ ከተገደለ በኋላ ግን እናቱ ጎቶልያ በይሁዳ ገዥ ሆና እስከ ስድስት ዓመት ነገሠች (ከ841-835 ከክ. በ.)። እርሷ ክፉ ሴት ነበረች። ማንም በሥልጣኗ እንዳይወዳደራት የመንግሥትን ዘር ሁሉ አጠፋች። ከሞት የተረፈ የአካዝያስ ልጅ ኢዮአስ ብቻ ነው። በኋላ ኢዮአስ ዮዳሄ በተባለው ሊቀ ካህናት ረዳትነት ነገሠ፤ ጎቶልያም ተገደለች። ታሪኳ ቀጥሎ በተዘረዘሩት ክፍሎች ተጽፎ ይገኛል፤ 2ነገ. 8፥18:25-28፤ 11፥1-20፤ 2ዜ.መ. 22፥1-23፥21፤ 24፥7።

**ጎቶንያል**፦ ከእስራኤላውያን መሳፍንት የመጀመሪያው። የካሌብ የታናሽ ወንድሙ ልጅ ነበረ፤ ኢያሱ 15፥17፤ መሳ. 3፥9። ዳቤርን ከያዘ በኋላ ካሌብ ልጁን ዓክሳን አጋባው፤ ኢያሱ 15፥15-19፤ መሳ. 1፥11-15። ኢያሱ ወልደ ነዌ ከሞተ በኋላ እስራኤላውያን ጣዖታትን ወደ ማምለክ አዘነበሉ፤ ስለዚህ በመስጴጦምያ ንጉሥ እጅ ወደቁ። እግዚአብሔርም ጎቶንያልን አስነሣቸው፤ ጎቶንያል እስራኤልን እየመራ ጠላትን ድል ነሣ። በእርሱም ዘመን እስራኤላውያን አርባ ዓመት በሰላም ኖሩ፤ መሳ. 3፥7-11።

**ጎዶልያስ**፦ ትርጉሙ «እግዚአብሔር ታላቅ ነው» ማለት ነው። ኢየሩሳሌም ከወደቀች በኋላ የባቢሎን ንጉሥ፥ ናቡከደነፆር በይሁዳ አገር በቀረው ሕዝብ ላይ አለቃ ያደረገው፤ 2ነገ. 25፥22። ነቢዩ ኤርምያስ በምጽጳ ከእርሱ ጋር ነበረ፤ ኤር. 40፥6። እስማኤል የተባለው የናታንያ ልጅ ጎዶልያስን ገደለው፤ 2ነገ. 25፥25፤ ኤር. 41፥1-3።

በዚህም ስም ሌሎች አራት ሰዎች ተጠርተውበታል፤ 1ዜ.መ. 25፥3:9፤ ዕዝ. 10፥18፤ ኤር. 38፥1-6፤ ሶፎ. 1፥1።

**ጎግ**፦ የሞሳሕና የቶቤል መስፍን፤ ሕዝ. 38፥2-3። «ማጎግ» ይመ.

**ጎፈር**፦ ጥድን የሚመስል ዛፍ፤ ዘፍ. 6፥14።

**ጐለጐለ**፦ በዘር ጊዜ ከእርሻ ላይ አረሙንና ሰርዶውን አነሣ፥ ዐፈሩንም ደለደለ፤ ኢዮብ 39፥10።

**ጐመራ**፦ ለመብሰል ደረሰ፥ በጣም አሸት ሆነ፤ መ.መ. 2፥13።

**ጐራዴ**፦ አንድ አፍ የሆነ ጐበጥ ያለ፥ ከብረት የተሠራ የሰይፍ ዓይነት፤ ሕዝ. 5፥1። «የጦር መሣሪያ» ይመ.

**ጐርፍ**፦ የፈተና ምሳሌ፤ ማቴ. 7፥25:27።

**ጐሽ**፦ ሰፊና ረጅም ቀንድ ያለው የዱር እንስሳ፥ የበረሀ በሬ፤ ኢዮብ 39፥9-12።

**ጐባጣ**፦ ቀጥ ብሎ ለመቆም የማይችል፤ ዘሌ. 21፥20፤ ሉቃ. 13፥ 11-13። «በሽታ» ይመ.

**ጓል**፦ የተድቦለቦለ ዐፈር፤ ኢዮብ 38፥37:38። ገበሬ በሚያርስበት ጊዜ ጓሉን ይከሰክሳል፤ ኢሳ. 28፥24።

**ጓዳ**፦ በውጭ ወይም በውስጥ የሚሠራ የቤት ተጨማሪ ክፍል። የሰሎሞን ቤተ መቅደስ ባለ ብዙ ጓዳዎች ነበረ፤ 1ነገ. 6፥5:8። ጓዳ የልብም ዕቃ፥ የምርጥ ዕቃ ማስቀመጫ ነው፤ ዕዝ. 8፥29። ሕዝቅኤል በራእይ ያየው የቤተ መቅደስ ንድፍ ብዙ ጓዳዎች እንደሚኖሩት ተገልጧል፤ ሕዝ. 41፥5-11።

**ጓጉንቸር**፦ እየዘለለ የሚሄድ፥ በውሃና በመሬት የሚኖር እንቁራሪት። በግብጽ ላይ ከወረዱት መቅሠፍቶች ሁለተኛው ጓጉንቸር ነበር፤ ዘጸ. 8፥2። በምሳሌነት ርኩስ መንፈስን ያመለክታል፤ ራእ. 16፥13።



**ጕልላት**፦ ከግንብ ወይም ከማናቸውም የቤት ጣራ ላይ የሚደረግ የቤት ዘውድ፤ በሸክላና በእንጨት በቆርቆሮም ይሠራል። አብዛኛውን ጊዜ አሠራሩ ክብ ነው፤ 1ነገ. 7፥41:42፤ ኢሳ. 54፥12። በድንኳንም ላይ ይደረጋል፤ ዘጸ. 36፥38። የትዕቢተኞችና የክፉዎች የበላይ ባለ ሥልጣናት ምሳሌ ሆኖ ተጠቅሷል፤ አሞጽ 9፥1።

**ጕልበት**፦ የጭንና የባት መጋጠሚያ። በጕልበት መንበርከክ የማክበር (2ነገ. 1፥13)፥ የመገዛት ምልክት ነው፤ ኢሳ. 45፥23፤ ፊል. 2፥10። 1. ጕልበት ማለት ዘርን ያመለክታል፤ ዘፍ. 35፥11። 2. የተፈጥሮንም ኃይል ሊያመለክት ይችላል፤ ዘዳ. 34፥7።

**ጕረኖ**፦ በድንጋይና በዐፈር የሚሠራ የበግ መመሰጊያ፤ ሕዝ. 34፥14። የሀብት ምሳሌ ነው፤ ዘፍ. 49፥14።

**ጕራጅ**፦ ጥቁር። ለፈረስ የመልክ ዓይነት መግለጫ ሆኖ ተጠቅሷል፤ ራእ. 6፥5።

**ጕርጅ**፦ ከአንድ ክፍል ውስጥ ለዕቃ ማስቀመጫ የሚሠራ ጓዳ፤ ዘፍ. 6፥14። እንደዚሁም በሆድ ውስጥ ምግብ የሚቀይበት የአካል ክፍል የሆድ ጕርጅ ይባላል፤ ምሳ. 18፥8፤ 20፥27።

**ጕበኛ**፦ ሰላይ፣ ተመልካች። የበር ጠባቂ ዘበኛም ጕበኛ ሊባል ይችላል፤ 2ሳሙ. 13፥34፤ ኢሳ. 21፥11፤ ሕዝ. 33፥2-9።

**ጕብኝት**፦ ማየት፣ መመልከት። የእግዚአብሔር ፍርድና በረከት ጕብኝት ተብሏል፤ ኤር. 10፥15፤ ሉቃ. 1፥68፤ 19፥44፤ 1ጴጥ. 2፥12።

**ጕብጕብ**፦ ከብርና ከወርቅ ከሌላም በተሠራ ዕቃ ላይ የሚቀረጽ ክብ የሆነ ጌጥ (ዘጸ. 25፥31፤ 1ነገ. 6፥18፤ መ.መ. 1፥11)፣ በጋሻ ጀርባ ላይ የሚደረግ ጕብር ጌጥ፤ ኢዮብ 15፥26።

**ጕድጓድ**፦ 1. የውሃ ማጠራቀሚያ። ዝናብ በማይገኝባቸው ወራት ውሃን ለማከማቸት በዐለታማ መሬት ውስጥ ጕድጓድ ይቈፈር ነበር። ውስጡን ይለቀልቁታል። ጕድጓዱ ሰፊና ጥልቅ ሲሆን፣ ውሃው እንዳይበላሽ አፉን ጠበብ አድርገው ይሠሩታል። የዝናብ ወይም የወንዝ ውሃ ከሞሉት በኋላ በትልቅ ድንጋይ ወይም በሌላ ነገር ይገጥሙታል። ዮሴፍና ኤርምያስ በባዶ ጕድጓድ ተጣሉ፤ ዘፍ. 37፥22፤ ኤር. 38፥6። በኢየሩሳሌም ብዙ ቤቶች የውሃ ማጠራቀሚያ ጕድጓዶች ነበሩአቸው፤ 2ነገ. 18፥31። ዖዝያን በቈላማው ቦታ ብዙ የውሃ ማጠራቀሚያ ጕድጓዶችን አስቈፍሮ ነበር፤ 2ዜ.መ. 26፥10።

2. የምንጭ ውሃ ጕድጓድ። ወንዝ በሌለበት አካባቢ ውሃ እስኪፈልቅ ድረስ ይቈፍራሉ። ዙሪያውን በድንጋይ ይከቡታል። በትልቅ ድንጋይም ይገጥሙታል፤ ዘፍ. 29፥2-10። ከላይ ማውጫ ይሠራለታል ወይም ሰው ወርዶ እንዲቀዳ እርከን ያበጁለታል። የአብርሃም ሎሌ ርብቃን ከምንጭ ውሃ ጕድጓድ ስትቀዳ አገኛት፤ ዘፍ. 24፥11:18። ይስሐቅ በጌራራ ብዙ የውሃ ጕድጓዶችን አስቈፈረ፤ ዘፍ. 26፥18-25። ክርስቶስ በውሃ ጕድጓድ አጠገብ



ሴቶች ከጕድጓድ ውሃ ሲቀዱ

አንዲት ሳምራዊት ሴት አነጋገረ፤ ዮሐ. 4፥6:7። ኤርምያስ የአምልኮትን ሁኔታ በምንጭ ውሃ ጕድጓድ መስሎ ተናገረ፤ ኤር. 2፥13።

**ጠላቂ**፦ ምግቡን ከአበትና ርጥበት ካለው ነገር፣ አፉን ጠለቅ አድርጎ የሚበላ አሞራ፤ ዘሌ. 11፥16። «ወርቆ» ይመ.

**ጠል**፦ በሌሊት ከሌሊቱ፣ ከቀኑ የፀሐይ ሙቀት የተነሣ ሌሊት ላይ የሚታይ ርጥበት። ጠል ከደመና ይገኛል፤ ምሳ. 3፥20። በበጋ ጊዜ በእስራኤል አገር ዝናብ አይዘንምምና ጠል ለግብርና አስፈላጊ ነው፤ ዘፍ. 27፥28፤ መሳ. 6፥37-40። ጠል ባይገኝ አገር ይጐዳል፤ 2ሳሙ. 1፥21፤ 1ነገ. 17፥1። በምሳሌነት በረከትን (ዘፍ. 27፥28)፣ መታደስን (ዘዳ. 32፥2፤ ኢዮብ 29፥19፤ መዝ. 133፥3፤ ኢሳ. 18፥4) ሊያመለክት ይችላል።

**ጠልሰም**፦ ሴቶች ለጌጥ በአንገታቸው ላይ የሚያደርጉት የብር ወይም የወርቅ አሸንክታብ፤ መ.መ. 1፥11።

**ጠማማ**፦ ቀጥተኛ ያልሆነ። አሳብ ጠማሞች እግዚአብሔርን ይንቃሉ፤ ምሳ. 14፥2። እግዚአብሔር ለጠማማ ሰው ጠማማ ይሆንበታል። በክፋቱ ይፈርድበታል ማለት ነው፤ መዝ. 18፥26። እግዚአብሔር ጠማማ ያደረገውን ወይም የፈረደበትን መለወጥ አይቻልም፤ መክ. 7፥13:14።

**ጠረቀ**፦ በእግር ብረት ወይም በእግር ግንድ አጣብቆ አሰረ፤ ሐ.ሥ. 16፥24።

**ጠርሴስ**፦ የኪልቅያ ዋና ከተማ። ጳውሎስ በጠርሴስ ተወለደ። በጳውሎስ ዘመን አምስት መቶ ሺህ ያህል ሕዝብ ይኖርበት ነበር፤ ሐ.ሥ. 9፥11፤ 11፥25፤ 21፥39፤ 22፥3። ካ. 6በ።

**ጠበቃ**፦ ሰውን ለመክሰስ፣ ወይም የሰውን መብት ለማስጠበቅ በፍርድ ቤት በሕግ መሠረት የሚከራከር፤ ሐ.ሥ. 24፥1-3። ክርስቶስ የምእመናን ጠበቃ ተብሏል፤ ይህም ስለ ኃጢአታቸው ተላልፎ መሞቱን ያስረዳል፤ 1ዮሐ. 2፥1:2። በክርስቶስ ስላመኑ፣ በፍርድ አደባባይ ለሚቆሙ ሁሉ መንፈስ ቅዱስ ጠበቃቸው ነው፤ ማቴ. 10፥16-20።

**ጠባቂ**፦ የጦር ሰፈርን፣ አገርን፣ ከተማን፣ ሰብልን፣ ሌላንም የሚጠብቅ ዘበኛ፤ 1ሳሙ. 14፥16፤ 2ሳሙ. 18፥24፤ ማቴ. 27፥65፤ 28፥4:11። ጠባቂዎች ልዩ ግንብ ወይም መጠበቂያ ይሠራላቸው ነበር፤ ኢሳ. 21፥8፤ ዕን. 2፥1። ነቢያት የእስራኤል ጠባቂዎች ተባሉ፤ ኤር. 6፥17፤ ሕዝ. 3፥17-21። እግዚአብሔር ካልጠበቀ የጠባቂ ትጋት ከንቱ ነው፤ መዝ. 127፥1። ገጽ 252 ይመ.

**ጠባይ (ጠባይዕ)**፦ ዐመል፣ ግብር፣ ሁኔታ፤ ሮም 1፥29። ጠባይ በነገረ መለኮት ትምህርት እንደ ባሕርይ ይተረጐማል።

**ጠብ**፦ በሰዎች መካከል ሊነሣ የሚችል ግጭት፤ 2ነገ. 5፥7። ክርስቲያን ከጠበኛነት መራቅ አለበት፤ ምሳ. 6፥19፤ ሮም 13፥13፤ 2ጢሞ. 2፥23። ሥዕሉን በሚቀጥለው ገጽ ይመ.



ጠባቂ፥ ዘብ፥ ዘበኛ



የሮማውያን ሴቶች ጸጉር አሠራር

**ጠቦት**፤ የበግ ግልገል፤ ኢሳ. 40፥11። በፋሲካ ሥርዓት የሚሠዋ እንስሳ፤ ዘጸ. 12፥3-21፤ ኢሳ. 53፥7። የአጥፊ አውሬ ተቃራኒ፤ ኢሳ. 65፥25። ቃሉ የፍየልን ግልገል ሊያመለክት ይችላል፤ ዘፍ. 27፥9፡16።

**ጠንቋይ**፤ መናፍስትን በመጥራት፥ በድግምት፥ በአስማት፥ በመተት በሌላም የሰውን ሁኔታ ወይም አንድን ነገር ለመለወጥ፥ የሚመጣውን ለመግለጥ የሚሠራ ሰው፤ ዘዳ. 18፥11፤ 1ሳሙ. 28፥3፤ ሐ.ሥ. 8፥9-24፤ 13፥6-12። «ጥንቆላ» ይመ.

**ጠያር**፤ ሰጋር፥ ሯጭ ማለት ነው። በተለይም የግመል ሰጋር ጠያር ይባላል፤ ኢሳ. 66፥20።

**ጠጅ ሣር**፤ ጥሩ መዐዛ ያለው ሣር። ለተቀደሰ የቅብዓት ዘይት እስራኤላውያን ይጠቀሙበት ነበር፤ ዘጸ. 30፥23።

**ጠገራ**፤ ለክብደት መለኪያ የሚያገለግል፥ ከእርሳስና ከናስ ከሌላም ማዕድን የሚሠራ፤ ዘካ. 5፥8። «ክብደት» ይመ.

**ጠጕር**፤ ጥንት በእስራኤላውያን ዘንድ ጠጕር የውበትና የክብር ምልክት ሆኖ ይቈጠር ነበር። ቡሀነት (በራነት) ደግሞ ይነቀፍ ነበር፤ 2ነገ. 2፥23፤ ኢሳ. 3፥24። ወንዶችም ሆኑ ሴቶች ጠጕራቸውን አስረዘሙ፤ 2ሳሙ. 14፥26። ጣዖትን እንደሚያመልኩ ሰዎች የጠጕራቸውን ዙሪያ መከርከም አልተፈቀደላቸውም፤ ዘሌ. 19፥27። ናዝራዊ ስእለቱን እስኪፈጽም ድረስ ጠጕሩን ፈጽሞ አይቈረጥም ነበር። በአዲስ ኪዳን ዘመን ጠጕር ለሴቶች ክብር ሲሆን ወንዶች ቢያስረዝሙት ግን ነውር ነው፤ 1ቆሮ. 11፥14።

**ጠፈር**፤ በመሬት ዙሪያ ያለው አየርና ሰማይ። ጠፈር በባሕሮችና በደመናዎች መካከል ይለያል፤ ዘፍ. 1፥6፡7።

**ጡብ**፤ ከሸክላ፥ ከጭቃ፥ አንዳንድ ጊዜም ከገለባ ጋር በተቀላቀለ ጭቃ የሚሠራ፥ በፀሐይ ወይም በእቶን እየተቃጠለ በድንጋይ ፈንታ ለሕንጻ መሥሪያ የሚያገለግል፤ ዘፍ. 11፥3፤ ዘጸ. 1፥14፤ 5፥7።

**ጡት መጣል**፤ ጡት መጥባትን መተው። ሕጻን ጡት መጥባት ሲተው ዕብራውያን ግብዣ ያደርጋሉ (ዘፍ. 21፥8)፥ መሥዋዕትም ያቀርባሉ፤ 1ሳሙ. 1፥24።



1450 ዓመታት ገደማ ከክ.ል. ሰዎች በጡብ ሕንፃ ሲሠሩ ከተዘጋጀ ሥዕል የተገለበጠ

**ጢ.ም፤** ግንባል ላይ የሚበቅል ጠጉር፥ በሴማውያን ነገድ የክብር ምልክት፥ ሲላጩትና ሲነጩት ግን የሐዘን ምልክት ነበረ፤ ዕዝ. 9፥3። «ጠጉር»፥ «ላጨ» ይመ.

**ጢ.ሞቴዎስ፤** ጢ.ሞቴዎስ ሐዋርያው ጳውሎስ በልስጥራን ያገኘው ወጣት ነው። አባቱ የግሪክ ሰው ሲሆን፥ እናቱ አይሁዳዊት ነበረች፤ ሐ.ሥ. 16፥1-3። ሴት አያቱና እናቱ ክርስቲያኖች ነበሩ፤ እርሱም ቅዱሳት መጻሕፍትን ተምሮ ነበር፤ 2ጢ.ሞ. 1፥5፤ 3፥14:15። የጳውሎስ የመንፈስ ቅዱስ ልጅ ነበረ። ሐዋርያው በሄደበት ሁሉ አብሮ ይሄድ ነበር፤ በኋላም ወደ ቆሮንቶስና ወደ ተሰሎንቄ መልእክተኛ ሆነ፤ በኤፌሶንም የሐዋርያው እንደራሴ ሆኖ ቀየ፤ 1ቆሮ. 4፥17፤ 1ተሰ. 3፥1-8፤ 1ጢ.ሞ. 1፥3። በስድስት የጳውሎስ መልእክቶች ላይ የጢ.ሞቴዎስ ስም እንደ አባሪ ደራሲ ተጨምሮ ተጺፈ። ሐዋርያው ጳውሎስ ሁለት መልእክቶችን ለጢ.ሞቴዎስ ጽፎለታል። 1 ጊዜ መታሰሩም ታውቋል፤ ዕብ. 13፥23።

ጳውሎስ መንፈሳዊ ልጁና ጓደኛው ስለሆነው ስለ ጢ.ሞቴዎስ ከፍ ያለ ምስጋና ቢያቀርብም (1ቆሮ. 16፥10፤ ፊል. 2፥19-22፤ 2ጢ.ሞ. 3፥10-11)፥ በእምነቱ እንዲጸና ስለ ወንጌል ሳያፍር መከራን እንዲቀበል፥ ከክፉ የጕልማሳነት ምኞትም እንዲሸሽ አስጠንቅቀው፤ 2ጢ.ሞ. 1፥7-8፤ 2፥22።

## የጢ.ሞቴዎስ መልእክት - 1ኛው፤

ጳውሎስ ይህን መልእክት ከመጻፉ ቢያንስ 8 ዓመታት በፊት በኤፌሶን ቤ.ክ.ን መሥርቶ ነበር። ከሮም እስር ቤት ተፈትቶ ሲወጣም፥ ኤፌሶንን እንደገና የጐበኘና ጢ.ሞቴዎስን በዚያች ከተማ እንዲቆይ አድርጎ የሄደ ይመስላል። ዘመኑ 63 ዓ.ም. ገደማ ይሆናል። በመቄዶንያ ወይም በሌላ አገር በመቆየቱ ይህን መልእክት ለእንደራሴው ጻፈ፤ 1፥3-4፤ 3፥14-15። በዚህም ጊዜ በቀርጤስ ለተወው ለቲቶ ተመሳሳይ መልእክት ጻፈ።

አከፋፈል ፦

1. የጳውሎስና የጢ.ሞቴዎስ ግንኙነትና አገልግሎት፤ ም.1።

2. የቤ.ክ. አስተዳደር፤ 2፥1-6፥2።

ሀ) የጉባኤ ጸሎት (2፥1-8) እና የሴቶች ድርሻ (2፥9-15)፥

ለ) የኤጲስ ቆጶስ (3፥1-7) እና የዲያቆን መስፈርት (3፥8-13)፥ የቤ.ክ. ጠባይና አምልኮ (3፥14-16)፥

ሐ) የሐሰት ትምህርት ጠባይ (4፥1-5) እና መፍትሔው (4፥6-16)፥

መ) ሰዎችን እንደየዕድሜአቸው (5፥1-2)፥ ባልቴቶችን (5፥3-16)፥ ሽማግሌዎችን (5፥17-25)፥ አገልጋዮችን (6፥1-2) ስለ መምከርና መምራት።

3. ስለ ልዩ ልዩ ሐሰተኛ ትምህርት (6፥3-5)፥ ስለ ፍቅረ ንዋይ (6፥6-10)፥ ስለ ጢ.ሞቴዎስ አካሄድ (6፥11-16)፥ ስለ ሀብታሞች (6፥17-19) እና ጢ.ሞቴዎስን ስለ ማበረታታት (6፥20-21)።

## የጢ.ሞቴዎስ መልእክት - 2ኛው፤

በ66 ዓ.ም. ገደማ ጳውሎስ እንደገና ተይዞ በሮም የሞት ፍርድ ተፈርዶበት በሰይፍ እንደሚሞት ይጠብቅ ነበር፤ 2ጢ.ሞ. 4፥6-8:16-18። ሐዋርያው ይህን መልእክት የጻፈው በሚከተሉት ዓላማዎች ይመስላል ፦ ሀ) ጢ.ሞቴዎስና የኤፌሶን ቤ.ክ. የተላለፈበትን ፍርድ እንዲያውቁ (4፥16:22)፥ ለ) ብቸኝነት ይሰማው ነበርና አብሮት የሚሠራ ደቀ መዝሙሩ፥ ማርቆስን ይዞ ወደ እርሱ እንዲመጣ (1፥15፤ 4፥9-14:21)፥ ሐ) የሮም ቄሣር ኔሮ ስደት ባስነሣ ጊዜ ጢ.ሞቴዎስ የወንጌልን ቃል እንዲጠብቅ (1፥13-14)፥ እንዲጸናበት (3፥14)፥ እንዲሰብከው (4፥2) እና በወንጌል ምክንያት ሳያፍር መከራን እንዲቀበል፤ 1፥8፤ 2፥3።

አከፋፈል ፦

1. የጳውሎስ ሁኔታና ስለ ጢ.ሞቴዎስ የነበረው ምኞት፤ ም. 1።

2. ጳውሎስ ለጢ.ሞቴዎስ የሰጠው አደራ፤ 2፥1-4፥5። በወታደር፥ በአስፖርተኛና በገበሬ ምሳሌነት መሠረት እንዲጸና (2፥1-13)፥ በከንቱ ክርክር እንዳይጠመድ (2፥14-26)፥ የመጨረሻውን ዘመን ክፋት በተማረው ትምህርትና በቅዱሳት መጻሕፍት ዕውቀት እንዲያሸንፍ (ም. 3)፥ ቃሉን ሁልጊዜ እንዲያስተምር፤ 4፥1-5።

3. የጳውሎስ ሕያው ተስፋ፤ 4፥6-8።

4. ልዩ ልዩ ጥያቄና ሰላምታ፤ 4፥9-22።

**ጢ.ሮስ፤** በታላቅ ባሕር ዳር የነበረች የፊንቄ ጥንታዊት ከተማ። ከተማይቱ በባሕር ዳር አጠገብ ባለው ደሴት ላይ በሲዶና ሰዎች ተቈረቈረች፤ ኢሳ. 23፥2:12። ከእስራኤል ልጆች ለአንዱ ለአሴር ብትመደብም፥ እርሱ አልወረሳትም፤ ኢያሱ 19፥29፤ 2ሳሙ. 24፥7። ንጉሥ ዳዊትና ልጁ ሰሎሞን ከጢ.ሮስ ነገሥታት ጋር ይተባበሩ ነበር፤ 2ሳሙ. 5፥11፤ 1ነገ. 9፥10-14፤ 2ዜ.መ. 2፥3-16። ጢ.ሮስ ታላቅ የንግድ ከተማ ነበረች፤ ሕዝ. 27። ነቢያት በጢ.ሮስ ላይ ትንቢት ተናገሩ፤ ኢሳ. 23፤ ኤር. 27፥3፤ ሕዝ. 26-28። የጢ.ሮስ ሕዝብ የኢየሱስን ትምህርት በከተማቸውም ተቀበሉት፤ ማር. 3፥8፤ 7፥24-31። ጳውሎስ ለሰባት ቀን በጢ.ሮስ ተቀመጠ፤ ሐ.ሥ. 21፥3-7። ዛሬ ብዙ ፍርስራሽ ይታይበታል፤ በበታውም ሹር የምትባል ትንሽ የሊባኖስ ከተማ ትገኛለች። ካ. 5ለ።

**ጢ.ሮአዳ፤** እስያ በተባለች በሮም ጠቅላይ ግዛት የነበረች ትልቅ ወደብ። ጳውሎስ ጢ.ሮአዳን ጐበኘ፤ ሐ.ሥ. 16፥8፤ 20፥5፤ 2ቆሮ. 2፥12። ዛሬ ከተማይቱ ፈርሳለች። ካ. 7ሰ።

**ጢ.ስ፤** የእሳት፥ የእግዚአብሔር መገኘትና የፍርድ ምልክት፤ ዘፍ. 19፥28፤ ዘጸ. 19፥18፤ ኢሳ. 6፥4፤ ሐ.ሥ. 2፥19፤ ራእ. 14፥11፤ 15፥8፤ 18፥9:18።

**ጢቅ አለ፤** ምራቁን ተፋ፥ ተጸየፈ ወይም ናቀ፤ ሚል. 1፥13።

**ጢባርዮስ፤** «ቄሣር» ይመ.

**ጢንጦ፤** የርስት ድርሻ። አንድ መሬት ሲከፈል እያንዳንዱ ክፍል ጢንጦ ይባላል፤ ሩት 4፥3።

**ጣርያ (ጣራ)፤** የቤት ባጥ፤ መ.መ. 1፥17። «ቤት» ይመ.



ሰገነት ያለው ቤት

**ጣት፤** ከእጅና ከእግር የሚወጣ አነስተኛ የአካል ክፍል፤ ዘጸ. 29፥12፤ 1ዜ.መ. 20፥6፤ ዮሐ. 8፥6፤ 20፥25:27። አንድ ድንቅ ወይም አዲስ ነገር በእግዚአብሔር ሲፈጸም የእግዚአብሔር ጣት እንዳደረገው ስለሚገለጽ፥ አሳቡ ከዚህ የበለጠ ማድረግ የሚችል መሆኑን ያሳያል፤ ዘጸ. 8፥19፤ 31፥18፤ መዝ. 8፥3፤ ዳን. 5፥5፤ ሉቃ. 11፥20።

**ጣውንት፤** ተቃዋሚ፥ ጉባን። ለአንድ ወንድ 2 ሚስቶች ቢኖሩት፥ አንዷ ለሁለተኛዋ ጣውንት ናት፥ እንደዚሁም ሴት ባሏን ፈትታ ሌላ ባል ብታገባ፥ አንዱ ለሌላው ጣውንት ነው። ስለዚህም ፍናናና ሐና ጣውንቶች ነበሩ፤ 1ሳሙ. 1፥6።

**ጣዖት፤** ከእንጨትና ከቀለጡ ማዕድናት የተሠራ የማምለኪያ ምስል። አሕዛብ ብዙ ዓይነት ጣዖት እየሠሩ ለአማልክታቸው ሰገዱ፤ ኢሳ. 2፥8። እስራኤላውያንም ጣዖትን ሠርተው አመለኩ፥ በዚህም እግዚአብሔር ተቈጣቸው፤ ዘጸ. 32፥1-10፤ መሳ. 2፥11-14፤ 2ነገ. 17፥7-18፤ 21፥11:12። ብዙ ጊዜ ጣዖትን ማምለክ ከወሲባዊ ግንኙነት ጋር የተያያዘ ነበር፤ 1ነገ. 15፥12፤ ሮም 1፥23-25። ጣዖት ራሱ ሕይወት የለውም፤ ኀይልም የለውም፤ መዝ. 114፥12-15፤ 1ቆሮ. 8፥4። ሆኖም ጣዖትን ማምለክ አእምሮን ያሳውራል (ኢሳ. 44፥18-20)፤ ያስነውራል (መዝ. 114፥16)፤ ከአጋንንት ጋር አንድ ያደርጋል፤ 1ቆሮ. 10፥20። ስለዚህ እስራኤል ጣዖትን እንዲያቃጥሉ ታዘዙ (ዘዳ. 7፥25)፤



የግብጽ አማልክት

ምእመናንም ከጣዖት መራቅ እንደሚገባቸው ታዝዘዋል፤ 1ቆሮ. 10፥14-22፤ 1ዮሐ. 5፥21። እግዚአብሔር ከሰጠን ውጭ ሌላ ነገር እንዲኖረን መመኘት ጣዖት ነው፤ ኤፌ. 5፥5። «ምስል» ይመ.



የመሰጴጦምያ ጣዖታት

**ጣፍናስ፤** በሰሜን ግብጽ የነበረ ትልቅ የተመሸገ ከተማ። የይሁዳ ሰዎች ኤርምያስን ወደ ጣፍናስ ወሰዱት። ኤርምያስ ናቡከደነፆር በጣፍናስ ዙፋኑን እንደሚያኖር ትንቢት ተናገረ፤ ኤር. 43፥7-10፤ ሕዝ. 30፥18።

**ጤና፤** በጠቅላላው የሰው ሁኔታ መልካም ሲሆን ጤና ይባላል። ብዙ ጊዜ ከበሽታ መራቅንና መዳንን ያመለክታል፤ ማቴ. 9፥12። ጤና ከሰው መንፈሳዊ ሁኔታ ጋር (መዝ. 38፥3)፥ በአካባቢም ካሉ ሰዎች ሁኔታ ጋር የተያያዘ ነው፤ ምሳ. 12፥18፤ 16፥24። ጤና ከኃጢአት (ማቴ. 9፥2-6)፥ ከጠላት የመዳን መግለጫ ነው፤ ኤር. 30፥17። እስራኤል

እንደ ሙሴ ሕግ ትእዛዝ ሲኖሩ ለምሳሌ ተላላፊ በሽታ ከያዛቸው ሰዎች በመለየት (ዘሌ. 13፥1-8)፥ ጽዳትንም በመጠበቅ (ዘሌ. 11፥39:40፤ 13፥47-58፤ 14፥33-53፤ 15፥1-33፤ ዘዳ. 23፥13) ከብዙ በሽታ ይድኑ ነበር። «በሽታ»፥ «ፈውስ» ይመ.

**ጤና አዳም**፤ ጥሩ ሽታ የሚሰጥ ተክል። በልዩ ልዩ መድኃኒት ውስጥ ይጨመር ነበር፤ ሉቃ. 11፥42።

**ጤዛ**፤ ከዝናም በኋላ፥ ወይም በጠል ወራት ጊዜ በሣርና በቅጠል ላይ ታቁር (ተቋጥሮ) የሚገኝ ውሃ። የማስተማር ዘዴ ምሳሌ ሆኖ ተጠቅሷል፤ ዘዳ. 32፥2።

**ጤግሮስ**፤ ከዔድን የወጣ ወንዝ፤ ዘፍ. 2፥10-14። በመስጴጦምያ ካሉ ሁለት ታላላቅ ወንዞች አንዱ ነው፤ ርዝመቱ 1840 ኪ.ሜ. ነው። ካ.1ለ።

**ጥላ**፤ በብርሃን ጊዜ የሚታይ አምሳል ግርዶሽ። በምሳሌነት ከሚጎዳና ከሚያስፈራ ነገር መከላከያና መጠለያ፥ መጠበቂያም (መዝ. 17፥8፤ ኢሳ. 30፥3)፥ ቶሎ ለሚያልፍና ለሚለወጥ ነገር መግለጫ (1ዜ.መ. 29፥15፤ ያዕ. 1፥17)፥ ወደ ፊት ለሚመጣ ነገር ተቀዳሚ ምሳሌና ስም በመሆን ይነገራል፤ ቆላ. 2፥17፤ ዕብ. 8፥5፤ 10፥1። ለሞትም መግለጫ ሆኖ ተጠቅሷል፤ መዝ. 23፥4፤ አሞጽ 5፥8።

**የጥላ ስፍረ ሰዓት**፤ የፀሐይ ብርሃን በደንብ ሲታይ ልዩ ልዩ መስመርና ምልክት ባለበት እንጨት ወይም ድንጋይ ጥላን በመጣል ሰዓት ይለካ ነበር፤ 2ነገ. 20፥11፤ ኢሳ. 38፥8።



የግብጽ የጥላ ሰዓት

**ጥል**፤ መጸየፍ፥ መጣላት፥ በሰው ላይ ክፉ ነገርን ማሰብ፥ የፍቅር ተቃራኒ፤ ምሳ. 10፥12፤ 15፥17። እንደ ነፍስ ገዳይነት ይቈጠራል፤ ዘዳ. 19፥11-13፤ 1ዮሐ. 3፥15። የሚጠላንን ሰው እንድንወድ ታዝዘናል፤ ዘጸ. 23፥5፤ ማቴ. 5፥43-45። ሰውን እንዳንጠላ እግዚአብሔር አዝዟል፤ ዘሌ. 19፥17። ጥል የሥጋ ሥራ ነውና በአማኞች ዘንድ መገኘት ከቶ አይገባውም፤ ገላ. 5፥20፤ ቲቶ 3፥3፤ 1ዮሐ. 2፥9፤ 4፥20። ኃጢአት ወደ ዓለም ስለገባ የጥል ጊዜ አለ፤ መክ. 3፥8። ለምሳሌ ምእመናን ሌላ ሃይማኖት የሚያስተምሩትን መቀበል ቀርቶ ሰላምምም ሊሉአቸው እንኳን አይገባቸውም፤ 2ዮሐ. 10። ደግሞም ሌላ ዓይነት ጥል አለ። ሰው ዘመዶቹን ካልጠላ የክርስቶስ ደቀ መዝሙር ሊሆን አይችልም፤ ሉቃ. 14፥26። ይህ ማለት ከዘመዶች ይልቅ ክርስቶስን መውደድ፥ ክርስቶስንም ማስቀደም ማለት ነው፤ ማቴ. 10፥37። ደግሞም ዘፍ. 29፥30:31፤ ሉቃ. 16፥13 ይመ.። እንደዚሁም «ያዕቆብን ወደድሁ ዔሳውን ጠላሁ» ሲል እግዚአብሔር ለዓለም የሰጠውን ተስፋ በበኩሩ በዔሳው ሳይሆን፥ በያዕቆብ በኩል ለማስተላለፍ እንደፈቀደ ያመለክታል፤ ሚል. 1፥2፤ ሉቃ. 1፥33፤ ሮም 9፥13።

**ጥልቅ**፤ ወደ ታች የራቀ፥ የጠለቀ፥ የተሰወረ ያልተገለጠ ማለት ነው። ቃሉ ለውሃዎች (ዘፍ. 1፥2፤ 49፥25)፥ ለብስጭት ሁኔታ (መዝ. 71፥20)፥ ለልብ ስሜት (መዝ. 130፥1)፥ ሙታን ለሚገኙበት (ሮም 10፥7)፥ የማይታዘዙ መናፍስት ለሚወሰኑበት (ሉቃ. 8፥31፤ ራእ. 9፥1:2፤ 20፥3)፥ ተመርምሮ ለማይገኝ ነገር ሁሉ ይነገራል፤ ሮም 11፥33።

**ጥልፍ**፤ በጨርቅ ላይ በተቀለመ ክር ተሰፍቶ የሚጨመር ጌጥ። ለቤተ መቅደስ መጋረጃዎችና ለካህናት ልብሶች ሥራ እግዚአብሔር ለጠላፊዎች የተለየ ችሎታና ጥበብ ሰጣቸው፤ ዘጸ. 26፥36፤ 27፥16፤ 28፥39፤ 35፥35፤ 38፥23፤ 39፥29። «ተግባረ እድ» ይመ.



አንዲት ሴት ጥልፍ ስትጠልፍ

**ጥመት**፤ ክፉት፥ ቅን አለመሆን፤ መዝ. 37፥7።

**ጥም**፤ ለውሃ፥ ለእግዚአብሔር በረከት ወይም እግዚአብሔርን ለማግኘት የሚነሣሣ ጥልቅ ፍላጎት፤ ዘጸ. 17፥3፤ መዝ. 42፥2፤ መሳ. 15፥18፤ ማቴ. 5፥6፤ ዮሐ. 4፥13-15፤ 6፥35፤ 7፥37፤ 19፥28፤ ራእ. 7፥16።

**ጥምቀት**፤ ጥምቀት የተለያየ ነው። በውሃ፥ በመንፈስ ቅዱስ፥ በሥቃይም መጠመቅ አለ፤ ሉቃ. 3፥16፤ 12፥50። ጥምቀት የሚከተሉትን አሳቦች ይይዛል። 1. መንጻት፤ ማር. 1፥1-4፤ ዮሐ. 3፥22-25፤ ሐ.ሥ. 22፥16፤ ቲቶ 3፥5። 2. መለወጥ፤ ማር. 1፥4-8፤ ሉቃ. 3፥7-14፤ 1ጴጥ. 3፥18-22። 3. መተባበር፤ 1ቆሮ. 1፥13፤ 10፥2፤ ገላ. 3፥27፤ ሮም 6፥3:4።

የዮሐንስ ጥምቀት ወደፊት የሚመጣውን ያመለክት ነበር፤ ማቴ. 3፥11:12።

የክርስቲያን ጥምቀት የተፈጸመውን የክርስቶስን ሥራ ያሳስባል፤ ሮም 6፥3:4። ሰው በአብ፥ በወልድና በመንፈስ ቅዱስ ስም ይጠመቃል፤ ማቴ. 28፥16-20።

በሐ.ሥ. «በኢየሱስ ክርስቶስ ስም ተጠመቁ» የሚለው፥ ሉቃስ የጴጥሮስን ትእዛዝ በሙሉ ሳይሆን በአጭሩ የጻፈው መሆኑን ያመለክታል። ሐዋርያት፥ አማኙ ከሥላሴ አካላት ጋር ግንኙነት እንዳለው ስለሚያውቁ የክርስቶስን ትእዛዝ እሚልተው የፈጸሙ መሆናቸውንም መረዳት አያስቸግርም፤ ሐ.ሥ. 2፥38። ሰው በኢየሱስ ክርስቶስ ስም ሲያምንም ኢየሱስ ክርስቶስ ፍጹም አምላክና ፍጹም ሰው ሆኖ የአብ አንድያ ልጅ፥ እንደዚሁም መንፈስ ቅዱስን ሰጭ መሆኑን ያምናል። ይህም በጴጥሮስ ስብከት ግልጥ ሆኗል፤ ሐ.ሥ. 2፥33:36። ይህን እውነት የማይቀበል መንፈስ ቅዱስን መሳደብ እንዳይሆንበት መጠንቀቅ አለበት፤ ማቴ. 12፥31:32። እንግዲህ «በክርስቶስ ስም መጠመቅ» ሥላሴን (ሦስቱን አካላት) እና ግብራቸውን ያጠቃልላል።

የመንፈስ ቅዱስ ጥምቀት በበዓለ ኀምሳ ዕለት በቤ.ክ. ተደረገ (ሐ.ሥ. 1፥5፤ 2፥1-4)፥ ከዚያ ጊዜ ጀምሮ ምእመናን ሁሉ በክርስቶስ ሥራ ከክርስቶስ አካል (ቤ.ክ.) ጋር አንድ በመሆን በቤ.ክ. ላይ የወረደውን መንፈስ ቅዱስ አብረው ይካፈላሉ፤ 1ቆሮ. 12፥13፤ ቲቶ 3፥3-5።

ክርስቶስ ሲጠመቅ የውሃና የመንፈስ ጥምቀት የተያያዘ ነበር፥ ይህም ለእኛ ምሳሌ ነው፤ ሉቃ. 3፥21:22፤ ሐ.ሥ. 2፥38፤ ቲቶ 3፥5። የመንፈስ ቅዱስ ጥምቀት የውሃን ጥምቀት ሊከተል ወይም ሊቀድም ይችላል፤ ሐ.ሥ. 8፥4-17፤ 10፥44-48።

ጥምቀት ከክርስቶስ ጋር አንድ ያደርገናልና በዚህ መሠረት ከኃጢአት እንደተለየን ቈጥረን በአዲስ ሕይወት እንኖራለን፤ ሮም 6፥1-11።

በቤ.ክ. ሊቃውንት የማይስማሙባቸው ነገሮች አሉ። ከእነዚህም ጥቂቶችን በአጭሩ እንገልጣለን።

1. አንዳንዶች ጥምቀት የሚለው ቃል በውሃ ውስጥ ማጥለቅን ያሳያል ሲሉ፥ ሌሎች ደግሞ «ማፍሰስ» የሚለው ቃል የጥምቀትን ምሥጢር ያመለክታል ይላሉ፤ ሐ.ሥ. 2፥33።

2. አንዳንዶች ማር. 16፥16 ና ሌላም ክፍልን ጠቅሰው ሰው ሳያምን ሊጠመቅ አይገባም ይላሉ። እንደዚሁም ሌሎች በብ.ኪ. ዘመን ሕፃናት ተገረዙ፤ ስለዚህ ልጆች እንደ እግዚአብሔር ሕዝብ ተቈጥረው እግዚአብሔር የቃል ኪዳን አባሎች አድርጓቸዋልና (ዘፍ. 17፥7፤ ሮም 4፥11፤ ገላ. 3፥29፤ ቆላ. 2፥11-12፤ 1ቆሮ. 7፥14) ሊጠመቁ ይገባቸዋል ይላሉ፤ ሐ.ሥ. 2፥39፤ 16፥15:33።

3. በዚያም ሆነ በዚህ ጥምቀት አስፈላጊ ነው፤ በረከቱ በክርስቶስ ከመንፈስ ቅዱስ ነውና። ተጠማቂው በረከትን የሚያገኘው ፦ (ሀ) በተለይ በሥርዓቱ፥ (ለ) በተለይ በእምነቱ፥ (ሐ) ጥምቀት በተለይ የቃል ኪዳን ተስፋ ስለታተመበት ነው በማለት ሊቃውንት በአሳብ ይለያያሉ።

ኢየሱስ «የምጠመቃት ጥምቀት አለችኝ» ሲል ሞቱን አመለከተ፤ ሉቃ. 12፥50፤ ማር. 10፥38:45፤ ዮሐ. 18፥11። ሞቱን በጥምቀት ይመስላል፥ ምክንያቱም ሰው በጥምቀት ከፊተኛው አሳዛኝ ኑሮ ስለሚለይና ወደ አዲስ ሕይወት ስለሚገባ ነው፤ ሮም 6፥3:4። ክርስቶስ ከሞቱና ከትንሣኤው በኋላ ሰዎችን በመንፈስ ቅዱስ እንደሚያጠምቃቸው ስለሚያውቅ ሥራውን ለመፈጸም ይመኝ ነበር፤ ዮሐ. 7፥39፤ ሉቃ. 12፥49-50። ክርስቶስ በእሳት ያጠምቃል ማለት ይፈርዳል፤ በሰዎች መካከል ያለውን ልዩነት ይገልጣል፤ ክፋትንም ያጠፋል፤ ሉቃ. 3፥16:17፤ 12፥49-53።

**ጥምድ**፤ «ቀንበር» ይመ.

**ጥሩር**፤ ከብረታ ብረት ወይም ከቆዳ የሚሠራ ከአንገት እስከ ጕልበት የሚለበስ የጦር መሣሪያ መከላከያ፤ 1ሳሙ. 17፥5፤ 1ነገ. 22፥34፤ ነሀ. 4፥16። የጽድቅ ምሳሌ ነው፤ ኤፌ. 6፥14:15። «የጦር መሣሪያ» ይመ.

**ጥሪ**፤ «መጥራት» ይመ.

**ጥራኮኒዶስ**፤ በግሪክ ቋንቋ ጥራኮኒዶስ ማለት ሸካራማ ማለት ነው። ከደማስቆ በስተደቡባዊ ምሥራቅ የሚገኝ ቦታ። ፊልጶስ በጥራኮኒዶስ ገዥ ነበረ፤ ሉቃ. 3፥1። አሁን በሶርያ ውስጥ ይገኛል። ካ. 5ሐ።

**ጥራጥሬ**፤ እንደ አተርና ባቄላ ያለ ልዩ ልዩ ዘር፤ ዳን. 1፥12:16።

**ጥርስ**፤ በአፍ ውስጥ ያለው የምግብ ማድቀቂያ። ጥርስ ማለት ግፍን (ምሳ. 30፥14)፥ ጥርስን ማጥራት ራብን (አሞጽ 4፥6)፥ ጥርስ ማፋጨትም ቍጣንና ፍርድን (ማቴ. 8፥12) ያመለክታል።

**ጥርስ ማፋጨት**፤ ቍጣን (ኢዮብ 16፥9)፥ ጥላቻን (መዝ. 37፥12)፥ መጕምጀትን (መዝ. 112፥10)፥ ጽኑ ሥቃይን ያሳያል፤ ማቴ. 8፥12፤ 13፥42፤ 25፥30።

**ጥርጥር**፤ የእምነት ጕድለት፤ ማቴ. 14፥31። አማኙ ያለ ጥርጥር በክርስቶስ ማመን (ማቴ. 28፥17፤ ዮሐ. 10፥24)፥ መመራት (ሐ.ሥ. 10፥20፤ 11፥12)፥ መጸለይ (ማቴ. 21፥21) አለበት። ማናቸውንም ነገር ተጠራጥሮ ቢያደርግ ኃጢአት ይሆንበታል፤ ሮም 14፥23። «ኑፋቄ» ይመ.

**ጥሻ (ጣሻ)**፤ ሥርና ቅጠል የበዛበት ቦታ። የሸፍታ ማደሪያና መዋያ ነው፤ 1ሳሙ. 23፥15:16።

**ጥቅልል**፤ ከደንገል በተሠራ ወረቀት ወይም በብራና ከተጻፈ በኋላ በሁለት በትሮች የሚጠቀለል መጽሐፍ። የቅጠል ዓይነት መጻሕፍት እስከ 100 ዓ.ም. ገደማ አልተሠሩም ነበርና መ.ቅ. መጽሐፍ ሲል የጥቅልልን ዓይነት ያመለክታል። የጥቅልል ርዝመት

እስከ ዐሥር ሜትር ሊደርስ ይችል ነበር። ጽሕፈቱም በዐምዶች ላይ ነበረ፤ ኢሳ. 34፥4፤ ኤር. 36፥2:20-23፤ ሕዝ. 3፥1-3፤ ሉቃ. 4፥17-19፤ 2ዮሐ. 12፤ ራእ. 5፥1:2፤ 2ጢሞ. 4፥13። «ጽሑፍና ጽሕፈት» ይመ.



የመጽሐፍ ጥቅልል

**ጥበብ፤** ማስተዋል፥ ዘዴ፥ ማንኛውንም ነገር ለማግኘት የመመርመር ችሎታ። የሥራ ችሎታ ያላቸው ጥበበኞች ይባላሉ፤ ዘጸ. 31፥2-5፤ ሕዝ. 27፥8:9።

በተለይም አስተዳዳሪዎች ሕዝብን እንዲመሩ ጥበብ ያስፈልጋቸዋል፤ ዘዳ. 34፥9፤ 2ሳሙ. 14፥20፤ 1ነገ. 3፥9:12፤ 4፥29። ፍጹም ጥበብ ያለው እግዚአብሔር ብቻ ነው፤ ኢሳ. 31፥2፤ ዳን. 2፥20-23። እርሱ ሁሉን እንደ ጥበቡ ያደርጋል፤ ምሳ. 3፥19፤ ሮም 11፥33-36። ከሁሉ በላይ ጥበብ የተገለጠው በክርስቶስ ነው፤ ምሳ. 8፤ 1ቆሮ. 1፥24:30:31፤ ቆላ. 2፥2:3። ሰው እግዚአብሔርን በመፍራት ጥበብን ያገኛል፤ በእግዚአብሔር መንገድ ይራመዳል፤ መዝ. 111፥10፤ ኢዮብ 28፥28፤ ያዕ. 1፥5። ሆኖም የተማሩ ሰዎች ጥበብ ከእግዚአብሔር ጥበብ ጋር ሲመዛዘን እንደ ምንም አይቈጠርም። ሰው ጥበበኛ ነኝ ቢልም በእግዚአብሔር ዘንድ እንደ ደንቆሮ ነው፤ ሮም 1፥22፤ 1ቆሮ. 1፥19-30፤ 3፥19:20፤ ያዕ. 3፥13-17። ጥበብ ከመንፈስ ቅዱስ ስጦታዎች አንዱ ነው፤ 1ቆሮ. 12፥8።

**ጥበብ፤** መጽሐፈ ጥበብ ትትሡ ሰሎሞን ጽፎታል የተባለው፥ የጥበብን ጥቅም የሚገልጽ መጽሐፍ ነው። የኦርቶዶክስና የካቶሊክ አብ.ክ. ከብ.ኪ. መጻሕፍት ጋር አብረው ይቀበሉታል።

**ጥብርያዶስ፤** በገሊላ ባሕር ዳር በምዕራብ በኩል በ20 ዓ.ም. ገደማ በሄሮድስ አንቲጳስ የተሠራ ከተማ። የመቃብር ቦታ ከሆነ በኋላ አይሁድ እንደ ርኩስ ስለቈጠሩት በጥብርያዶስ ለመኖር ፈቃደኞች አልነበሩም። ኢየሱስ ወደዚህ ከተማ የገባ መሆኑ አልተጻፈም። ዛሬ የገሊላ ዋና ከተማ ነው። ካ.5ለ።

**ጥብሳት፤** (ጠባሳ)፤ ትኩሳት ያለበት በሽታ፤ ዘዳ. 28፥22። በእሳት ምክንያት የሚሆን ጥብሳትም ሊሆን ይችላል። «በሽታ» ይመ.

**ጥና፤** የዕጣን ማጠኛ ዕቃ። ካህኑ የእሳት ፍም ጨምሮ ዕጣን ያጥንበታል፤ ዘሌ. 16፥12፤ ዘኍ. 16፥46። በሙሴ ዘመን ጥና ከናስ (ዘኍ. 16፥39)፥ በኋላም ከወርቅ ይሠራ ነበር፤ 1ነገ. 7፥50፤ ራእ. 8፥3-5። ናዳብና አብዩድ ያልተፈቀደውን እሳት በጥናዎቻቸው ስለጨመሩ ተቀሠፉ፤ ዘሌ. 10፥1:2። ቆሬና ወገኖቹ እንዲሁም ንጉሥ ዖዝያን ሳይገባቸው ጥና ይዘው ስላጠኑ ተቀሠፉ፤ ዘኍ. 16፥16-35፤ 2ዜ.መ. 26፥16-20።



**ጥንቈላ፤** እግዚአብሔር ባልፈቀደው መንገድ መንፈሳዊ ኃይልን መፈለግ። ከጥንት ጀምሮ ጥንቈላ የታወቀ ነው፤ ጠንቋዮች የነገሥታት አማካሪዎች ነበሩ፤ የእግዚአብሔርንም ሥራ ተገዳድረዋል፤ ዘጸ. 7፥8-22፤ ኢሳ. 19፥3፤ ዳን. 2፥2። በከነዓን ምዋርተኛ፥ ሞራ ገላጭ፥ አስማተኛ፥ መተተኛ፥ በድግምት የሚጠነቍል፥ መናፍስትን የሚጠራና ሙታን ሳቢ ጠንቋይ ይገኝ ነበር። ሥራቸው ይመሳሰላል። እነዚህም ርኩስ መንፈስንና የሙታንን መናፍስት በመጠየቅ ምሥጢራውያን አስማትን በመድገም፥ ልዩ ልዩ መሥዋዕትን በማቅረብ፥ የእንስሳትን ሆድ ዕቃና ሌሎች ነገሮችንም በመመልከት የሚመጣውን ነገር ይናገሩ፥ ጠላቶቻቸውን ይጐዱና ወዳጆቻቸውን ይጠብቁ ነበር፤ ዘዳ. 18፥9-14። በየአርእስቱ ይመ.

እስራኤላውያን በጠንቋዮች መንገድ እንዳይሄዱ ተከለከሉ። ጠንቋዮችንም እንዲያጠፉ ታዘዙ፤ ዘጸ. 22፥18፤ ዘሌ. 20፥27። እንደ ኢዮስያስ ያሉ እውነተኞች ነገሥታት አስወገዷቸው (2ነገ. 23፥24)፥ እንደ ምናሴ ያሉት ግን ራሳቸው ይጠነቍሉ ነበር፤ 2ነገ. 21፥6። ሳኦል በመጀመሪያ ጠንቋዮችን አጠፋ፤ በኋላ ግን መናፍስት ጠሪ በመጠየቅ እግዚአብሔርን አስቈጣ፤ 1ሳሙ. 28፥3-19።

በመ.ቅ. የተገለጡ አንዳንድ የጠንቋይ ሥራዎች፥ (ሀ) በትሮን ወደ እባብ መለወጥ፥ (ለ) ውኃን ወደ ደም መለወጥ፥ (ሐ) ሙታንን መጥራት ናቸው፤ ዘጸ. 7፥10-11:20-22፤ 1ሳሙ. 28፥14።

ሰው እግዚአብሔርን እንጂ ጠንቋይን መጠየቅ አይገባውም፤ 1ዜ.መ. 10፥13:14። እንደዚሁም የሰው ኃይል በጸሎት እንጂ በኃይለ፥ በአስማት፥

በድግምት በሌላም የሚገኝ መሆን የለበትም፤ ሉቃ. 4፥6:7። ምእመናን ከጥንቈላ መራቅ፥ የጥንቈላንም ዕቃ ማቃጠል ይገባቸዋል፤ ሐ.ሥ. 19፥19:20፤ ገላ. 5፥20፤ ራእ. 22፥15። ምንም እንኳ ብዙ ጠንቋዮች ኃይል ሳይኖራቸው ገንዘብ ለማግኘት ቢያታልሉም፥ አንዳንዶች በርኩስ መንፈስ ምክንያት ልዩ ኃይል ይኖራቸው ይሆናል፤ ተአምራትንም ያደርጋሉ። የእግዚአብሔር ሰው ግን በመንፈስ ቅዱስ ኃይል ሊቃወማቸው ይችላል፤ ሐ.ሥ. 8፥9-24፤ 13፥6-12፤ 16፥16-18።

**ጥንቸል፤** «እንስሳት» ይመ.

**ጥዝጣዜ፤** የቍስል ሕመም ስሜት፥ የመከራ ምሳሌ ነው፤ መዝ. 69፥26።

**ጥጃ፤** የላም ልጅ። በብዙ አገሮች ጥጃ የጕልበትና ዘርን የማግኘት ምሳሌ ስለሆነ፥ ሕዝቡ አማልክታቸውን በጥጃ ምስል ሠርተው ያመልኩ ነበር። አሮን እስራኤል በጥጃ አማካይነት እግዚአብሔርን እንዲያመልኩ አሰበ። ኢዮርብዓም የወርቅ ጥጃዎችን በቤቴልና በዳን አኖረ። አምልኮቱም ብዙ ዐይነት ዘማዊነትን አስከተለ፤ እግዚአብሔርንም አስቈጣ፤ ዘጸ. 32፥1-፯፤ 1ነገ. 12፥28-30።



የግብጽ ጣኦታት የጥጃ ምስል

**ጥጋብ፤** የሥጋ ወይም የነፍስ ርካታ፤ ዘፍ. 41፥34:53፤ ምሳ. 6፥30፤ ማር. 8፥4። እውነተኛ ርካታ ከእግዚአብሔር ይገኛል፤ መዝ. 17፥15፤ 81፥16፤ 105፥40፤ 107፥9፤ 132፥15፤ 145፥16።

**ጥጋት፤** ያልለሰለሰ፥ ያልታረሰ መሬት። የኃጢአተኛ ልብ ምሳሌ ነው፤ ኤር. 4፥3:4፤ ሆሴዕ 10፥12።

**ጥፋት፤** በመ.ቅ. ጥፋት ብዙ ጊዜ ለዘለዓለም ከእግዚአብሔር የመራቅንና ከጸጋውም የመውጣትን ሁኔታ ያመለክታል፤ ፊል. 1፥28፤ 1ጢሞ. 6፥9። ይሁዳና የዐመፅ ሰው የጥፋት ልጆች ተብለዋል፤ ዮሐ. 17፥12፤ 2ተሰ. 2፥3።

**የጥፋት ርኵሰት፤** «ርኵሰት» ይመ.

**የጥፋት ውሃ፤** በኖኅ ዘመን የዘነመ ዝናም። የሰው ክፋት ሲበዛ፥ የልቡ አሳብና ምኞት ሲከፋ እግዚአብሔር ሰውን ሊያጠፋ ወሰነ። ኖኅ ግን በእግዚአብሔር ፊት ሞገስን አገኘ፥ በእግዚአብሔርም ትእዛዝ መርከብን ሠራ፥ የጥፋት ውሃ በምድር ላይ ሲመጣ ኖኅ ቤተሰቡና ወደ መርከቡ ያስገባቸው እንስሳት ዳኑ፤ ሌሎች ግን ጠፉ። ምድር ሁሉ ከአንድ ዓመት በላይ በውሃ ተሸፈነ። አንዳንዶች ዓለም ሁሉ፥ ሌሎች ደግሞ ለኖኅ ይታይ የነበረው ምድር ሁሉ ተሸፈነ ብለው ይተረጕማሉ። ነገር ግን አብዛኞች በኖኅ ዘመን እንደሆነ እንዲሁ በክርስቶስ መምጣት ይሆናል ስለሚል፥ ዓለም ሁሉ ነው በሚለው አሳብ ይስማማሉ። ታሪኩ በዘፍ. 6፥5-8፥18 ተጽፏል። ከጥፋት ውሃ በኋላ እግዚአብሔር ዓለምን እንደገና በውሃ እንዳያጠፋ ቃል ኪዳን ሰጠ፤ ዘፍ. 8፥20-9፥17። የጥፋት ውሃ የዓለም መጨረሻ ፍርድ ምሳሌ ነው፤ ማቴ. 24፥37-39። ጴጥሮስም እንደገለጠው ውሃው የጥምቀት ምሳሌ ተብሏል፤ 1ጴጥ. 3፥20:21።

**የጦር መሣሪያ፤** ሰው ወደ ጦርነት ሲሄድ በቤቱ የሚገኘውን መሣሪያ ይዞ ይዘምት ነበር። ቋሚ ወታደር ግን ልዩ የጦር ልብስና መሣሪያ ነበረው። ንጉሥና ከፍተኛ የጦር መኰንን የጦር መሣሪያ የሚሸከምላቸው ጋሻ ጃግሬ ነበራቸው። የወታደር መሣሪያ በሁለት ይከፈላል።

1. መመከቻ። አላባሽ አግሬ ጋሻ፥ ጋሻ (1ነገ. 10፥16:17)፥ የራስ ቍር፥ ገምባሌ፥ ጥሩር፤ 1ሳሙ. 17፥5-7። የተራ ወታደር መመከቻ ከቆዳ የተሠራ ሲሆን፥ የነገሥታትና የጦር አለቆች መመከቻዎች ግን በናስ ወይም በብረታብረት ይሸፈኑ ነበር፤ 1ነገ. 14፥27።

2. ማጥቂያ፤ ሰላጢን (ኢዮብ 39፥23)፥ ሰይፍ (1ሳሙ. 17፥51)፥ ቀስትና ፍላጻ (ዘፍ. 27፥3)፥ ቀጭኔና ካራ (1ነገ. 18፥28)፥ ወንጭፍ (መሳ.20፥16)፥ ጕመድ (ሕዝ. 39፥9)፥ ጕራዴ (ሕዝ. 5፥1)፥ ጦር፥ ጭሬ፤ 1ሳሙ. 17፥6:7። ነገሥታት ደግሞ ሠረገሎችን ለጦርነት ያዘጋጁ ነበር (ዘጸ. 14፥25)፤ ፍላጻዎችንና ትልልቅ ድንጋዮችን



የቄሣር ወታደሮች የራስ ቍር

የሚወረውሩ መሣሪያዎችንም ይሠሩ ነበር፤ 2ዜ.መ. 26፥14:15። «ጦርነት»፣ «ጦር ሠራዊት» ይመ.

**ጦር ሠራዊት፤** ከመጀመሪያ ጀምሮ ሕዝቦች ስላልተስማሙ ወደ ጦር ሜዳ መውጣት የተለመደ ሆነ። ታላላቅ መንግሥታትም ብዙ የጦር ሠራዊት ያደራጁ ነበር፤ የጦር ሠራዊት መኰንኖች በመንግሥት ዘንድ ታላላቅ ሰዎች ነበሩ። በእስራኤል ኅብረተሰብ ከ20 ዓመት በላይ የነበሩ ወንዶች ሁሉ በጦርነት መሳተፍ ነበረባቸው (ዘኍ. 1፥3)፣ ወታደሮች በጭፍራ በሺህና በመቶ አለቆች መሪነት ይሰለፉ ነበር፤ ዘኍ. 31፥14። አንዳንዶች ወደ ጦር ሜዳ እንዳይሄዱ ይፈቀድላቸው ነበር፤ ዘዳ. 20፥1-9።



የሮም ወታደሮች

እስራኤላውያን ከነዓንን ከያዙ በኋላ ጠላት ሲነሣባቸው፣ አንድ መሪ ሰዎችን በሙሉ ለጦርነት ያሰልፋቸው ነበር፤ መሳ. 6፥33-35፤ 1ሳሙ. 11፥5-7። ሳኦል ከነገሠ በኋላ ግን ቋሚ የጦር ሠራዊት



የሮም መቶ አለቃ

አዘጋጀ፤ 1ሳሙ. 13፥2። ዳዊትም ከሊታውያንንና ፈሊታውያንን ለክብር ዘብ ቀጠረ፤ 2ሳሙ. 8፥18። እስከ ነገሥታት ዘመን ድረስ የእስራኤል ወታደሮች በተለይ እግረኞች ነበሩ (1ሳሙ. 4፥10)፣ ሰሎሞን ግን ብዙ ፈረሰኞችንና ሠረገሎችን ጨመረ፤ 1ነገ. 10፥26-29። ወታደሮች በዘመቱ ጊዜ በምርኮ ይተዳደሩ ነበር (1ሳሙ. 30፥24)፣ ቋሚ ጦር ሠራዊት ደግሞ ከንጉሡ ማዕድ ይቀለብ ነበር (1ነገ. 4፥27)፤ ወታደሮች ለጦርነት ሲወጡ በአንድ ሰፈር ያድራሉ። ሰፈሩም ሁልጊዜ ይጠበቃል፤ መሳ. 7፥19፤ 1ሳሙ. 17፥20፤ 25፥13፤ 26፥5።

የሮም ጦር ሠራዊት ዋና ክፍሎች ሌጊዎንና ጭፍራ ይባሉ ነበር። በአንድ ጭፍራ ዐሥር መቶ አለቆች ይገኙ ነበር፤ ማር. 5፥9፤ ሐ.ሥ. 10፥1፤ 27፥1። «ጦርነት»፣ «የጦር መሣሪያ» ይመ.

**ጦርነት፤** ውጊያ ለመግጠም መሰለፍ። የጥንት ሰዎች ወደ ጦርነት ሲሄዱ፣ በአምላካቸው ፈቃድ እንደሚዘምቱ ያምኑ ነበር፤ 2ነገ. 18፥32-35። በእስራኤል አገር ነገሥታት ወደ ጦርነት ከመውጣታቸው በፊት መሥዋዕትን ይሠዉ (1ሳሙ. 7፥8-10፤ 13፥8-9)፣ እግዚአብሔርንም ይጠይቁ ነበር። ጦርነታቸውንም የእግዚአብሔር ጦርነት ይሉት ነበር፤ 1ሳሙ. 18፥17፤ 1ነገ. 22፥5-28፤ 2ነገ. 3፥11። ወታደሮች በቀንደ መለከት ድምፅ ይጠሩ ነበር (መሳ. 3፥27፤ 1ሳሙ. 13፥3)፣ ካህናት መለከት ይነፉ (2ዜ.መ. 13፥12)፣ ታቦትም ተሸክመው ወደ ጦርነት ይሄዱ ነበር፤ ዘዳ. 20፥1-4፤ ኢያሱ 6፥1-21፤ 1ሳሙ. 4።

የጦርነት ስልትና ዘዴ ብዙ ዓይነት ነበረ። አንዳንድ ጊዜ ጦርነት በተመረጡ ጀግኖች ይጀመር ነበር፤ 1ሳሙ. 17፤ 2ሳሙ. 2፥14-16። ወታደሮች በድንገት ወደ ጠላቶቻቸው ሲደርሱ እንደሚያሸንፉ



ከአሦር የቅርጻ ቅርጽ ጥበብ የተገኘ

ብዙ ጊዜ ይታያል፣ ዘፍ. 14፥15፣ ኢያሱ 11፥1-9፣ መሳ. 7፥19-23። ኢያሱ፥ ሌሎችም በድብቅ ጦርና የተሸነፉ በመምሰል ዘዴ ተጠቀሙ፣ ኢያሱ 8፥3-23፣ መሳ. 20፥20-48። አንድ የጦር ሠራዊት በጦር ሜዳ ላይ ጠላት ሲበረታበት፥ ወደ ግንብ ወይም ወደ ተመሸገ ከተማ ይገባ ነበር፥ ጠላቱም ምሽጉን ከብቦ ሊይዘው ይሞክር ነበር፣ 2ሳሙ. 20፥15፣ 2ነገ. 6፥24:25፣ ሕዝ. 4፥2። ተሸናፊዎች እንደተገደሉ ወይም ባሪያዎች ሆነው እንዳገለገሉ ተገልጧል፣ ዘዳ. 20፥16-18፣ አሞጽ 1፥6:9:13። በጦርነት የተገኘው ምርኮ ለእግዚአብሔር እርም ካልሆነ በቀር ጦር ሠራዊቱ ይካፈለው ነበር፣ ዘኍ. 31፥27፣ ኢያሱ 22፥8፣ 1ሳሙ. 30፥24:25።

የክርስቶስ ተከታይ እንደ ወታደር ነው። በመንፈስ በኩል ከሰይጣንና ከኃጢአት ጋር ይዋጋል፣ 2ቆሮ. 10፥3-5፣ 1ጢሞ. 1፥18፣ 2ጢሞ. 2፥3:4፣ ያዕ. 4፥1፣ 1ጴጥ. 2፥11። ዕቃ ጦሩም መንፈሳዊ ነው፣ ሮም 13፥12፣ 2ቆሮ. 6፥7፣ ኤፌ. 6፥11-18፣ 1ተሰ. 5፥8።

ጦርነት ከሰው ኃጢአት የተነሣ ወደ ዓለም እንደገባ ግልጥ ነው። አዎ፣ «አትግደል» ተብሎ ታዝዟል፣ ሆኖም ዳኞች የሞት ፍርድ እንዲፈርዱ ተፈቀደላቸው፣ እስራኤልም ጠላቶቻቸውን እንዲያጠፉ ብዙ ጊዜ ታዘዙ፣ ዘሌ. 27፥29፣ ዘኍ. 21፥2:3፣ 1ሳሙ. 15፥3። በአ.ኪ. ግን የክርስቶስ ፈቃድ የሚፈጸመውና ቤ.ክ. የምትስፋፋው በመንፈሳዊ እንጂ በሥጋዊ ኃይል አይደለም፣ ማቴ. 26፥52፣ 2ቆሮ. 10፥3-5፣ ኤፌ. 6፥12። ሆኖም ጦርነት በዚህ ዓለም የማይቀር መሆኑን ኢየሱስ ተናገረ፣ ማቴ. 24፥6። በጦርነትም ምሳሌ አስተማረ፣ ሉቃ. 14፥31:32። እንግዲህ ክርስቲያን ወታደር ሊሆን ይችላልን? አንዳንዶቹ በተለይ ማቴ. 5፥43-45 እና 10፥23 እየጠቀሱ ክርስቲያን ወታደር ሊሆን አይገባውም ይላሉ። ጠላትን መከላከል እንደሚገባ ፈቀደ (ሉቃ. 14፥31:32)፥ ጳውሎስም የክርስቲያን ገርነት ውሱን መሆኑን (ሮም 12፥18)፥ መንግሥትም ራሱን በሰይፍ መጠበቅ እንደሚገባው አስተማረ (ሮም 13፥1-4) ይላሉ። ቢሆንም ክርስቲያን በጦርነት ሰውን መግደል የሚያሳዝን ነገር መሆኑን ማሰብ ይገባዋል። «ጦር ሠራዊት»፥ «የጦር መሣሪያ» ይመ.

**የጦርነት መጽሐፍ**፤ «የያሻር መጽሐፍ» ይመ.

**ጦቢት**፤ መጽሐፈ ጦቢት ሽማግሌው ጦቢት በንጉሡ በስልምናሶር ዘመን ወደ አሦር ከተማረከ በኋላ፥ እርሱና ልጁ ጦቢያ ተቸግረው ሳለ እግዚአብሔር በመልአኩ ሩፋኤል አማካይነት ረድቶአቸው ከችግር ሁሉ እንደወጡ የሚተርክ መጽሐፍ ነው። የኦርቶዶክስና የካቶሊክ አብ.ክ. ከብ.ኪ. መጻሕፍት ጋር ቈጥረው ይቀበሉታል። ስለ ቤተ መቅደስ መፍረስና መታደስ፥ ስለ ዮናስ ትንቢት ፍጻሜም ይናገራል፣ ጦቢት 14፥4-9። የጦቢት 4፥16ና የማቴ. 7፥12 ቃል አንድ ነው።

**ጦቢያ**፤ ነህምያን በመቃወም ሰንባላጥን የደገፈ አሞናዊ፣ ነህ. 2፥10:19:20፣ 4፥3:7:8፣ 6፥1-14:17-19። ካህኑም ኤልያሴብ ከእግዚአብሔር ቤት ጓዳዎች አንዱን ለመኖሪያ ሰጠው፣ ነህምያ ግን አስወጣው፣ ነህ. 13፥4-9። በመጽሐፈ ጦቢት ከተጠቀሰው ጦቢያ የተለየ ሰው ነው። *

**ጨለማ**፤ የብርሃን ተቃራኒ። በምሳሌነት ድንቁርናንና አለማስተዋልን (ኢዮብ 37፥19፣ ኢሳ. 9፥2)፥ ክፋትን (2ቆሮ. 4፥6፣ 1ዮሐ. 1፥5:6)፥ የኵነኔን ሁኔታም ያመለክታል፣ ማቴ. 22፥13። ደግሞም እግዚአብሔር የማይታይ መንፈስ ስለሆነ መሰወሪያው ጨለማ እንደሆነ ተነገሯል፣ መዝ. 18፥9:11።

**ጨረር**፤ የፀሐይ ብርሃን፥ በተለይ ጥዋትና ማታ የሚታየው ብርሃን ጨረር ይባላል፣ ዕን. 3፥4።

**ጨረቃ**፤ እግዚአብሔር በአራተኛው ቀን ጨረቃን ፈጠረ። ጨረቃ በሌሊት ይሠለጥናል፣ ዘፍ. 1፥16። በጨረቃ ወሮች ይቈጠሩሉ። «ወር»፥ «መባቻ» ይመ.። ጨረቃ እንደ ፀሐይ የዚህ ዓለም የማይናወጥ ሁኔታ ምሳሌ ነው፣ መዝ. 72፥5። ስለዚህ የጨረቃ ወደ ደም መለወጥ (በግርዶሽ ጊዜ) ለዓለም ለውጥና መጨረሻ ምሳሌ ሆነ፣ ኢዩ. 2፥31፣ ማር. 13፥24። አንዳንድ የጥንት ሰዎች ጨረቃን ያመልኩ ነበር፣ ኢዮብ 31፥26-28።

**ጨረባ**፤ ትንኞችን ከአየር የምትጠልፍ ወፍ። በብርድ ዘመን ወደ ደቡብ፥ ወደ ሙቀት አገር ትሄዳለች፣ ኢሳ. 38፥14፣ ኤር. 8፥7፣ ምሳ. 26፥2። «ወፎች» ይመ.

**ጨርቃም**፤ የስድብ ቃል፥ ውራጅ ለባሽ፥ የማይረባ፥ ከንቱ ማለት ነው። ንቀትንና ውርደትን ያመለክታል፣ ማቴ. 5፥22።

**ጨካኝ፥ ጭክና**፤ ምሕረት የሌለው፥ ሕገ ወጥ፥ ግፈኛ፣ ምሳ. 11፥17፣ ማቴ. 25፥24፣ ሉቃ. 19፥21፣ ይሁዳ 14-15።

**ጨዋታ**፤ በዕብራውያን መካከል ዘፈን (ኤር. 31፥4)፥ እንቆቅልሽና ታሪክ የተለመዱ ነበሩ፣ 1ነገ. 10፥1፣ ሕዝ. 17፥2። ልጆች እንደ ታላላቆች ይጫወቱ ነበር፣ ማቴ. 11፥16:17። በግሪክ ዓለም ብዙ ዓይነት የጨዋታ ውድድር ነበረ። በአዲስ ኪዳንም ሩጫና ቡጢ ለምሳሌ ተጠቅሷል፣ 1ቆሮ. 9፥24-27፣ 2ጢሞ. 2፥5፣ 4፥7:8፣ ዕብ. 12፥1:2።

**የጨዋታ ስፍራ**፤ እንደ አስቴድየም ያለ ብዙ ሰዎች ቴአትር (ድራማ) ወይም እስፖርት የሚመለከቱበት ቦታ። ሮማውያን በብዙ ከተማዎች የጨዋታ ስፍራዎችን ሠርተው ነበር፣ ሐ.ሥ. 19፥29።

**ጨው**፤ በጥንት ዘመን የጨው ጥቅም ልዩ ልዩ ነበረ።

1. የምግብ ማጣፈጫ፣ ኢዮብ 6፥6።
2. ከእህል ቍርባን (ከመሥዋዕት) ጋር የሚቀርብ፣

ዘሌ. 2፥13።

3. ለመድኃኒት፤ ሕዝ. 16፥4።

4. የቃል ኪዳን ማረጋገጫ፤ ዘኍ. 18፥19፤ 2ዜ.መ. 13፥5።

5. የጦር ሠራዊት የጠላትን ከተማ ሲያፈርስ አንዳንድ ጊዜ ወና እንዲሆን ጨው ይዘራበታል፤ መሳ. 9፥45። ጨው የፍርድ ምልክት ነው፤ ዘፍ. 19፥26፤ መዝ. 107፥34።

6. እንደ ገንዘብ ምንዛሪ ያገለግል ነበር፤ ዕዝ. 4፥14። ኢየሱስ ክርስቶስ ደቀ መዛሙርቱን የዓለም ጨው ሲል ሰየማቸው፤ ማቴ. 5፥13። በዚህ ምሳሌ ዓለም በኃጢአት እንዳይበላሽ ክርስቲያኖች እንደሚሠሩ ይገልጣል፤ ማር. 9፥50፤ ቆላ. 4፥6።

**ጨው ባሕር፤** በአቀማመጡ ከዓለም ሁሉ ዝቅ ያለ ባሕር። ከታላቁ ባሕር ጠለል 390 ሜትር ያህል ይቀንሳል። ርዝመቱ 80፥ ስፋቱ 15 ኪ.ሜ. ነው። ጨው ስለበዛበት ዓሣ የለበትም። የጨው ባሕር (ዘፍ. 14፥3፤ ዘኍ. 34፥3፤ ዘዳ. 3፥17፤ ኢያሱ 3፥16፤ 2ሳሙ. 8፥13፤ 2ነገ. 14፥7)፥ አንዳንድ ጊዜም በመ.ቅ. የዓረባ ባሕር ተብሎ ይጠራል፤ ዘዳ. 3፥17፤ ኢያሱ 3፥16፤ 12፥3፤ 2ነገ. 14፥25። ከ. 2ለ።

**ጫጉላ፤** ሙሽራና ሙሽራይት በተጋቡ ጊዜ ለተወሰነ ጊዜ የሚኖሩበት ቤት (ጕጆ)፤ ኢዩ. 2፥16።

**ጭራሮ፤** ደረቅ እንጨት። ጭራር የሚባለው በተለይ ቀጫጭን የሆነና በቁሙ የደረቀ፥ ለማገዶ የሚያገለግል ነው፤ ሐ.ሥ. 28፥3።

**ጭሬ፤** አጭር ልሳነ ጠባብ ጦር፤ 1ሳሙ. 17፥6:45። «የጦር መሣሪያ» ይመ.

**ጭቃ፤** በጥንት ዘመን የቤት መሥሪያ ጡብ ሸክላና የቤት ዕቃዎች ከጭቃ ይሠሩ ነበር። በአንዳንድ አገሮች ሰዎች ከጭቃ በተሠሩ ሸክላዎች ላይ ይጽፉ ነበር፤ ዘፍ. 11፥3፤ ዘጸ. 1፥14፤ ኤር. 18፥4፤ ሕዝ. 4፥1።



ጸሐፊ በጭቃ ላይ ሲቀርጽ

**የጭቃ ሰሌዳ፤** በልዩ ልዩ ዓይነት ቅርጽ ጭቃውን ከሠሩና የሚያስፈልጋቸውን ጽሑፍ ወይም ሥዕል ሳይደርቅ ከቀረጹ በኋላ በእሳት ወይም በፀሐይ ያደርቁት ነበር። በእስራኤልና በአቅራቢያዋ ባሉት አገሮች ይህን የመሰሉ ከጭቃ የተሠሩ ሰሌዳዎች ከመሬት ውስጥ ተገኝተዋል። እነዚህም ከ3000 ዓመት ከክ.ል. ጀምሮ የተሠሩ እንደሆኑ ተገምቷል፤ ሕዝ. 4፥1።

**ጭን፤** ሰው መሐላውን ለማጽናት ሲፈልግ እጁን ከሌላው ጭን በታች አድርጎ ይምላል፤ ዘፍ. 24፥2:9፤ 47፥29። ሰው በቶሎ እንዲሞት ጭኑ ይሰበር ነበር፤ ዮሐ. 19፥31:32።

**ጭንቁር፤** በሰውነት ላይ የሚወጣ አደገኛ ቍስል፤ 2ጢሞ. 2፥17። «በሽታ» ይመ.

**ጭንጋፍ፤** ያለቀኑ የወረደ ፅንስ፤ ኢዮብ 3፥16። በምሳሌያዊ አነጋገር ታናሽና ክብር የማይገባው ማለትን ያሳያል፤ 1ቆሮ. 15፥8።

**ጭንጫ ድንጋይ፤** ውስጡ የማይማስ ወይም ለእርሻ የማይጠቅም ድንጋያማ መሬት፤ ዘዳ. 8፥15፤ ማቴ. 13፥5።

**ጭጋግ፤** በበጋ ወራት እንደ ጥቁር ደመና ያለ መሬትን የሚሸፍን፥ እንደ ደመና ፀሐይን የሚጋርድ፤ ሐ.ሥ.13፥11። የፍርድ ቀን ሁኔታ በጭጋግ ተመስሏል፤ ሶፎ. 1፥15።

**ጰንጠቆስጤ፤** በግሪክ ቋንቋ ኀምሳኛ ማለት ነው። «በዓላት» ይመ.

**ጲላጦስ፤** ከ26-36 ዓ.ም. የነበረ የይሁዳ ገዥ። የጴንጤን አገር ሰው ወይም ጴንጤን የተባለ ቤተሰብ ወገን ነው። የሮምን ወታደሮች ሰንደቅ ዓላማዎች ወደ ኢየሩሳሌም በማምጣቱ አይሁድን አስቀየመ። በጭቃና ገዛ፤ ብዙ ሰዎችን አስገደለ፤ ሉቃ. 13፥1። ከገሊላ ገዥ ከሄሮድስ ጋር ተጣላ፤ ሉቃ. 23፥12። አይሁድ ኢየሱስን በትንግት የሞት ፍርድ እንደፈረዱበት ሰመቀ፥ ሚስቱም ስለ ኢየሱስ ፍርድ ሁኔታ አስጠነቀቀችው፤ ማቴ. 27፥18-19። ጲላጦስ ኢየሱስን ወደ ሄሮድስ በመላክ፥ በየፋሲካው እንደሚደረገው በመጠቀም በመማረፍም ሊያድነው ሞከረ፤ ሉቃ. 23፥6-25፤ ዮሐ. 19፥1-3። ጲላጦስ ኢየሱስ ንጹሕ እንደሆነ ሦስት ጊዜ መሰከረ፤ ሉቃ. 23፥4:15:22። የኢየሱስን መንፈሳዊ ሥልጣን ፈራ፤ ዮሐ. 18፥33-38፤ 19፥7-11። ሆኖም ሁከትን ስለፈራ እጁን ታጠበና ፍርድን አጓደለ፤ ኢየሱስንም ለሞት አሳልፎ ሰጠ፤ ማቴ. 27፥24-26። በአይሁድ አልተደሰተምና የኢየሱስን የክስ ጽሕፈት ለመለወጥ ፈቃደኛ አልነበረም፤ ዮሐ. 19፥19-22። ግን ለዮሴፍ የኢየሱስን ሥጋ ፈቀደ፤ ማር. 15፥42-47። አይሁድ መቃብሩ እንዲጠበቅ ሲለምኑ በራሳቸው ጠባቂዎች እንዲያስጠብቁት አዘዛቸው፤ ማቴ. 27፥62-66። ከዚህ በኋላም ብዙ ሳምራውያንን ያለ ምክንያት ስላስገደለ፥ በ36 ዓ.ም ተከስሶ ተሻረ፤ በገዛ እጁም

እንደሞተ ይተረካል። አንዳንዶችም እምኖ ሞተ ይላሉ።

**ጲስድያ፤** ብዙ ሽፍቶችና ሕገ ወጥ ነገዶች የነበሩበት ተራራማ አገር። ዋና ከተማው አንጾኪያ ነበረ፤ ሐ.ሥ. 13፥14፤ 14፥24፤ 2ቆሮ. 11፥26። በታው የሚገኘው ዛሬ ቱርክ በተባለው አገር ውስጥ ነው። ካ. 6በ።

**ጳስኮር፤** 1. በኤርምያስ ዘመን የእግዚአብሔር ቤት አለቃ የነበረ የኢሜር ልጅ። ኤርምያስን ተቃውሞ በእግር ግንድ አሰረው። ኤርምያስም የጳስኮርን መማረክ ተነበየ፤ ኤር. 20፥1-6። 2. የይሁዳ ንጉሥ ሴዴቅያስ ወደ ኤርምያስ የላከው የመልክያ ልጅ፤ ኤር. 21፥2። እርሱም ኤርምያስን ከተቃወሙትና በጭቃ ጉድጓድ ከጣሉት አለቆች አንዱ ነበረ፤ ኤር. 38፥1-6። 3. ኤርምያስን ከተቃወሙት አለቆች የአንዱ የጎዶልያስ አባት፤ ኤር. 38፥1-6።

**ጳትሮስ፤** በደቡብ ግብጽ ያለ አገር፤ ኢሳ. 11፥11፤ ኤር. 44፥1። ፈትሩሲም የሚባሉ ነገዶች ይኖሩበት ነበር፤ ዘፍ. 10፥13-14፤ 1ዜ.መ. 1፥11-12።

**ጳንጦስ፤** በትንሹ እስያ በስተሰሜን ያለ አገር። ዛሬ በቱርክ ውስጥ ይገኛል፤ ሐ.ሥ. 2፥9፤ 1ጴጥ. 1፥1-2።

**ጳውሎስ፤** በተበተኑት አይሁድ ዘንድ እንደተለመደው ጳውሎስ ሁለት ስም ነበረው። የዕብራይስጥ ስሙ ሳውል ነበረ። በጳፉ ከበርያሱስ ጋር እስኪከራከር ድረስ በዚህ ስም ይጠራ ነበር። ከዚያ ቀጥሎ ግን በሮማዊ ስሙ ጳውሎስ ተብሎ ተጠራ፤ ሐ.ሥ. 13፥9።

የልጅነቱ ጊዜ፤ በጠርሴስ ከተማ ተወለደ፤ ሐ.ሥ. 21፥39። እዚያም ድንኳን መስፋትን ተማረ፤ ሐ.ሥ. 18፥3። የሮም ዜግነትን ከአባቱ ወረሰ፤ ሐ.ሥ. 22፥26-28። ነገር ግን አባቱ ከብንያም ወገን የሆነ ፈሪሳዊ ነበረ፤ ፊል. 3፥4-6፤ ሐ.ሥ. 23፥6። ለትምህርት ወደ ኢየሩሳሌም ተልኮ ስመ ጥር ከሆነው አስተማሪ ከገማልያል የሙሴን ሕግና የአይሁድን ወግ ጠንቅቆ ተማረ፤ ሐ.ሥ. 22፥3፤ 26፥4-5። ጕልማሳ በሆነ ጊዜ ስለ አይሁድ ሃይማኖት ቀንቶ በክርስቶስ ያመኑትን አጥብቆ ጠላቸው፤ ሊያጠፋቸውም ፈለገ። እስጢፋኖስ በተወገረ ጊዜ እዚያ ተገኝቶ በእርሱ መገደል ተስማማ፤ ሐ.ሥ. 7፥59-60፤ 8፥1-3፤ 9፥1-2።

በክርስቶስ ማመኑ፤ ጳውሎስ (ሳውል) አማኞችን ለማሳሰር ወደ ደማስቆ ሲጓዝ ሳለ ጌታ ኢየሱስ ክርስቶስ ከሰማይ ጠራው። ጳውሎስ ኃጢአቱን ተረድቶ በክርስቶስ አመነ፤ ሐ.ሥ. 9፥1-9፤ 22፥4-11፤ 26፥9-18። በኋላ ሐናንያ ወደ እርሱ ተልኮ ጳውሎስ ለወንጌል ሥራ በተለይም ወንጌልን ለአሕዛብ ለመስበክ እንደተጠራ ገለጸለት። ጳውሎስም በዚያ ጊዜ ተጠመቀ፤ ሐ.ሥ. 9፥10-19፤ 22፥12-16።

የመጀመሪያው የወንጌል ሥራው፤ በደማስቆ ምኵራቦች ጥቂት ቀን ሰበከ፤ ሐ.ሥ. 9፥20-22። በኋላ ወደ ዓረብ አገር ሄዶ እንደገና ወደ ደማስቆ ተመለሰ፤ ገላ. 1፥17። ከዚያም መሸሸ ግድ ሆነበት፤ ሐ.ሥ. 9፥23-25፤ 2ቆሮ. 11፥32-33። ጴጥሮስን ሊጠይቅ ወደ ኢየሩሳሌም ሄደ። ይህም ካመነ ከሦስት ዓመት በኋላ ነው፤ ገላ. 1፥18። ሐዋርያት ማመን አለማመኑን ሲጠራጠሩ በርናባስ ወደ እነርሱ አስገባው፤ ሐ.ሥ. 9፥26-28። አይሁድ ሊገድሉት ሲፈልጉ እግዚአብሔር ከዚያ ፈቀቅ እንዲል አዘዘው፤ ሐ.ሥ. 22፥17-21። ወደ ጠርሴስም ሄዶ አያሌ ዓመት እዚያ ተቀመጠ፤ ሐ.ሥ. 9፥29-30። በርናባስ ከዚያ ወደ አንጾኪያ አመጣው። አንድ ዓመት አብረው በአንጾኪያ አስተማሩ፤ ሐ.ሥ. 11፥25-26። ምጽዋትን ወደ ኢየሩሳሌም ወሰዱ፤ ሐ.ሥ. 11፥29-30፤ ገላ. 2፥1-10።

ጕዞዎቹ፤ አንደኛ ጕዞው፤ ሐ.ሥ. 13፤ 14። በ48 ዓ.ም. ገደማ ጳውሎስና በርናባስ ማርቆስም ከአንጾኪያ ቤ.ክ. ተልከው በመርከብ ተሳፍረው ወንጌልን ለማስተማር ተነሡ። በመጀመሪያ በቆጵሮስ ቀጥሎም ወደ ጲስድያና ወደ ሊቃኦንያ አገሮች ሄደው በልዩ ልዩ ከተማ ወንጌልን ከሰበኩ በኋላ የአማንያንን ማኅበሮች አቋቋሙ። ወደ አንጾኪያ በሚመለሱበት ጊዜ ያቋቋሙአቸውን አብ.ክ. እየጐበኙ የቤ. ክ. ሽማግሌዎችን ሾሙ። ካ. 6።

የኢየሩሳሌም ሸንጎ፤ በአንደኛውና በሁለተኛው ጕዞ መካከል እነጳውሎስ ወደ ኢየሩሳሌም ተላኩ። ከኢየሩሳሌም አንዳንድ አይሁድ ወደ አንጾኪያ መጥተው፥ አሕዛብ ካልተገረዙና የሙሴን ሕግ ካልጠበቁ ሊድኑ አይችሉም እያሉ ስላስተማሩ ብዙ ክርክር ተነሥቶ ነበር፤ ገላ. 2፥11-14፤ ሐ.ሥ. 15፥1-35።

ሁለተኛ ጕዞው፤ ሐ.ሥ. 15፥36-18፥22። ጳውሎስና ሲላስ ከአንጾኪያ ተነሥተው በሶሪያና በኪልቅያ በኩል ወደ ልስጥራን ሄዱ። በዚያም ጢሞቴዎስን አግኝተው ጕዞአቸውን ወደ መቄዶንያ ቀጠሉ (ሉቃስን ከጢሮአዳ እስከ ፊልጵስዩስ ይዘውት ሄዱ)። በፊልጵስዩስና በተሰሎንቄ በቤርያም ቤ.ክ. ተመሠረተ። ጳውሎስ ወደ ግሪክ አገር ገብቶ በአቴና ሰበከ። በኋላ በቆሮንቶስ ከተማ አንድ ዓመት ከስድስት ወር ተቀምጦ አስተማረ። አቂላንና ጵርስቅላን በኤፌሶን ትቷቸው ወደ ቂሣርያና ወደ አንጾኪያ መጣ። ካ. 6።

ሦስተኛ ጕዞው፤ ሐ.ሥ. 18፥23-21፥16። ጳውሎስ ከአንጾኪያ ተነሥቶ ወደ ገላትያ አገርና ወደ ፍርግያ በመሄድ አማኞችን አጸና። ቀጥሎም ወደ ኤፌሶን ሄዶ ለሦስት ዓመት ያህል እያስተማረ ተቀመጠ። ብዙዎችም አመኑ። ከኤፌሶን ወደ መቄዶንያና ወደ ቆሮንቶስ ሄዶ አብ.ክ.ን አጽናና። እንደዚሁም ወንጌልን እየሰበከና አማኞችን እያጸና ጕዞውን እስከ ኢየሩሳሌም ቀጠለ። ካ. 7።

እስራቱ፤ ሐ.ሥ. 21፥17-28፥31። ጳውሎስ በኢየሩሳሌም በቤተ መቅደስ ሳለ ተይዞ ታሰረ፥ ወደ ቂሣርያ ተልኮ ሁለት ዓመት ታስሮ ቆየ። ከዚያም በኋላ ወደ ቄሣር ይግባኝ ስላለ ወደ ሮም ተላከ። ሁለት

ዓመት ከታሰረ በኋላ ተፈትቶ የወንጌልን ሥራ ቀጠለ። እንደገና በሮም ታስሮ በ67 ዓ.ም. ተገደለ፤ 2ጢሞ. 1፥16-17፤ 2፥9፤ 4፥6-8።

*መደምደሚያ፤* በወንጌል ሥራ ከጳውሎስ የበለጠ አይገኝም፤ 1ቆሮ. 15፥8-10፤ 2ቆሮ. 12፥11-12። በአካል ደካማ ቢሆንም ስለ ክርስቶስ ብዙ መከራን ተቀበለ፤ 2ቆሮ. 11፥23-27፤ 12፥7-10። በክርስቶስ ኃይልን አገኘ፤ ፊል. 4፥12-13። ዋና ዓላማውም ክርስቶስን ማወቅ ነበረ፤ ፊል. 3፥7-14። የጳውሎስ ታላቅነት በተለይ በሦስት ረገድ ይታያል።

1. ወንጌል ባልተሰበከበት ቦታ አብ.ክ.ን መሠረተ። ይህንም ያደረገው ብቻውን ሳይሆን እነጢሞቴዎስን በማሠልጠን ነው።

2. አይሁድ ሆኑ አሕዛብ ያለ ግዝረትና ያለ እሪት ሕግ በእምነት እንዲጸኑ ቤ.ክ. መሠረታዊ ትምህርትን እንድትወስን አደረገ።

3. መልእክታትን በመጻፉ፥ ሉቃስንም በማስከተሉ የክርስትና ትምህርት እስከ አሁኑ ትውልድ እንዲዳረስ ምክንያት ሆነ።

**ጳጳስ፤** ቃሉ በግሪክ ቋንቋ «ኤጲስ ቆጶስ» ሲሆን መሠረታዊ ትርጉሙ «ጠባቂ»፥ «ተቈጣጣሪ» ማለት ነው። በአ.ኪ. «ጳጳስ» ና «ሽማግሌ» ማለት አንድ ሹመትን ያመለክታሉ፤ ሐ.ሥ. 20፥17:28። «ሽማግሌ» ይመ.

**ጳፉ፤** የቆጵሮስ ዋና ከተማ፤ ሐ.ሥ. 13፥6-13። ካ. 6ፕ።

**ጴርጋሞን፤** በጥንት ዘመን በትንሹ እስያ፥ የሚስያ ክፍለ አገር ዋና ከተማ። የነዋሪዎቹ ሃይማኖት ምልክት እባብ ነበረ። ለአውግስጦስ ቄሳር መቅደስ በዚያ ተሠርቶ ነበር። ጳውሎስ በኤፌሶን ሳለ ቤ.ክ. በዚያ የተመሠረተች ይመስላል፤ ሐ.ሥ. 19፥10። በጴርጋሞን ከተማ አማኞች በጽኑ ተፈተኑ፤ ራእ. 1፥11፤ 2፥12-17። ጴርጋሞን በነበረበት አጠገብ ትንሽ ከተማ ይገኛል። ካ. 7ሰ። «በለዓም» ይመ.

**ጴጥሮስ፤** ከዐሥራ ሁለቱ ሐዋርያት አንዱ። በመጀመሪያ ስምዖን ተባለ፥ በኋላ ግን ኢየሱስ ኬፋ ብሎ ሰየመው። በአራማይክ ኬፋ፥ በግሪክ ጴጥሮስ ማለት አለት ማለት ነው፤ ማር. 3፥16፤ ዮሐ. 1፥43። የትውልድ ቦታው ቤተ ሳይዳ ነበረ። እንደ አይሁድ ሊቃውንት ብዙ ትምህርት አልተማረም፤ ማር. 14፥70፤ ዮሐ. 1፥45፤ ሐ.ሥ. 4፥13። ከወንድሙ ከእንድርያስ ጋር ዓሣ እያጠመደ በቅፍርናሆም ኖረ፥ ሚስት ነበረችው፤ . ማር. 1፥29-30። እንድርያስ በመጀመሪያ ከኢየሱስ ጋር አስተዋወቀው፤ ዮሐ. 1፥41-43። በኋላም ኢየሱስ ሰዎችን እንዲያጠምድ (እንዲያሳምን) ጠራው፤ ማር. 1፥16-17፤ ሉቃ. 5፥1-11። ደቀ መዝሙር ሳለ ለሐዋርያነት ተጠራ፤ ማር. 3፥13-16። ሐዋርያት ያደረጉትን ሁሉ አደረገ፥ በተለይ ደግሞ ኢየሱስ የኢያኢሮስን ልጅ ሲያስነሣ (ማር. 5፥35-43)፥ በተራራ ክብሩን ሲገልጥ (ማር. 9፥2-8)፥ በጌቴሴማኒ ሲጸልይ ጴጥሮስ አብሮ ተገኘ፤ ማር. 14፥32-42። በባሕር ላይ እየተራመደ ወደ ኢየሱስ ለመሄድ ደፈረ፥ ግን ከእምነቱ ጉድለት የተነሣ ሊሰጥም ሲል ኢየሱስ አዳነው፤ ማቴ. 14፥28-31። ኢየሱስ ክርስቶስ (መሢሕ) መሆኑን መሰከረ፥ ነገር ግን ኢየሱስ በሞቱ ሰዎችን እንደሚያድን በመጀመሪያ አላስተዋለም፤ ማቴ. 16፥15-23። «መሢሕ» ይመ.። ኢየሱስን ለመያዝ የመጡትን ሰዎች በሰይፍ ለመከላከል ሞከረ፤ ዮሐ. 18፥10-11። በኋላም ሦስት ጊዜ ኢየሱስን ካደ፤ ማር. 14፥66-72። በትንሣኤ ዕለት ጴጥሮስ ወደ ጌታ መቃብር ሮጠ (ዮሐ. 20፥3-7)፥ በኋላ ኢየሱስ ታየው፤ ሉቃ. 24፥34። ኢየሱስ በገሊላ ባሕር ዳር «ትወደኛለህን?» እያለ ሦስት ጊዜ ጠየቀው፤ «በጎቼን አሰማራ» ካለውም በኋላ እንዴት እንደሚሞት ነገረው፤ ዮሐ. 21፥1-23።

ከዕርገት በኋላ የክርስቶስ ተከታዮች መሪ ነበረ (ሐ.ሥ. 1፥15-22)፥ በበዓለ ኀምሳ ዕለት ሰበከ፤ ሐ.ሥ. 2፥14-42። ከዮሐንስ ጋር አንካሳ ፈወሰ፥ ከዚህም የተነሣ በሸንጎ ተጠየቀ፥ ቀጥሎም ተገረፈ፤ ሐ.ሥ. 3፥1-4፥22፤ 5፥17-42። ትዋታላችሁ ባላቸው መሠረት ሐናንያና ሰፊራ ሞቱ፤ ሐ.ሥ. 5፥1-11። ወደ ሰማርያ እንዲሄድ በሐዋርያት ተመረጠ፤ በብዙ መንደሮች ወንጌልን ሰበከ፤ ሐ.ሥ. 8፥14-25። ወደ ልዳና ወደ ኢዮጴ ሲሄድ በሽተኞችን ፈወሰ፤ ሐ.ሥ. 9፥32-43። በኢዮጴ ሳለ ራእይ አየና በጌታ ትእዛዝ ወደ ቆርኔሌዎስ ቤት ሄደ። እዚያም ወንጌልን በመስበኩ አሕዛብ ወደ ቤ.ክ. ሊገቡ ቻሉ፤ ሐ.ሥ. 10። ወደ ኢየሩሳሌም ሲመለስ አንዳንዶች ተከራከሩ፥ ጴጥሮስ ግን እግዚአብሔር እንዴት እንደመራው ነገራቸው። ቤተ ክርስቲያንም ወንጌል ለአሕዛብ ጭምር እንደተሰጠ ተረዳች፤ ሐ.ሥ. 11፥1-18። በሄሮድስ ታሰረ፤ ምእመናን ሲጸልዩለት ግን በእግዚአብሔር መልአክ ተፈታ፤ ሐ.ሥ. 12፥1-17። ወደ አንጾኪያ ሲወርድ መጀመሪያ ከአሕዛብ ጋር በላ፥ ግን አይሁድን ፈርቶ አፈገፈገ። ከአሕዛብ ጋር የነበረውን ግንኙነት ሲያቋርጥ ጳውሎስ ወቀሰው፤ ገላ. 2፥11-16። በኢየሩሳሌም ጉባኤ ስለ አሕዛብ ጳውሎስ ያቀረበውን አሳብ ደገፈ፥ ሰዎች ሁሉ በአንድ መንገድ እንደሚድኑ መሰከረ፤ ሐ.ሥ. 15፥7-11። ሁለት መልእክቶችን ጻፈ። በኔሮ ዘመነ መንግሥት በሮም ከተማ ተሰቅሎ ሞተ።

ከዚህ በላይ ከተዘረዘሩት ታሪኮች ሌላ ጴጥሮስ በተፈጥሮው ኃያልና ጉበዝ እንደነበረ ይታያል። ችኩል ነበረና ነገሩን ሁሉ ጠለቅ ብሎ ባለማስተዋል አንዳንድ ጊዜ ስሕተት ውስጥ ይገባ ነበር። ስሕተቱን ሲያውቅ ከልቡ አዘነ፤ ሉቃ. 5፥8፤ ማር. 14፥72። በሙሉ ልቡ ክርስቶስን ማስደሰትና መከተል ፈለገ፤ ዮሐ. 21፥17። እንደ አይሁድ ሊቃውንት ባይማርም፥ የጳውሎስ ትምህርት አንዳንድ ጊዜ ከባድ መሆኑን ቢመሰክር እንኳን፥ ወንጌልን በግልጥ ሰበከ (2ጴጥ. 3፥16)፥ ብዙ ሰዎችንም አሳመነ። ጴጥሮስ የሐዋርያት መሪ እንደሆነ ግልጥ ነው፤ ደግሞም ከሌሎች ሐዋርያት ይልቅ ልዩ ሥልጣን እንደተሰጠው እናስተውላለን፤ ማቴ. 16፥18-19። ይህንም የተቀበለው ለአይሁድና ለአሕዛብ የወንጌልን በር እንዲከፍት ነው። ግን ይህን ልዩ ሥልጣን ለሌሎች እንዳስተላለፈ ወንጌል አይገልጥም። «ሐዋርያ»፥

«ማሰርና መፍታት»፣ «መክፈቻ»፣ «የቤተ ክርስቲያን አስተዳደር» ይመ.

## የጴጥሮስ መልእክት 1ኛው፤

ቅዱስ ጴጥሮስ ይህን መልእክት የጻፈው በጨካኙ ቄሣር በኔር ዘመን በ63 ዓ.ም. ሳይሆን አይቀርም። በዛሬው ሰሜን ቱርክ አገር ለኖሩት ክርስቲያኖች ሲጽፍ፣ በስደት ጊዜ እንዲበረቱና እንደሚገባ እየተመላለሱ የተዘጋጀላቸውን ክብር እንዲጠብቁ ይመክራቸዋል። መልእክቱ በስልዋኖስ እጅ «ከባቢሎን» ተጻፈ፤ ባቢሎን ሲል ምናልባት በግብጽ ያለ ቦታን ወይም ሮምን ያመለክት ይሆናል፤ 5፥12-13።

ጴጥሮስ አንባቢዎቹን በእግዚአብሔር ጸጋ እንዲቆሙ ሲመክራቸው (5፥12) ለሚከተሉት ነጥቦች አጽንኦት ይሰጣል ፦

ሀ) የክርስቲያን ክብርና ተስፋ፤ 1፥1-2:3-5፤ 2፥4-10፤ 3፥14-18፤ 4፥14፤ 5፥4:10።

ለ) የክርስቶስ ሞት ምክንያትና አርአያነት፤ 1፥1-2:18-19፤ 2፥21-24፤ 3፥18፤ 4፥1-2:13።

ሐ) የፊተኛውና የአሁኑ ኑሮአቸው ልዩነት፤ 1፥14:18-19፤ 2፥25፤ 4፥3።

መ) ክርስቲያናውያን ትእግሥት፤ 1፥13-5፥9።

ሠ) የእግዚአብሔር ቃል አሠራር፤ 1፥10፤ 23-25፤ 2፥2-3።

ረ) ብ.ኪ. በአ.ኪ. መፈጸሙ፤ 1፥10-12:18-19፤ 2፥4-10፤ 3፥10-12።

አከፋፈል ፦

1. በሥላሴ ግብር ላይ የተመሠረተ ሰላምታ፤ 1፥1-2።

2. ክርስቲያን የሚያቀርበው ምስጋና፤ 1፥3-12።

3. ክርስቲያን የተጠራለት ቅድስና፤ 1፥13-5፥11።

ሀ) የቅድስና ምክንያት፤ የክርስቶስ መገለጥ፣ የእግዚአብሔር ባሕርይ፣ የክርስቶስ ሥራ፣ የአማኝ ዳግመኛ መወለድ፤ 1፥13-2፥3፤

ለ) የቅድስና ሁኔታ፤ አማኞች ፦ መንፈሳዊ ቤት፣ የተመረጠ ሕዝብና በዓለም እንግዶች መሆናቸው፤ 2፥4-12፤

ሐ) የቅድስና ጠባይ፤ አክብሮት በቤተ መንግሥት፣ በሥራ፣ በክርስቶስ ሕይወት፣ በቤተሰብ፤ 2፥13-3፥7፤

መ) በልዩ ልዩ ሁኔታዎች የቅድስና መገለጥ፤ በሁሉም ወገድ (3፥8-17)፣ በክርስቶስ አርአያነት (3፥18-4፥6)፣ በዓለም መጨረሻ መቃረብ (4፥7-11)፣ በፈተና ዘመን (4፥12-19)፣ በሽማግሌዎች አገልግሎት (5፥1-4)፣ በአጠቃላይ አካሄድ (5፥5-11)።

4. የጴጥሮስ ሁኔታና ቡራኬ፤ 5፥12-14።

## የጴጥሮስ መልእክት 2ኛው፤

መልእክቱ በቅዱስ ጴጥሮስ እንደተጻፈ ይነገራል፤ 1፥1:16-18 (ከማቴ. 17፥1-5 ጋር አስተያይ)፤ 3፥1:15። ሐዋርያው የሚሞትበት ጊዜ እንደተቃረበ ይታያልና ዘመኑ 67 ዓ.ም. ገደማ ሊሆን ይችላል፤ 1፥12-15። 1ኛው የጴጥሮስ መልእክት በቤ.ክ ላይ ከውጭ የሚመጣውን ስደት ሲያመለክት፣ 2ኛው መልእክት ከውስጥ የሚነሣውን ስሕተት ይቃወማል። ሐሰተኞች የራሳቸውን «ዕውቀት» ያጋንኑ ነበር፤ «ግኖስቲክ» ይመ.። ም. 2ን ከይሁዳ መልእክት ጋር ስናስተያየው ያም መልእክት ስለ እነዚህ ሐሰተኞች ሳይጻፍ እንዳልቀረ መገመት ይቻላል።

በዚህ መልእክት ጴጥሮስ አረኛ ሆኖ (1፥12-15፤ 3፥1-2:12-14፤ ዮሐ. 21፥15-17)፥ ወዳጆቹ በእውነተኛ ዕውቀት መሠረት እንዲያድጉ፣ ሐሰትን እንዲቃወሙና የክርስቶስን ዳግም ምጽአት በእምነት እንዲጠባበቁ ይጽፍላቸዋል።

አከፋፈል ፦

1. ክርስቶስን የማወቅ በረከት፤ 1፥1-4።

2. የዕውቀት ሁኔታ፤ 1፥5-21፤

የዕውቀት፥ ሀ) ሂደት (5-7)፣ ለ) ጥቅም (8-11)፣ ሐ) አስፈላጊነት (12-15)፣ መ) መሠረት (16-21)።

3. የዕውቀት ተቃራኒ፤ ም.2፤

የሐሰተኞች፥ ሀ) መነሣት (1-3)፣ ለ) ፍርድ (4-10)፣ ሐ) ጠባያት (11-22)።

4. የዕውቀት ፍጻሜ፤ ም.3፤

ሀ) የክርስቶስ ዳግም ምጽአት እርግጠኛነት (1-10)፥

ለ) የአንባቢዎች የአፀፋ ምላሽ (11-18)።

**ጵርስቅላ፤** «አቂላ» ይመ.

**ጵንፍልያ፤** በሐዋርያው ጳውሎስ ዘመን የነበረች በትንሹ እስያ በስተደቡብ በታላቁ ባሕር ጥግ የተገኘች ታናሽ የሮም ክፍለ አገር። በጰንጠቆስጤ ቀን ከጵንፍልያ የመጡ ሰዎች በኢየሩሳሌም ተገኙ፤ ሐ.ሥ. 2፥10። ጳውሎስ በመጀመሪያ ጉዞው በዋና ከተማዋ በጴርጌን ወንጌልን ሰበከ፤ ሐ.ሥ. 13፥13፤ 14፥24-25፤ 15፥38። ዛሬ ጵንፍልያ በቱርክ ውስጥ ትገኛለች።

**ጸሎተ ምናሴ፤** የይሁዳ ንጉሥ ምናሴ ታስሮ ሳለ የጸለየው ጸሎት ነው። በትልቁ የአማርኛ መጽሐፍ ቅዱስ ከ2ኛ ዜ.መ. 33፥12 ቀጥሎ ታትሟል።

**ጸሎት፤** ሰው በእግዚአብሔር መልክና ምሳሌ ለእግዚአብሔር ስለተፈጠረ ከእግዚአብሔር ጋር ለመገናኘት ይፈልጋል። መገናኛውም ጸሎት ስለሆነ ይጸልያል። በማንኛውም ሃይማኖት ጸሎት አለ። የክርስቲያን ጸሎት ግን በክርስቶስ አማካይነት ስለሆነ ሁኔታው የተለየ ነው። ጸሎት ከእግዚአብሔር ጋር ያለን የመገናኛ ምልክትና የግንኙነታችን ማጽኛ ነው።

ጸሎት ኅብረትን፣ ምስጋናን፣ ስግደትን፣ ንስሓን፣ ልመናን፣ ምልጃን ያጠቃልላል። ሰዎች በልዩ ልዩ አቋቋም፣ በታና ጊዜ ሊጸልዩ ይችላሉ። ዋናው ነገር ግን የልብ መሰበር ነው፤ ዮሐ. 4፥20-24። እነሙሴ፣ እነሳሙኤልና እነጳውሎስ ጸሎታቸውን ጽፈውልናል። ዳዊትም የጸሎት መጽሐፍ አበርክቶልናል። ክርስቶስ በቃልም በሥራም የጸሎትን መንገድ አስተምሮናል፤ ሉቃ. 11፥1-13፤ 18፥1-14፤ ዮሐ. 17። እግዚአብሔር የልጆቹን ጸሎት በደስታ ይሰማልና ጸሎት ብዙ ኃይል አለው፤ 1ጴጥ. 3፥12፤ ያዕ. 5፥17። አለመጸለይ ኃጢአት ነው፤ 1ሳሙ. 12፥23።

ጸሎታችን እንደሚከተለው መሆን አለበት ፦

1. በእምነት፤ ዕብ. 11፥6።
2. በኢየሱስ ስም፤ ዮሐ. 14፥6:13፤ 16፥23።
3. እንደ እግዚአብሔር ፈቃድ፤ 1ዮሐ. 5፥14-15።
4. በመንፈስ ቅዱስ፤ ይሁዳ 20።
5. ንስሓ በመግባት፤ መዝ. 66፥18፤
   ኢሳ. 59፥1-2፤ ማቴ. 5፥23-24።
6. ይቅር ባይ በመሆን፤ ማቴ. 6፥14-15።
7. ባለመሰልቸት፤ ሉቃ. 11፥5-13።
8. በነገር ሁሉ፤ ፊል. 4፥6።
9. ስለ ሰው ሁሉ፤ 1ጢሞ. 2፥1-4።
10. በማንኛውም ጊዜ ሁሉ፤ 1ተሰ. 5፥17። «አቡነ ዘበሰማያት» ይመ.

**ጸራቢ (ጠራቢ)፤** ለቤት ሕንፃ፣ ለግብርናና ለሌላም ሥራ ሁሉ የሚውለውን ዕቃ ከድንጋይና ከእንጨት የሚሠራ፤ 1ነገ. 7፥9፤ 2ዜ.መ. 34፥11፤ አሞጽ 5፥11። ዮሴፍ (ማቴ. 13፥55)፣ ኢየሱስም (ማር. 6፥3) ጸራቢዎች ነበሩ። «ተግባረ እድ» ይመ.

**ጸባኦት፤** በዕብራይስጥ ቋንቋ ጸባኦት ማለት ሠራዊት፣ ጭፍራ ማለት ነው። በብ.ኪ. የሠራዊት ጌታ ተብሎ የተተረጐመው በአ.ኪ. እንዳለ «ጸባኦት» ተብሏል፤ ኢሳ. 1፥9፤ ሮም 9፥29፤ ያዕ. 5፥4። እንደ ዕብራይስጡ ትክክለኛ አሳብ የጸባኦት ጌታ እንጂ ጌታ ጸባኦት አያሰኝም። ይህም የሠራዊት ጌታ እንደ ማለት ነው።

**ጸናጽል፤** ከናስና ከብር፣ ከሌላም የሚሠራ የዜማ ዕቃ። እንዲንቧቧ ናስም ሆነ ብረት ይደረግበታል። ለእግዚአብሔር ክብር ይዘመርበታል፤ 2ሳሙ. 6፥5፤ መዝ. 150፥5፤ 1ዜ.መ. 13፥8፤ 2ዜ.መ. 5፥13፤ 1ቆሮ. 13፥1።

**ጸጋ፤** «ካሪስ» የሚለውን የግሪክ ቃል የሚተረጕም ሲሆን፣ ሦስት የዕብራይስጥ ቃላትን አሳብ ይይዛል፤ እነርሱም «ሞገስ»፣ «ፍቅር» እና «ምሕረት» (ወይም «ቸርነት») በተሰኙት የአማርኛ ቃላት ይተረጐማሉ። የእግዚአብሔር ጸጋ በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ በሙላ ቀርቧል፤ ዮሐ. 1፥16:17። የዘላለም ሕይወት የጸጋ ስጦታ ነው፤ ሮም 6፥23። ስለዚህ ጸጋ እግዚአብሔር በተለይ ለሰው ያሰው



ጸናጽል

መልካም አስተያየትና የሚያፈልቀው ፍጹም ፍቅር ነው፤ ሉቃ. 1፥28፤ ቲቶ 2፥11። ጸጋ ለሰው ሁሉ የሚገለጠው ከእግዚአብሔር ቸርነት የተነሣ እንጂ ማንም ሰው የተገባው ሆኖ አይደለም፤ ሮም 4፥4-5፤ 5፥6፤ ኤፌ. 2፥4። እግዚአብሔር በጸጋው ደኅንነትን ፈጽሞልናል፤ ኤፌ. 2፥6-8፤ 2ጢሞ. 1፥9። የእግዚአብሔርን ጸጋ የምንቀበለው በጌታ በኢየሱስ ክርስቶስ በማመን ነው፤ ዕብ. 4፥16፤ ኤፌ. 2፥8። ያለ ክርስቶስ በሕግ ወይም በሥራ እንጸድቃለን ብንል የጸጋው ተቀባዮች ልንሆን አንችልም፤ ገላ. 5፥4-5፤ ሮም 8፥1-2፤ 5፥1:15-17። የእግዚአብሔር ጸጋ ምእመናንን ያጸናል (ሐ.ሥ. 20፥32፤ 2ቆሮ. 9፥14፤ 12፥9፤ 2ጢሞ. 2፥1)፤ ልዩ ልዩ መንፈሳዊ ስጦታን ይሰጣል፤ ሮም 12፥6-8፤ ኤፌ. 3፥8። ይህንን ጸጋ ቸል እንዳንለው መጠንቀቅ አለብን፤ ሮም 6፤ ይሁዳ 4።

**ጸፉ፤** መቃ። በብስጭትና በጸጸት ጊዜ የሚሆን ድርጊትን ያመለክታል፤ ኤር. 31፥19።

**ጸፍጸፍ፤** በመሬት ላይ የሚሆን የድንጋይ ወይም የእንጨት ንጣፍ። በኢየሩሳሌም ጸፍጸፍ የተባለ የፍርድ አደባባይ ነበረ፤ በዚህ ስፍራ ጲላጦስ ኢየሱስን አሳልፎ ሰጠ፤ ዮሐ. 19፥13።

**ጺቅላግ፤** ከቤርሳቤሕ በስተሰሜን 15 ኪ. ሜ. ርቆ የሚገኝ ከተማ። የጌት ንጉሥ አንኩስ ጺቅላግን ለዳዊት ሰጠ (1ሳሙ. 27፥1-7)፣ ዳዊትም ከዓመት በላይ በዚያ ተቀመጠ፤ 2ሳሙ. 1፥1። በኋላ ግን እንደ ይሁዳ ነገሥታት ከተማ ተቈጠረ።

**ጺቅ አለ፤** ምራቁን ተፋ፣ ተጸየፈ፣ ናቀ፤ ኢዮብ 17፥6።

**ጺን፤** ከቤርሳቤሕ በስተደቡብ የሚገኝ ምድረ በዳ። እስራኤላውያን ከግብጽ ከወጡ በኋላ ለረጅም ጊዜ በጺን ሰፈሩ፤ ዘኍ. 13፥21፤ 33፥36።

**ጻድቅ፤** ጻድቃን፤ በሕግ የጸና፣ እንደ ሕግ የሚኖር እውነተኛ። እግዚአብሔር በባሕርዩ ጻድቅ ነው፤ ዕዝ. 9፥15፤ 2ጢሞ. 4፥8። ሰዎች እንደ እግዚአብሔር ሕግ ሲኖሩ ጻድቃን ይባላሉ። ይህ ማለት ያለ ስሕተት ናቸው፤ ምንም ኃጢአት አልሠሩም ማለት ሳይሆን አካሄዳቸውን በእግዚአብሔር ፊት አደረጉ፤ እንደ ሕጉም ኖሩ ማለት ነው። ለምሳሌ ኖኅና ዘካርያስ ጻድቃን ተባሉ። ነገር ግን ጕድለት

ተገኝተባቸዋል፤ ዘፍ. 6፥9፤ 9፥21፤ ሉቃ. 1፥6 እና 1፥18-20። በእስራኤል ዘንድ ብዙዎች ሕግን በመጠበቅ ራሳቸውን እንደ ጻድቃን ቈጠሩ፤ ነገር ግን ለእግዚአብሔር መንግሥት አልበቁም፤ ማቴ. 5፥20፤ ሉቃ. 18፥9-14፤ ሮም 10፥3። ከክርስቶስ በቀር ፍጹም ጻድቅ አይገኝም፤ ሮም 3፥11-18፤ 1ጴጥ. 3፥18። እንደ ዳዊትና ኢሳይያስ፣ እንደ ጴጥሮስና ጳውሎስ ያሉ ታላላቅ የእግዚአብሔር ሰዎች ኃጢአት አድርገው ኃጢአተኝነታቸው ተሰማቸው፤ መዝ. 51፥4፤ ኢሳ. 6፥5፤ ሉቃ. 5፥8፤ 1ጢሞ. 1፥15። ነገር ግን በክርስቶስ የሆኑ ሁሉ ጻድቃን ናቸው። መንግሥተ ሰማያትንም ይወርሳሉ፤ ማቴ. 25፥46፤ ሮም 5፥19። ይህ የሚደረግላቸው የክርስቶስ ጽድቅ ስለተቈጠረላቸው ነው፤ 1ቆር. 1፥30:31፤ 2ቆር. 5፥21። «ጽድቅ» ይመ.

**ጻፊ፣ (ጸሓፊ)፤** በነገሥታት ዘመን በቤተ መንግሥት አገልጋዮችና አማካሪዎች ሆኑ፤ 1ዜ.መ. 27፥32። ጥሩ ልብስ ለብሰው የቀለም ቀንድ በወገባቸው ይይዙ ነበር፤ ሕዝ. 9፥2። ከምርኮ በኋላ እንደ ዕዝራ የሕግ ምሁራን ሆኑ፤ ዕዝ. 7፥6። በመጀመሪያ ካህናት ነበሩ፣ በኋላም ራሳቸውን ችለው ልዩ ቡድን ሆኑ። በደንባቸው መሠረት ለዕለት ኑሮአቸው አስፈላጊውን ነገር በእጅ ሥራ እያገኙ በነፃ ሕግን ያስተምሩ ነበር፤ ጳውሎስ በዚህ ዓይነት ሥራ እየተጠቀመ ወንጌልን ይሰብክ ነበር፤ ሐ.ሥ. 20፥34።

የጻፊ ሥራ ሦስት ዓይነት ነበረ፤ ይኸውም የሙሴን ሕግ በትክክል መተርጐም (ማር. 7፥1-13)፣ ለሰዎች ሕግን ማስተማር (ሉቃ. 2፥46)፣ ዳኛ መሆን (ሉቃ. 22፥66) ነበረ። ሕጉ እንዳይጣስ የሽማግሌዎች ወግ የተባለውን አጥር አበጁ። ይህንም በሕዝብ ጫንቃ ላይ ጫኑት፤ ማቴ. 15፥2-6። ክርስቶስ ስለ ግብዝነታቸው ብዙ ጊዜ ወቀሳቸው፤ ማቴ. 23፤ ሉቃ. 20፥46-47። ከጻፎች ብዙዎቹ የፈሪሳውያን አሳብ ደጋፊዎች ነበሩ፤ ሐ.ሥ. 23፥9። ጻፎች ክርስቶስንና ሐዋርያትን ተቃወሙ፤ ማቴ. 26፥57፤ ሐ.ሥ. 4፥1-5።



የእስራኤል ሕግ ጸሓፊ ለሕዝብ ሲያነብ

**ጽላት፤** የተጠረቡ ድንጋዮች። ዐሥርቱ ቃላት በሁለቱ ጽላት ላይ በእግዚአብሔር ጣት ተጻፉ። እነዚህም የምስክር ጽላት ተባሉ፤ ዘጸ. 31፥18፤ 34፥1፤ ዘዳ. 4፥13፤ 5፥22። በሙሴ እጅ የተቀረጹት፣ በእግዚአብሔር እጅ የተጻፈባቸው ሁለቱ ጽላት የት እንደደረሱ አልታወቀም። ጽላት የልብ ምሳሌ ሊሆን ይችላል፤ 2ቆር. 3፥3። «ታቦት» ይመ.

**ጽሑፍና ጽሕፈት፤** በብሉይ ኪዳን ሙሴ፣ ኢያሱ፣ ሳሙኤል፣ ዳዊት፣ ኢሳይያስ፣ ባሮክ፣ ዕዝራ፣ ሌሎችም ጽፈዋል ተብለው ተገልጸዋል፤ ዘኍ. 33፥2፤ ኢያሱ 8፥32፤ 1ሳሙ. 10፥25፤ 2ሳሙ. 11፥14፤ 2ዜ.መ. 26፥22፤ ኤር. 30፥2፤ ዕዝ. 8፥34። እንዲሁም በጸሓፊነት ሙያ የሠለጠኑ ሰዎች ነበሩ፤ 1ዜ.መ. 2፥55፤ 24፥6።



የጽሕፈት መሣሪያዎች

በአዲስ ኪዳንም ዘካርያስ፣ ጌታችን፣ ሐዋርያው ዮሐንስ፣ ሉቃስ፣ ጳውሎስ፣ ጤርጥዮስ፣ ሌሎችም ጽፈዋል ተብለው ተገልጸዋል፤ ሉቃ. 1፥63፤ ዮሐ. 8፥6፤ 21፥24፤ ሉቃ. 1፥1-4፤ ገላ. 6፥11፤ ሮም 16፥22። ብዙውን ጊዜ ቃሉን የተቀበሉት በጸሓፊዎች ያስጽፉ ነበር፤ ኤር. 36፥32፤ ሮም 16፥22።

ጽሑፉ በዓለት ላይ፣ በሰሌዳ፣ በጡብና በብራና ይጻፍ ነበር፤ ኢዮብ 19፥24፤ ኢሳ. 30፥8፤ ሕዝ. 4፥1፤ 2ጢሞ. 4፥13። ለመጻፊያ በብዕርና በቀለም ይጠቀሙ ነበር፤ ኤር. 8፥8፤ 3ዮሐ. 13፤ 2ዮሐ. 12። ጽሑፉም የሰሌዳ፣ የጥቅልል ወይም የጥራዝ መልክ እንዲይዝ ይደረግ ነበር፤ ኢሳ. 8፥1፤ 34፥4፤ 2ጢሞ. 4፥13።

ቅዱሳት መጻሕፍትን የገለበጡ ጸሓፊዎችና ተርጓሚዎች በብዙ ጥንቃቄ እንደሠሩ ታሪካቸው ይመሰክርላቸዋል። ሆኖም አንዳንድ ጊዜ መሳሳታቸው አልቀረምና ጥንታውያን የቅዱሳት መጻሕፍት ግልባጮችና ትርጒሞች በብዙ ሳይሆን በጥቂት ይለያያሉ።

የእግዚአብሔር ቃል በጽሑፍ ሲወርድ ሲዋረድ የመጣ ስለሆነ፣ አይሁድና ክርስቲያኖች ምን ጊዜም ልጆቻቸው ንባብና ጽሕፈት እንዲማሩ ለማድረግ ብዙ ጥረዋል፤ ዘዳ. 6፥4-9፤ ሲራክ 8፥8-9፤ 30፥1-6።

**ጽሕፈት፤** ምዝገባ። ግብር ለመክፈል ወይም ለሌላ ምክንያት ሰዎች ሁሉ እንዲመዘገቡ ሲታዘዝ ጽሕፈት ይባላል። በሮም ዘመን መንግሥት ልዩ ልዩ ጽሕፈት እንደነበረ ከዓለም ታሪክ ታውቋል፤ በሉቃ. 2፥1-3 የተጠቀሰው ጽሕፈት በየትኛው ዓመት እንደነበረ ለመወሰን አልተቻለም። በሐ.ሥ. 5፥37 የተጠቀሰው ግን በ6 ዓ.ም. ነበረ። «ዓመፅ» ይመ.

**ጽሩያ፤** የዳዊት እኅት። ልጆቿም አቢሳ፥ ኢዮአብ፥ አሣሄል ነበሩ፤ 1ዜ.መ. 2፥16፤ 2ሳሙ. 17፥25፤ 1ሳሙ. 26፥6፤ 2ሳሙ. 2፥18።

**ጽርአ፤** «ለምጽ» ይመ.

**ጽዋ፤** ከብዙ ነገር በልዩ ልዩ ዓይነትና መልክ ሊሠራ የሚችል መጠጫ ዕቃ። በምሳሌነት እግዚአብሔር ለሰው ያቀደውን በረከት ወይም መከራ ያመለክታል፤ መዝ. 11፥6፤ 16፥5፤ 23፥5፤ ማቴ. 20፥22-23፤ 26፥39፤ ዮሐ. 18፥11፤ ራእ. 15፥7።

**ጽዮን፤** ኢየሩሳሌም ከተመሠረተችባቸው ተራራዎች አንዱ። ቃሉ አምባ ማለት ነው። መጀመሪያ በኢያቡሳውያን ተመሽጎ፤ ቀጥሎም ዳዊት ያዘው፤ ታቦቱንም ወደ ጽዮን አመጣ፤ 2ሳሙ. 5፥6-9፤ 6፥10-12። በኋላ ግን ጽዮን ቤተ መቅደስ ለተሠራበት ሞሪያ ለተባለው ተራራ መጠሪያ ሆነ (ኢሳ. 8፥18፤ 18፥7፤ 24፥23)፤ ለመላዋ ኢየሩሳሌምም መጠሪያ ስም ሆነ፤ 2ነገ. 19፥21፤ መዝ. 48፥2፤ 69፥35። ጠቅላላው የአይሁድ ሕዝብም በቦታው ስም ጽዮን እየተባሉ ይጠራሉ፤ መዝ. 126፥1። በምሳሌነት መንግሥተ ሰማያትን ሊያመለክት ይችላል፤ ዕብ. 12፥22።

**ጽድቅ፤** ጽድቅ ማለት ፦ ሕግን መፈጸም፥ እንደ ሕግ መኖርና መመራት፥ ትክክለኛነት፥ እውነት ማለት ነው።

1. የእግዚአብሔር ጽድቅ፤ እግዚአብሔር በጽድቅ ይኖራል። ሁሉን በባሕርዩ መሠረት ያደርጋል። ዓለምን በጽድቅ መሠረተ፤ በጽድቅም ይፈርዳል፤ ለእያንዳንዱ እንደ ሥራው ዋጋውን ይሰጣል፤ መዝ. 10፥8፤ ዳን. 9፥7፤ ሐ.ሥ. 17፥31፤ 1ጴጥ. 1፥17።

2. የሰው ጽድቅ፤ ሰዎች እንደ ሕግ ሊኖሩ ታዝዘዋል። ነገር ግን ሕግን የፈጸመ አንድ እንኳ የለም። ሕግን የሚከታተሉ እሱና በመጠን ይፈጽሙታል፤ «ጻድቅ» ይመ.። ነገር ግን ሁሉ ኃጢአትን ሠርተዋል፤ የእግዚአብሔርም ክብር ጎድሎአቸዋል፤ ሮሜ 3፥23። «ኃጢአት» ይመ.

እንግዲህ ኃጢአተኛ ሕግን ሳይፈጽም ሲቀር በእግዚአብሔር ፊት በጽድቅ ሊቆም እንዴት ይችላል? ጳውሎስ በሮም 3፥20-5፥21 ና በሌላም ቦታ ለዚህ ጥያቄ ሰፋ ያለ ማብራሪያ ይሰጣል። የሚከተሉትን ነገሮች ልብ ማድረግ ይገባል።

ሀ) «የሕግን ሥራ በመሥራት» ማንም አይጸድቅም፤ ሮም 3፥20፤ ገላ. 2፥16።

ለ) ሰው በእግዚአብሔር ጸጋ ይጸድቃል፤ ሮም 3፥24፤ ኤፌ. 2፥8። ይህም በሰው ዘንድ ምክንያት ሳይገኝ፥ እግዚአብሔር እንዲሁ በፍቅሩ ኃጢአተኞችን ለማዳን እንደወሰነ ያሳያል፤ 2ጢሞ. 1፥9።

ሐ) ሰው በክርስቶስ ደም ይጸድቃል። ክርስቶስ ጻድቅ ሆኖ የኃጢአትን ውጤት ስለ ኃጢአተኞች ተቀበለ፤ በኃጢአተኞች ፈንታ የሕግን እርግማን በመስቀል ላይ ተሸከመ፤ ሮም 3፥25፤ 5፥9፤ ገላ. 3፥13። «ማስተስረያ» ይመ.

መ) ሰው በእምነት ይጸድቃል። ይህም ማለት ሰው በእግዚአብሔር ሲያምን ተስፋውን ሁሉ በጌታ ላይ ይጥላል፤ ሮም 3፥25፤ 5፥1፤ ገላ. 2፥16፤ «እምነት» ይመ.። ሲያምን እምነቱ ጽድቅ ሆኖ ይቈጠርለታል። የዚህም ዋና ምሳሌ አብርሃም ነው፤ ሮም 4፥3-5:22-25፤ ገላ. 3፥6-8። የጽድቅ መቈጠርና የኃጢአት አለመቈጠር የተያያዙ ናቸው፤ ሮም 4፥6-8፤ «ተቈጠረ» ይመ.። ለምእመናን የሚቈጠር የእግዚአብሔር ጽድቅ ነው። አማኙ ከክርስቶስ ጋር ተባብሯልና እግዚአብሔር በክርስቶስ ያየዋል። በክርስቶስ ጽድቅ ይገኛል፤ ኤር. 23፥6፤ ሮም 3፥21፤ 1ቆሮ. 1፥30-31፤ 2ቆሮ. 5፥21፤ 2ጴጥ. 1፥1።

ሠ) ሰው ያለ ሕግ ሥራ ይጸድቃል፤ ሮም 3፥28፤ 4፥5።

ረ) ይህ ጽድቅ በብ.ኪ. ተነግሮ ነበር፤ ዕን. 2፥4፤ ሮም 1፥17፤ 3፥21።

ሰ) እግዚአብሔር በዚህ መንገድ ሰዎችን በማጽደቅ ጻድቅ መሆኑን ይገልጣል፤ ሮም 3፥25:26።

ቀ) አማኞች ክርስቶስን ሲከተሉ በጽድቅ መንገድ ሊራመዱ ይጀምራሉ። ምንም እንኳን ለውጥ በሕይወታቸው እንዲሁ ባያስተውሉ ጠባያቸው ሊለወጥ ይችላል፤ ማቴ. 25፥31-46፤ ሮም 6፥19። ለውጥ ባይገኝ ግን እምነታቸው እውነተኛ የልብ እምነት አይደለምና አልጸደቁም። የሰው መጽደቅ የሚታየው በሥራው ነውና ሥራ እምነቱን ይሞላል። እውነተኛ መሆኑን ያረጋግጣል፤ ያዕ. 2፥18-26።

**ጽጌ ረዳ፤** ሽታው ደስ የሚያሰኝ አበባ። የልዩ ልዩ ዓይነት አበባ ስም ከዕብራይስጥ ሲተረጎም ጽጌ ረዳ ተብሎ የተጠራ ይመስላል፤ መ.መ. 2፥1፤ ኢሳ. 35፥1።

**ጾም፤** በሃይማኖት ምክንያት ያለ ምግብና ያለ መጠጥ መዋል፤ አስ. 4፥16። ደግሞም ከሥጋና ከሚያስከር መጠጥ መከልከልንም ያመለክታል፤ ዳን. 10፥2:3። ሙሴ አርባ ቀንና አርባ ሌሊት ጾመ፤ ዘዳ. 9፥9:19። የእስራኤል ሕዝብ በማስተስረያ ቀን እንዲጾሙ ታዘዙ፤ ዘሌ. 16፥29-31። ከምርኮውም በኋላ አራት የጾም ጊዜያት ታወጁ፤ ዘካ. 8፥19። ደግሞም አይሁድ ከሐማ እጅ ከዳኑ በኋላ ጾም ታወጀ፤ አስ. 9፥31። ከእነዚህም ሌላ በልዩ ልዩ ምክንያት የግል (2ሳሙ. 12፥22)፥ ወይም የማኅበር ጾም አለ፤ መሳ. 20፥26፤ ኢዩ. 1፥14።

ጾም ኀዘንን (ነህ. 1፥4)፥ ንስሓን (1ሳሙ. 7፥6)

ያሳያል። ሰዎች በጾም ራሳቸውን አዋረዱ (መዝ. 69፥10)፥ የእግዚአብሔርን እርዳታ ፈለጉ፤ ዘጸ. 34፥28፤ ዕዝ. 8፥21-23። ነቢያት ጾም ማለት ምን እንደሆነ በመልካም ሁኔታ ገልጠዋል፤ ኢሳ. 58፥1-12፤ ኤር. 14፥11:12።

በአ.ኪ. ዘመን አይሁድ የማስተስረያ ጾምን አከበሩ፤ ሐ.ሥ. 27፥9። ፈሪሳውያን ሰኞና ሐሙስ ይጾሙ ነበር፤ ሉቃ. 18፥12። እነሐናም ብዙ ጊዜ ይጾሙ ነበር፤ ሉቃ. 2፥37። ክርስቶስ አርባ ቀን ጾመ (ማቴ. 4፥2)፥ ስለ ጾምም አስተማረ። ደቀ መዛሙርቱ ከእርሱ ጋር ሳሉ አልጾሙም። ከዚያ በኋላ ግን እንደ ሌሎች እንደሚጾሙ ነገራቸው፤ ማቴ. 9፥14-17። በጾም ጊዜ እግዚአብሔርን እንጂ ሰውን መመልከት አይገባም፤ ማቴ. 6፥16-18። ምእመናን ወንጌላውያንን ሲልኩ፥ ሽማግሌዎችን (ቀሳውስትን) ሲሾሙ ጾሙ፤ ሐ.ሥ. 13፥2:3፤ 14፥23። ዋናው የጾም ዓላማ ከእግዚአብሔር ጋር መገናኘት ነውና ሰው ሲጾም ጊዜውን በጸሎት ሊያውል ይገባዋል፤ ዕዝ. 8፥23፤ ማቴ. 17፥21፤ ሉቃ. 2፥37።

ጾም፥ ምእመናን ሁለንተናቸውን ከዓለማዊ አሳብና ምኞት መልሰው በመንፈሳዊ ነገር ላይ ሙሉ በሙሉ በማረፍ አብዝተው እንዲጸልዩ ያደርጋል።

**ጾርዓ፡** ከኢየሩሳሌም በስተምዕራብ 25 ኪ. ሜ. ርቆ የሚገኝ የሶምሶን ከተማ፤ መሳ. 13፥2፤ 16፥31።

**ፀሐይ፡** ቀንና ሌሊት፥ ጊዜያትና ዐቅጣጫዎች የሚታወቁትና የሚለዩት በፀሐይ ነው፤ ዘፍ. 1፥14-16፤ ኢሳ. 45፥5:6። ፀሐይ ለእርሻ አስፈላጊ ነው፤ ዘዳ. 33፥14። የእግዚአብሔርን ታማኝነት ያመለክታል፤ መዝ. 19፥4-6፤ 72፥5። የክርስቶስ ክብር እንደ ፀሐይ ለእነጴጥሮስ ታየ፤ ማቴ. 17፥2፤ ራእ. 1፥16። ጻድቃን እንደ ፀሐይ ያበራሉ፤ ማቴ. 13፥43። በመጨረሻው ጊዜ ፀሐይ ይጨልማል፤ ኢዩ. 2፥10:31። «ጨረቃ» ይመ.

በጥንት ዘመን ሰዎች በፊንቄና በግብጽ፥ አንዳንዴም በእስራኤል ፀሐይን ያመልኩ ነበር፤ ኢዮብ 31፥26-28፤ 2ነገ. 21፥3:5፤ 23፥5፤ ሕዝ. 8፥16።

ኢያሱ 10፥13፤ 2ነገ. 20፥11፤ ኢሳ. 38፥8 በፀሐይ ላይ የተደረጉትን ተአምራት ይገልጣሉ።

**ፀባኦት፡** «ጸባኦት» ይመ.

**ፀዳል፡** (ጸዳል)፥ የብርሃን ውጋጋን ነፀብራቅና ብልጭታ። የፍርድና የጽድቅ ምሳሌ ነው (ኢሳ. 59፥9፤ አሞጽ 5፥20)፤ የእግዚአብሔርን ክብር ያመለክታል፤ ሕዝ. 8፥2፤ ዕን. 3፥4:11።

**ፃሕል፡** ከሸክላ፥ ከናስ፥ ከብረት፥ ከብርና ከወርቅ የሚሠራ ጎድጓዳ ወይም ዝርግ ወጭት (ሳሕን)፤ ምሳ. 25፥11።

**ፃዕር፡** ጭንቀት፥ ከሞት አፋፍ መድረስ፤ ኢዮብ 21፥6።

**ፈሊታውያን (ፈልቲ)፡** የፍልስጥኤማውያን ነገድ። ዳዊት ከእነዚህና ከከሊታውያን የክብር ዘበኞችን ይመርጥ ነበር፤ 2ሳሙ. 8፥18፤ 1ነገ. 1፥38።

**ፈላስፎች፡** ሐ.ሥ. 17፥18። «ፍልስፍና» ይመ.

**ፈረስ፡** ለጦርነትና የጭነት ከብት። የልብ ቢስ ሰው ምሳሌ ነው፤ መዝ. 32፥9። «እንስሳት» ይመ.



ፈረስ ከነልጓሙ

**ፈረሱላ፡** ከእርሳስ የሚሠራ የሚዛን ድንጋይ። 17 ኪሎ ያህል ይሆናል። «ታላንት» የሚለውን ቃል ለማብራራት በግርጌ ማስታወሻ ተጠቅሷል፤ ራእ. 16፥21።

**ፈረፈር፡** ከገደልና ከሸለቆ ሥር ያለ ዋሻ መሰል ጉድጓድ፤ ኢዮብ 30፥6።

**ፈሪሳውያን፡** ከአይሁድ የሃይማኖት ወገኖች አንዱ ክፍል። የሙሴን ሕግ በብዙ ጥንቃቄ ተረጐሙ። ሰዎች ሕጉን እንዳይተላለፉ ብዙ ትእዛዝና ሥርዓት ጨመሩበት። ይህም ለተራው ሕዝብ ከባድ ሸክም ሆነ፤ ማቴ. 15፥1-4፤ 23፥1-4። ዋና አሳባቸው ሰው የሚጸድቀው በግል ሕይወቱና ሕግን በመፈጸም ነው የሚል ነበር፤ ሐ.ሥ. 15፥5። በመካከላቸው እንደ እነኒቆዲሞስና እንደ እነጳውሎስ ያሉ ቅን ሰዎች ነበሩ። ብዙዎች ግን በሕግ ላይ የተጨመረውን የአባቶች ወግ እየተመለከቱ ዋናውን የሕግ መንፈስ፥ ፍርድን፥ ምሕረትንና ታማኝነትን ረሱ። በዚህ ምክንያት ክርስቶስ ደጋግሞ ግብዞች በማለት ወቀሳቸው፤ ሉቃ. 11፥37-44፤ ማቴ. 23። በክርስቶስ ዘመን ፈሪሳውያን ስድስት ሺህ ያህል ደርሰው ነበር፤ ሀብታሞችም ነበሩ፤ ብዙ ጊዜም በምኵራቦች መሪዎች ነበሩ። ፈሪሳውያን የተቃወሙ በቤተ መቅደስም ሥልጣን ያገኙ ሰዱቃውያን የሚባሉ ወገኖችም ነበሩ፤ ሐ.ሥ. 23፥6-8። ፈሪሳውያን ክርስቶስን ለመግደል ተማከሩ፤ ዮሐ. 11፥47-57። በኋላም አንዳንዶች

በክርስቶስ አመኑ፤ ሐ.ሥ. 15፥5። «ሳዱቃውያን» ይመ.

**ፈርስ፤** ከሆድ ውስጥ ያለ የእበር ጥርቅም፤ ዘጸ. 29፥14፤ ዘሌ. 8፥17።

**ፈርባር፤** የዕብራይስጥ ቃል ነው፤ ትርጉሙን አይታወቅም። ምናልባት መመላለሻ ክፍል ወይም ቤት ማለት ይሆናል፤ 1ዜ.መ. 26፥18፡19።

**ፈርዖን፤** የኢትዮጵያ ነገሥታት «አፄ» ይባሉ እንደ ነበር ከጥንት ጀምሮ የግብጽ ነገሥታት «ፈርዖን» ይባሉ ነበር። በብሉይ ኪዳንም የተጠቀሱት ከጥቂቶች በቀር በመጠሪያ ስም ስማቸው ሳይለዩ በዚህ የማዕረግ ስማቸው ብቻ ይጠራሉ።

1. በአብርሃም ዘመን የነበረው፤ ዘፍ. 12፥15-20።

2. በዮሴፍ ዘመን የነበረው፤ ዘፍ. 37-50።

3. እስራኤልን ያስጨነቀው፤ ዘጸ. 1ና2፤ ዕብ. 11፥23፡24።

4. በአገሩ ላይ መቅሠፍት እንዲወርድ ምክንያት የሆነው፤ ዘጸ. 3-15።

እስራኤላውያን ከግብጽ የወጡበት ዓመት የተረጋገጠ አይደለም። ሆኖም እግዚአብሔርን በመገዳደር «እስራኤልን አልለቅም» ያለው፥ ዳግማዊ ራምሲስ የተባለው ፈርዖን የነበረ ይመስላል። እርሱ በእግዚአብሔር እንዳያምን ልበ ደንዳና ነበረ፤ ዘጸ. 7፥14። ከመቅሠፍቶቹም የተነሣ ሊጸጸት ቢጀምርም (ዘጸ. 8፥8፡28)፥ በአፎይታ ጊዜ ሁሉ በደንዳናነቱ ጸና፤ ዘጸ. 8፥15፡32፤ 9፥34። በሰው ክፋት እንኳ እንደሚከበር ለማሳየት እግዚአብሔር የደነደነውን ልቡን አጸና፤ ዘጸ. 7፥3-5፤ 10፥1፡2፤ 14፥4፤ ሮም 9፥17።

5. ይሁዳዊው ሜሬድ ያገባት የቢትያ አባት፤ 1ዜ.መ. 4፥18።

6. ኤዶማዊውን ብላቴና ሃዳድን የተቀበለው፤ 1ነገ. 11፥17-22።

7. የሰሎሞን አማት፤ 1ነገ. 3፥1፤ 7፥8፤ 9፥16፡24፤ 11፥1።

8. ሺሻቅ የተባለው፤ 1ነገ. 11፥40፤ 14፥25፡26፤ 2ዜ.መ. 12፥2-12።

9. ሴዋር የተባለው፤ 2ነገ. 17፥4።

10. ኒካው የተባለው፤ በኤር. 25፥19. የተጠቀሰው ፈርዖን እርሱ ነው፤ «ኒካው» ይመ.

11. ሖፍራ የተባለው (ኤር. 44፥30)፤ የይሁዳን ንጉሥ ሴዴቅያስን ሊረዳ መጥቶ የተመለሰው እርሱ ሳይሆን አይቀርም፤ ሕዝ. 17፥15-17፤ ኤር. 37፥5፡7።

**ፈርጥ፤** ከዕንቍና ከአልማዝ፥ ከወርቅና ከብር በሚሠራ ዘውድ ወይም ቀለበት ላይ የሚደረግ ልዩ ጌጥ። በልብሰም ላይ አልፎ አልፎ የሚጣል ጥለት ፈርጥ ይባላል፤ ዘጸ. 25፥7፤ 28፥11። «ማዕድን» ይመ.

**ፈሰሴ፤** በአንድ አገር ላይ የሚጣል የግብር ዕዳ፤ 2ነገ. 23፥33፤ 2ዜ.መ. 36፥3።



ባለ ፈርጥ የጆሮ ቀለበት

**ፈሳሽ ነገር፤** በሕመም ሆነ በማይገባ ሁኔታ ከሰውነት የሚወጣ ሁሉ። እንደ ሙሴ ሕግ ወንድንም ሆነ ሴትን ያረክሳል፤ ዘሌ. 15። በሉቃ. 8፥43-48 የተጠቀሰችው ሴት እንደ ሙሴ ሕግ ሰውን መንካት አይፈቀድላትም ነበር። «በሽታ» ይመ.

**ፈስጋ፤** በተራራማ አገር ከፍ ያለ ዳገት ወይም የተራራ ጫፍ፤ ዘኍ. 21፥20፤ 23፥14፤ ዘዳ. 3፥27፤ 34፥1።

**ፈቃድ፤**

1. የእግዚአብሔር ፈቃድ። እግዚአብሔር ሳይገደድ እንደፈቀደ ሁሉንም ነገር ያደርጋል፤ ቲቶ 1፥1-2። ሰው እግዚአብሔርን ደስ በሚያሰኝ መንገድ ይመላለስ ዘንድ እግዚአብሔር ፈቃዱን ለሰው በሕጉ ገልጧል። ሕጉ፥ እግዚአብሔር ፈቃዱን ከሚገልጥባቸው መንገዶች አንዱ ነው። ከዚህም በተጨማሪ እግዚአብሔር ዓላማውን የሚያራምድበት የተሰወረ ፈቃድ አለው፤ ዘዳ. 29፥29፤ ኤፌ. 1፥5፡11። ሰው በእግዚአብሔር ፈቃድ መሠረት ይኖር ዘንድ የሚያስፈልገው የተገለጠው ፈቃድ ብቻ ነው፤ ሚክ. 6፥8። አብ ፈቃድ አለው (ማቴ. 7፥21፤ ዕብ. 10፥7)፥ ወልድ ፈቃድ አለው (ሉቃ. 22፥42፤ ዮሐ. 4፥34፤ ዕብ. 10፥7-9)፥ መንፈስ ቅዱስ ፈቃድ አለው፤ ዕብ. 2፥4፤ 1ቆሮ. 12፥4-11። ሦስቱ አካላት በባሕርይ አንድ ስለሆኑ ፈቃዳቸው አንድ ነው። «ሥላሴ»፥ «እግዚአብሔር ቍ. 5 እና 6»፥ «የእግዚአብሔር መጋቢነት 4» ይመ.

2. የሰው ፈቃድ፤ እግዚአብሔር፥ ሰው የሚፈልገውን በነፃነት እንዲመርጥ ስላደረገ፥ የሰው ልጅ መልካምንም ሆነ ክፉውን ለመሥራት አይገደድም፥ ወይም በውጭ ኃይል አይወሰንም፤ ዘዳ. 30፥19፤ ኢሳ. 7፥11-12፤ ማቴ. 17፥12፤ ዮሐ. 5፥40፤ ያዕ. 1፥13-14፤ 4፥7። ሰው በኃጢአት ከመውደቁ በፊት መልካሙንና እግዚአብሔር የሚወደውን ለመምረጥና ለማድረግ አቅምና ዝንባሌ ነበረው (ዘፍ. 1፥26፡31፤ መክ. 7፥29፤ ኤፌ. 4፥24፤ ቆላ.

3፥10)፣ ሆኖም ይህ ችሎታ ተለዋዋጭ መሆን ስለሚችል፣ ሰው በኃጢአት ከወደቀ በኋላ ክፉውንና እግዚአብሔር የማይወደውን መረጠ፤ ዘፍ. 2፥16-17፤ 3፥6፡17። ሰው በኃጢአት ከወደቀ በኋላ ወደ ደኅንነት የሚያደርስ አቅም አልነበረውም፤ ኤር. 17፥9፤ ዮሐ. 6፥44፡65፤ 15፥5፤ ሮም 3፥11። ስለዚህ ከዚያ ዓይነት መልካም ነገር ጋር በመቃቃሩ (ሮም 3፥9-12፡23፤ 8፥7-8) እና በኃጢአት ምውት በመሆኑ (1ቆሮ. 2፥14፤ ኤፌ. 2፥1-2፡5፤ ቆላ. 2፥13)፣ በኃይሉ ራሱን ወደ መልካም ሊመልስ ወይም ሊያዘጋጅ አይችልም፤ ዮሐ. 3፥3-6፤ ቲቶ 3፥3-5። እግዚአብሔር ሰውን በጸጋው ሲመልሰውና ወደ ራሱ ሲያመጣው ከተፈጥሮ ከኃጢአት ቀንበር ያላቅቀዋል፤ ዮሐ. 8፥34፡36፤ ሮም 6፥6-8፤ ቆላ. 1፥13-14። በጸጋውም መንፈሳዊ የሆነውን መልካም ነገር በነፃነት ለመምረጥና ለመፈጸም ያስችለዋል፤ ፊል. 2፥13፤ ሮም 6፥14፡17-19፡22። ይህም ሆኖ ግን በውስጡ የኃጢአት ቅሬት ገና ስላለ፣ መልካሙን ነገር ሁሉ አጠቃልሎ አይመርጥም፤ ወይም መጥፎውንም ከመምረጥ ጨርሶ አይቆጠብም፤ ገላ. 5፥17፤ ሮም 7፥14-25፤ 1ዮሐ. 1፥8፡10። ሰው መልካሙን ነገር ብቻ የሚከተለው ከትንሣኤው በኋላ ነው፤ ዕብ. 12፥23፤ 1ዮሐ. 3፥2፤ ይሁዳ 24፤ ራእ. 21፥27።

**ፈተና፤** ፈተና በብዙ መንገድ ሊመጣ ይችላል።

1. ዕቃ እንደሚፈተን ሰውም ይፈተናል፤ 1ሳሙ. 17፥39፤ 1ነገ. 10፥1። ክርስቶስ በሰው ተፈተነ፤ ማር. 8፥11፤ 12፥15፤ ሉቃ. 10፥25።

2. ሰው ራሱን ለአንድ ዓይነት ነገር ያዘጋጀ ለመሆኑ ራሱን ሊፈትን ይገባዋል፤ 1ቆሮ. 11፥28፤ 2ቆሮ. 13፥5።

3. ሰው እግዚአብሔርን ለመፈታተን ይሞክራል፤ ግን እንዳይፈታተን ተጽፏል፤ ዘጸ. 17፥2፤ ዘዳ. 6፥16፤ ሐ.ሥ. 5፥9፤ 15፥10።

4. ሰይጣን ሰዎችን ይፈትናል፣ ስለዚህም «ፈታኝ» ተብሏል፤ ማቴ. 4፥3፤ 1ተሰ. 3፥5። መከራን በማብዛት (1ጴጥ. 5፥9፤ ራእ. 2፥10)፣ የማይገባ ምኞትን በመቀስቀስ (ማቴ. 4፥3፤ 1ቆሮ. 7፥5)፣ ሰዎችን በማጣላት (ኤፌ. 4፥27)፣ ስለ እግዚአብሔር እውነት ጥርጥርን ወይም ሐሰትን በመዝራት ሊጥላቸው ይሞክራል፤ ዘፍ. 3፥1-5፤ ማቴ. 4፥5-11። ሆኖም ምእመናን በእግዚአብሔር ኃይል ሊቃወሙት ይችላሉ፤ እግዚአብሔር የፈተናውን መውጫ መንገድ ያዘጋጅላቸዋል፤ 1ቆሮ. 10፥13፤ ኤፌ. 6፥11-18።

5. እግዚአብሔር የሰው እምነት እንዲገለጥ ሰውን ይፈትናል፤ ዘፍ. 22፥1፤ ዘጸ. 16፥4፤ 20፥20። በዚህም ሰዎች ይነጻሉ (1ጴጥ. 1፥6)፣ ትዕግሥትን ይማራሉ (ያዕ. 1፥2-4)፣ የእግዚአብሔርንም ፍቅር በይበልጥ ያስተውላሉ፤ ዘፍ. 22፥15-18፤ ሮም 5፥3-5። ሆኖም እግዚአብሔር ሰውን በክፉ አይፈትንም።

ፈተና ራሱ ኃጢአት አይደለም፤ ግን ሰው ሲፈተን በምኞቱም ሲወድቅ ኃጢአት ይሠራል፤ ያዕ. 1፥13-15። ወደ ፈተና እንዳንገባ ከፈተናም እንድንወጣ ለመጸለይ ታዘዝናል፤ ማቴ. 6፥13፤ 26፥41። ክርስቶስ ተፈተነ፤ ግን በፈተናው አልተሸነፈም፤ ሉቃ. 4፥1-13፤ 22፥28፤ ዕብ. 4፥15። በፈተና የሚጸና የተባረከ ነው፤ ያዕ. 1፥12።

**ፈውስ፤** ከበሽታ መዳን፣ ጤናን ማግኘት። በመ.ቅ. ዘመን ልዩ ልዩ መድኃኒት ታውቋል፤ እንደዚሁም ሐኪሞችና ባለመድኃኒቶች ነበሩ። በተለይ በግብጽና በግሪክ አገሮች የመድኃኒትና የቀዶ ጥገና ትምህርት ከፍ ያለ ነበረ። ሆኖም የዛሬ የሕክምና ሊቃውንት እስከ 1900 ዓ.ም. ገደማ ድረስ የነበረው መድኃኒትና የሕክምና ሥራ የተሟላ አይመስላቸውም። ሰዎች በመድኃኒት ሲያምኑ በነፍስ ሊጠነክሩ ይችላሉ። ጥቅሙ ከእምነት እንጂ ከመድኃኒት አልነበረም። ዛሬ ግን ብዙ ጊዜ በመድኃኒት ቢያምኑም ባያምኑም መድኃኒቱ ፍቱን ነውና ይሠራል።

መ.ቅ. ባለ መድኃኒቶች መኖራቸውን እንጂ ሥራቸውን ብዙ አይገልጥም፤ ዘፍ. 50፥2፤ 2ዜ.መ. 16፥12፤ ኤር. 8፥22፤ ማር. 2፥17፤ 5፥26፤ ቆላ. 4፥14። ለቍስል ሕክምና ነበራቸው፤ ምሳ. 25፥20፤ ኢሳ. 1፥6። በሕዝቅያስ እባጭ ላይ የበለስን ጥፍጥፍ ለበጡ (ኢሳ. 38፥21)፣ በወይን ጠጅና በዘይት ተጠቀሙ፤ ሉቃ. 10፥34፤ 1ጢሞ. 5፥23።

የመ.ቅ. ጸሐፊዎች ስለ ፈውስ ሲያስተምሩ ዋና አሳባቸው እግዚአብሔር ፈዋሽ እንደሆነ ነው፤ ዘጸ. 15፥26። በብ.ኪ. አልፎ አልፎ ሰዎች እንደተፈወሱ ተገልጧል። ማርያምና ንዕማን ከለምጽ ተፈወሱ፤ ዘኁ. 12፥1-15፤ 2ነገ. 5፥8-14። ኤልያስ የሰራፕታዋን ሴትዮ ልጅ (1ነገ. 17፥7-24)፣ ኤልሳዕም የሱነማዊቷን ሴትዮ ልጅ ከሞት አስነሡ፤ 2ነገ. 4፥32-37።

ክርስቶስ ብዙ ሰዎችን ፈወሰ፤ የዳሰሱት ሁሉ እንኳን ዳኑ፤ ማቴ. 4፥23፡24፤ 9፥35፤ 14፥36። ከተፈወሱት ሰዎች መካከል የሃያ ሦስቱ ታሪክ ተገልጧል። ከእነርሱም ሌላ ኢየሱስ የናይንን ሴት ወንድ ልጅ (ሉቃ. 7፥11-17)፣ የኢያኢሮስን ሴት ልጅ (ማቴ. 9፥18-26)፣ አልዓዛርንም ከሞት እንዳስነሣ የሚናገሩት ታሪኮች ተጽፈዋል፤ ዮሐ. 11፥43፡44።

ኢየሱስ ዐሥራ ሁለቱ ሐዋርያት ድውያንን እንዲፈውሱ ሥልጣን ሰጣቸው፤ ማቴ. 10፥1። ሰባ ተከታዮቹም አጋንንትን አወጡ፤ ሉቃ. 10፥17። መንፈስ ቅዱስ ከወረደ በኋላ ብዙ ሰዎች በሐዋርያት (ሐ.ሥ. 2፥43፤ 5፥12-16)፣ በእስጢፋኖስ (ሐ.ሥ. 6፥8)፣ በፊልጶስ (ሐ.ሥ. 8፥5-8)፣ በጳውሎስና በበርናባስ (ሐ.ሥ. 14፥3፤ 19፥11፡12፤ 28፥8-10) ተፈወሱ። ከተፈወሱትም የታወቁት በኢየሩሳሌምና በልስጥራን የነበሩ አንካሶች ናቸው፤ ሐ.ሥ. 3፥1-8፤ 14፥9፡10። ኤንያ የተባለም ሽባ ተፈወሰ፤ ሐ.ሥ. 9፥32-35።

ደግሞም ሐዋርያት ሞቢታንና አውጤኪስን ከሙታን አስነሡ፤ ሐ.ሥ. 9፥36-41፤ 20፥9-12። የመፈወስ ስጦታ ለቤተ ክርስቲያን ተሰጠ፤ 1ቆሮ. 12፥9፡30፡31።

በክርስቶስ ሥራ የወንጌል ሥራና ፈውስ የተያያዙ ነበሩ፤ ኢሳ. 53፥4፤ ማቴ. 8፥16፡17፤ 10፥7፡8፤ ማር. 2፥5። ሐዋርያትም የወንጌልን ቃል ሲያስተምሩ ሰዎችን በመፈወስ ቃሉን እንደሚያረጋግጡ ክርስቶስ ተናገረ። እንደ ቃሉም ተደረገ፤ ማር. 16፥17-20፤ ዮሐ. 14፥12፤ 2ቆሮ. 12፥12፤ ዕብ. 2፥3፡4።

ክርስቶስ በቃሉ (ማቴ. 8፥16፤ ዮሐ. 4፥50)፣ በመዳሰስ (ሉቃ. 5፥13)፣ እጅ በመጫን (ማር. 6፥5)፣ ጭቃን በመቀባት (ዮሐ. 9፥6፡7) ሰዎችን ፈወሰ። ሐዋርያትም እንደዚሁ አደረጉ፤ ደግሞም በዘይት ተጠቀሙ፤ ማር. 6፥13፤ ያዕ. 5፥14።

የፈውስ ኃይል እንዲገኝ ምን ያስፈልጋል? ለዚህ ሙሉ መልስ መስጠት አይቻልም። ነገር ግን የሚከተለውን ብናስተውል ይረዳን ይሆናል፤ ለክርስቶስ እንኳን ልዩ የፈውስ ጊዜ የነበረው ይመስላል፤ ሉቃ. 5፥17። ወደ እርሱ የመጡትን ሁሉ ፈወሰ። ነገር ግን አንዳንድ ጊዜ በሽተኞችን ሳይፈውስ አለፈ፤ ዮሐ. 5፥2-5። ሐዋርያት ጥሮፊሞስንና ጢሞቴዎስን አልፈወሱም፤ 1ጢሞ. 5፥23፤ 2ጢሞ. 4፥20።

ሰዎች ሲፈወሱ ብዙ ጊዜ ሦስት ድርጊቶች እንደ ተፈጸሙ እናያለን፣ እነርሱም የሚከተሉት ናቸው ፦ (ሀ) ለመዳን ፈቃደኛ መሆንና መለመን፤ ዮሐ. 5፥6፤ ያዕ. 5፥14። ብዙ ጊዜ ሰዎች ለበሽተኞች ለመኑ፤ ዮሐ. 4፥49። (ለ) ንስሐ፤ ማር. 2፥1-12፤ ያዕ. 5፥16። (ሐ) እምነት፤ ይህ በሽተኛውን (ማቴ. 9፥22፡29፤ ሐ.ሥ. 14፥9) ወይም የበሽተኛውን ወዳጆች እምነት የሚመለከት ይሆናል፤ ማር. 2፥5፤ 9፥22-24፤ ሉቃ. 7፥6-10። በናዝሬት ሰዎች ካለማመናቸው የተነሣ ክርስቶስ ከጥቂቶች በቀር ብዙ ድውዮችን አልፈወሰም፤ ማር. 6፥5። «ተአምር» ይመ.

**ፈጪ፤** በምሳሌነት ጨቆነ፤ ኢሳ. 3፥15። «ወፍጮ» ይመ.

**ፈፋ፤** በዝናብ ጊዜ ትንሽ ወንዝ የሚፈስበት፤ 1ነገ. 17፥5-7።

**ፉር፤** በዕብራይስጥ ፑር ይላል። በአሦር ቋንቋ «ፑሩ» ማለት ለዕጣ የሚሆን ጠጠር ድንጋይ ማለት ነው። አይሁድን ለማጥፋት ሲል ጠላታቸው ሐማ ፉር የተባለውን ዕጣ አስጥሎ ዕድል የሚሰጥ ቀን ለማወቅ ተተነኰለ፤ አስ. 3፥7፤ 9፥24። አይሁድ ከሐማ እጅ ከዳኑ በኋላ የሦስት ቀን የደስታ በዓል ተወሰነላቸውና በዓሉ ፉሪም (ዕጣዎች) በሚል ስም ተሰየመ፤ አስ. 9፥26-32። በዓሉም በአዳር ወር (በመጋቢት) ከ13ኛው ቀን እስከ 15ኛው ቀን ይከበራል። «በዓላት» ይመ.

**ፉካ፤** ጠባብ የማንብ ወይም የማናቸውም ቤት ቀዳዳ። ጠባብ መስኮትም ፉካ ይባላል፤ ሕዝ. 8፥7።

**ፉጥ፤** 1. የካም ልጅ፤ ዘፍ. 10፥6። 2. በአፍሪካ ውስጥ የሚገኝ አንድ አገር። ዛሬ ስሙ ስለተለወጠ የትኛው እንደሆነ አይታወቅም። አንዳንዶች ከግብጽ በስተምዕራብ፣ ሌሎች ደግሞ ከግብጽ በስተደቡብ ነበረ ይላሉ፤ ሕዝ. 30፥5፤ 38፥5፤ ኤር. 46፥9።

**ፊልሞና፤** የሚከተለውን ይመ.

## ወደ ፊልሞና የተላከ መልእክት፤

ፊልሞና በቆላስይስ የኖረና ወንጌልን ከሐዋርያው ጳውሎስ እንደበት የሰማ ሰው ነው። ቤቱ የቆላስይስ ቤ.ክ. መሰብሰቢያ ሆነ፤ ፊልሞና 2፤ ቆላ. 4፥17። አናሲሞስ የተባለ ባሪያ የነበረው ሲሆን፣ የስሙ ትርጓሜም «ጠቃሚ» ማለት ነው፤ 10-11። አናሲሞስ ከፊልሞና ኰብልሎ በሙሄድ በሮም እስር ቤት ታስሮ ከሚገኘው ከሐዋርያው ጳውሎስ ጋር ተገናኘ፤ በዚያም ወንጌልን ሰምቶ አመነና ጳውሎስን ማገልገል ጀመረ። ባሪያ ከጌታው ሲሸሽ በሮማውያን ሕግ መሠረት የሞት ፍርድ ሊፈረድበት ይችል ነበር። ጳውሎስ ግን አናሲሞስ አሁን በክርስቶስ የፊልሞና ወንድም በመሆኑ ከጌታው ጋር ሊያስታርቀው ፈለገ። ስለዚህ ይህን መልእክት ጽፎ አናሲሞስን ወደ ቆላስይስ ላከው። ይህ የተፈጸመው ምናልባት በ62 ዓ.ም. ገደማ ሊሆን ይችላል። ጳውሎስ የባርነትን ሕግ አልተቃወመም። ስለ ባሪያዎችና ስለ አሠሪዎች በሰጠው ክርስቲያናዊ ትምህርት ግን የባርነትን ኑሮ ለወጠ፤ በመጨረሻም አማኞች ወንድማማቾች በመሆናቸው ባርነት የሚቀርበትን አቅጣጫ አሳየ፤ ፊልሞና 16፤ ቆላ. 4፥1፤ ኤፌ. 6፥5-9። «ባሪያ»፣ «ባርነት» ይመ.። ሐዋርያው እንደዚህ በማድረጉ ማናቸውንም የኅብረተሰብ ሁኔታ ለማሻሻልና ለመለወጥ ወይም ፈጽሞ ለማስቀረት የሚቻልበትን ዘዴ ጠቆመ። ሐዋርያው የሚያቀርበው ልመና ክብደት ቢኖረውም፣ አጻጻፉ በወዳጆች መካከል የሚኖረውን ለስላሳ ያለ የግንኙነት ባሕርይ የያዘ አጻጻፍ ነው። ልመናውንም በ 3 ክፍሎች አከታትሎ ያቀርባል ፦

1. ወንድማማችነታቸውን አጠናከረ፤ 1-9።
2. ምክንያቱን አብራራ፤ 10-16።
3. ፈቃዱን አነሣሣ፤ 17-25።

**ፊልክስ፤** ከ52-60 ዓ.ም. የነበረ የይሁዳ ገዥ። ስለ ትክክለኛ ፍርድ የማያስብ ጉቦ ተቀባይ ነበር፤ ጳውሎስ በእርሱ ዘንድ ተከሰሰ፤ ሐ.ሥ. 23፥24-24፥27።

**ፊልድልፍያ፤** በጥንት ዘመን በትንሹ እስያ የነበረች ከተማ። አንድ ንጉሥ ለወንድሙ ታማኝነት መታሰቢያ ከተማይቱን ሠርቶ ፊልድልፍያ ብሎ ሰየማት። ትርጓሜው የወንድማማች ፍቅር ማለት ነው። በ17 ዓ.ም. ከተማይቱ በመሬት መንቀጥቀጥ ፈረሰች፣ እንደገናም ተሠራች። ጳውሎስ በኤፌሶን ሳለ ቤ.ክ. በፊልድልፍያ የተመሠረተች ይመስላል፤ ሐ.ሥ. 19፥10፤ ራእ. 1፥11፤ 3፥7-13። ዛሬ ከተማይቱ አላሳሕር ትባላለች። ካ. 7ሰ።

**ፊልጶስ፤** የኢጡርያስና የጥራኮኒዶስ ገዥ። «ሄሮድስ» ይመ.

**ፊልጶስ፤** የሄሮድስ ወንድም የሄሮድያዳ ባል። «ሄሮድስ» ይመ.

**ፊልጶስ ሐዋርያ፤** ከዐሥራ ሁለቱ ሐዋርያት አንዱ፤ ማቴ. 10፥3። እንደ እንድርያስና ጴጥሮስ ከቤተ ሳይዳ ነበረ። ኢየሱስ ካገኘው በኋላ ናትናኤልን ወደ ኢየሱስ አመጣው፤ ዮሐ. 1፥42-47። የኢየሱስን ኃይል ባለማስተዋሉ በተፈተነ ጊዜ አጥጋቢ መልስ አልሰጠም፤ ዮሐ. 6፥5-7። ከእንድርያስ ጋር ግሪኮችን ወደ ኢየሱስ አቀረበ፤ ዮሐ. 12፥20-22። የኢየሱስንም ሥራ ባለማስተዋሉ አብን እንዲያሳያቸው ኢየሱስን ጠየቀ፤ ዮሐ. 14፥8-11። በኋላ ከሌሎች ሐዋርያት ጋር የትንሣኤው ምስክር ሆነ፤ ሐ.ሥ. 1፥13፤ 2፥14።

**ፊልጶስ ወንጌላዊ፤** በኢየሩሳሌም ቤ.ክ. ከተሾሙት ሰባት አገልጋዮች አንዱ፤ ሐ.ሥ. 6፥3-5። እስጢፋኖስ ከሞተ በኋላ ፊልጶስ ወደ ሰማርያ ወርዶ ሲያስተምር ብዙ ሰዎች በስብከቱ አመኑ። በዚያን ጊዜም መንፈስ ቅዱስ ወደ ምድረ በዳ ሲመራው፥ ስለ ክርስቶስ የተጻፈውን የኢሳይያስን ትንቢት ይመረምር የነበረውን ኢትዮጵያዊ ሰው አግኝቶ ክርስቶስን ሰበከለት (ሐ.ሥ. 8)፥ በኋላም ትንቢት ይናገሩ ከነበሩ ከአራት ደናግል ሴቶች ልጆቹ ጋር በቂሣርያ ተቀመጠ፤ ሐ.ሥ. 21፥8:9።

**ፊልጶስ ቂሣርያ፤** ከቅድስት አገር በስተሰሜን፥ ከአርሞንዔም ተራራ በስተደቡብ የሚገኝ ከተማ። የዮርዳኖስ ወንዝ መፍለቂያ እዚያ ነበረ። በባሕር ዳር ከነበረው የቂሣርያ ዋና ከተማ ሌላ ቂሣርያ መሆኑን ለማሳየት ፊልጶስ ቂሣርያ ተባለ፥ በፊልጶስ ተሠርቶ ነበርና፤ «ሄሮድስ 6» ይመ.። በፊልጶስ ቂሣርያ አቅራቢያ ኢየሱስ ደቀ መዛሙርቱን ስለ ራሱ ማንነት ጠየቃቸው፤ ማር. 8፥27-38። ካ. 5ሐ።

**ፊልጵስዩስ፤** ፊልጵስዩስ በመቄዶንያ አውራጃ የምትገኝ የግሪክ ከተማ ናት። የተመሠረተችውም ከሮም እንሥቶ ወደ ምሥራቅ አገሮች በሚያመራው ታላቅ ጐዳና ላይ ነው። «ፊልጵስዩስ» የተባለችበት ምክንያት የመቄዶንያ ንጉሥ የሆነው ፊልጶስ የተባለው የታላቁ እስክንድር አባት ከተማይቱን ስለያዘና በ358 ከክ. ል. ዳግመኛ ስለቈረቈራት ነው። በ168 ከክ. ል. ሮማውያን ግሪኮችን ባሸነፉ ጊዜ እንደ ሌሎች ሁሉ የሮም ንጉሠ ነገሥት መንግሥት ከተማ ሆነች። ቀጥሎ ቅኝ አገር ሆና ለነዋሪዎችዋ የሮም ዜግነት ተሰጣቸው። ወንጌል የደረሳት ጳውሎስ ለ2ኛው የስብከት ወንጌል ጕዞው ሲወጣ ነው። ፊልጵስዩስ ወንጌልን ለመስማት ከአውሮፓ ክፍለ ዓለም የመጀመሪያይቱ ከተማ ናት፤ ሐ.ሥ. 16፥9-12። የመጀመሪያዎቹ የቤ.ክ. አባሎች ልድያ የተባለችዋ ሐር ሻጭና የወኅኒ ቤት ጠባቂ ናቸው፤ ሐ.ሥ. 16፥14-33። ካ. 6ሸ።

**የፊልጵስዩስ መልእክት፤** ቅዱስ ጳውሎስ ይህን መልእክት በጻፈ ጊዜ እስረኛ ስለነበረ የሞት ፍርድ ሊፈረድበት ይችል ነበር፤ 1፥1:7:13:20-24፤ 2፥23-24። አንዳንዶች ጳውሎስ በኤፌሶን ታስሮ ሳለ መልእክቱን በ54 ዓ.ም. ገደማ እንደጻፈው ያስባሉ፤ 2ቆሮ. 11፥23። የሚበዙቱ ግን ጳውሎስ ሮም ሆኖ እንደላከው ስለሚገምቱ ምናልባት በ62 ዓ.ም. ሳይጻፍ አልቀረም፤ ሐ.ሥ. 28፥30-31።

በሐዋርያውና በፊልጵስዩስ ቤ.ክ. መካከል ልዩ መግባባትና ፍቅር ነበረ። ቤ.ክ.ቱ ለወንጌል ሥራው ብዙ ጊዜ ድጋፍ ሰጥታዋለች፤ 4፥15-16። አሁንም አፍሮዲጡ ከፊልጵስዩስ ተልኮ ጳውሎስን ሲያገለግል ሳለ ታሞ ነበርና አፍሮዲጡ ወደ ፊልጵስዩስ መመለሱ የተሻለ መሆኑን ጳውሎስ አምኖበት ደብዳቤ ጽፎ በእጁ ሊልካቸው ወሰነ፤ 2፥25-30። በመልእክቱ የሚከተሉትን ነጥቦች መመልከት ተገቢ ይሆናል ፦

1. ለሚሰጥ እርዳታ የምስጋና ምክንያቶች፤
   1፥3-5፤ 4፥10-19።
2. የጳውሎስ የግል ሕይወት ዓላማ፤ 3፥4-14።
3. የክርስቶስ ትሥጉትና ክብር የተገለጠበት ታላቅ አንቀጽ፤ 2፥5-11።
4. ስለ ክርስቲያናዊ ትብብር ትምህርት፤ 1፥27-30፤
   2፥1-4:12-18፤ 3፥17-18፤ 4፥2-3።
5. የጳውሎስ ደስታ፤ ሐዋርያው ቢታሰርም፥ አንዳንድ ምእመናን ባይስማሙም (4፥2)፥ «ውሾች» እና «የክርስቶስ መስቀል ጠላቶች» ቢኖሩም (3፥18-19) ዋናው ስሜቱ ደስታ ነው። የደስታ አሳብ 16 ጊዜ ያህል በዚህ አጭር መልእክት ይገኛልና ለመልእክቱ አከፋፈል ቍልፍ ቃል ይሆናል።

የጳውሎስ ደስታ በሚከተሉት ነጥቦች ይታያል ፦

1. በፊልጵስዩስ ቤ.ክ. አቋም፤ 1፥1-9
2. በተስፋው፤ 1፥10-30
3. ክርስቶስን ከፍ ከፍ በማድረጉ፤ 2፥1-11
4. በፊልጵስዩስ ቤ.ክ. ትዕግሥት፤ 2፥12-18
5. አብረው በሚሠሩት ጓደኞቹ፤ 2፥19-30
6. ክርስቶስን በማወቅ፤ 3፥1-15
7. በሰማያዊ ርስቱ፤ 3፥16-21
8. በመንፈሳዊ ትብብር፤ 4፥1-3
9. በጌታው፤ 4፥4-9
10. በፊልጵስዩስ ቤ.ክ. ልግስና፤ 4፥10-20
11. በሰላምታና በቡራኬ፤ 4፥21-23።

**ፊስጦስ፤** ከፊልክስ ቀጥሎ እስከ ሞተበት ዓመት እስከ 62 ዓ.ም. ድረስ የነበረ የይሁዳ ገዥ። ከፊልክስ የተሻለ ገዥ ነበረ፥ ግን ጳውሎስ ንጹሕ መሆኑን እያወቀ አይሁድን ለማስደሰት ወደ ኢየሩሳሌም ለፍርድ ሊልከው አሰበ። ጳውሎስ ግን ወደ ቄሣር ይግባኝ አለ። ንጉሥ አግሪጳንና በርኒቄን ለማስደሰት ጳውሎስን በፊታቸው አቀረበ፤ ሐ.ሥ. 24፥27፤ 25፥1-26፥32።

**ፊሶን፤** ከዔድን የወጣ ወንዝ፤ ዘፍ. 2፥11። ዛሬ የትኛው እንደሆነ አይታወቅም።

**ፊት**፤ የሰው ስሜቱ በፊቱ ይታወቃል፤ መዝ. 83፥16፤ ምሳ. 15፥13። ፊትን መሰወር መራቅን ያሳያል፤ መዝ. 27፥9። ሰው የእግዚአብሔርን ፊት ሊያይ አይችልም፤ ዘጸ. 33፥20። ሰው ሲሞት ፊቱ ይሸፈን ነበርና ለሐማ የሞት ምልክት ሆነ፤ አስ. 7፥8፤ ዮሐ. 11፥44።

**ፊንሐስ**፤ 1. የአልዓዛር ልጅ፣ የአሮን የልጅ ልጅ፤ ዘጸ. 6፥25፤ 1ዜ.መ. 6፥4:50፤ ዕዝ. 7፥5፤ 8፥2። ለእግዚአብሔር ቀንቶ እስራኤላዊውን ዘንበሪንና ምድያማዊቱን ከስቢን በመግደል መቅሠፍትን አቆመ፤ እግዚአብሔርም የሰላሙን ቃል ኪዳን ሰጠው፤ ዘኁ. 25፤ መዝ. 106፥28-31። ሙሴም የመቅደሱን ዕቃ አስይዞ ወደ ጦርነት ላከው፤ ዘኁ. 31፥6። የሮቤልና የጋድ፣ የምናሴም ነገዶች ስለሠሩት መሠዊያ እንዲጠይቁ ለተላኩት መልእክተኞች መሪ ነበረ፤ ኢያሱ 22፥13:30:32። አባቱን ከቀበረ በኋላ (ኢያሱ 24፥33)፣ በአባቱ ምትክ የካህናት አለቃ ሆነ፤ መሳ. 20፥27:28፤ 1ዜ.መ. 9፥20። 2. ክፉ ከነበሩት ከሁለቱ የዔሊ ልጆች ታናሹ፤ 1ሳሙ. 1፥3፤ 2፥12-17:29። ከወንድሙ ጋር የእግዚአብሔርን ታቦት ወደ ሰልፍ ወሰደ፣ ሁለቱም በጦርነቱ ላይ ሞቱ፤ የፊንሐስ ሚስት ከድንጋጤ የተነሣ ወልዳ ሞተች፤ 1ሳሙ. 2፥34፤ 4። በሳኦል ዘመን የልጅ ልጁ ካህን ነበረ፤ 1ሳሙ. 14፥3።

**ፊንቄ**፤ ከገሊላ ወደ ሰሜን እስከ 200 ኪ.ሜ. ያህል ስፋት ያለው በታላቁ ባሕር ዳር ያለ አገር። ዋና ከተማዎች በንግድ፣ በኪነ ጥበብና በሥነ ጽሑፍ የታወቁ ጢሮስና ሲዶና ናቸው። ከዚህ አገር ለመጣችው ሴት ክርስቶስ ልጅዋን ፈወሰላት፤ ማር. 7፥24-30። ጳውሎስ በስብከት ጉዞው ይህን አገር ጎበኘ፤ ሐ.ሥ. 15፥3።

**ፊደል**፤ በጽሕፈት የቋንቋ መግለጫ። «ዕብራይስጥ»፣ «ግሪክ» ይመ.። ሕግን በፊደል



የግሪክ ተማሪ ፊደል ሲያጠና፤ በ450 ገደማ ከክ.ል. በሸክላ ዕቃ ላይ ተቀርጾ የተገኘ

መተርጐም ማለት የሕጉን መንፈስ፣ ስሜትና ምክንያት ባለማስተዋል ቃል በቃል መፈጸም ማለት ነው፤ ሮም 7፥6፤ 2ቆሮ. 3፥6።

**ፋራን**፤ ከቤርሳቤህ በስተደቡብ በሲና ውስጥ የሚገኝ ምድረ በዳ። እስማኤል በፋራን ተቀመጠ (ዘፍ. 21፥21)፣ እስራኤላውያንም በዚያ ተጓዙ፤ ዘኁ. 10፥12፤ 12፥16፤ 13፥26። የፋራን ተራራ ኤልፋራን ተብሏል (ዘፍ. 14፥6)፣ የትኛው እንደሆነ ግን አይታወቅም። ዕንባቆም ክርስቶስ ከፋራን እንደሚመጣ ተናገረ፤ ዕን. 3፥3። ይህም ምናልባት ኤፍራታን (ሚክ. 5፥2)፣ ወይም ከግብጽ መምጣቱን ያመለክት ይሆናል።

**ፋርስ**፤ ከጤግሮስ ወንዝ በስተምሥራቅ የነበረች አገር። መንግሥቷ ሲስፋፋ ሱሳ መናገሻ ከተማ ሆነ። ሜዶንን አጣምራ በቂሮስ መሪነት ባቢሎንን በ539 ከክ. ል. አሸነፈች። ቂሮስ እስራኤላውያን ወደ ኢየሩሳሌም ተመልሰው ቤተ መቅደስ እንዲሠሩ ፈቀደ፤ ዕዝ. 1። የፋርስ ንጉሥ አርጤክስስ አስቴርን አገባ፣ ስለ አይሁድ ሕዝብ የለመነችውን ልመና ተቀበለ፤ መጽሐፈ አስቴር ይመ.። ዕዝራም ብዙ ሰዎችን አስከትሎ ወደ ኢየሩሳሌም እንዲመለስና ሕጉን እንዲያስተምር ፈቀደለት (ዕዝ. 7፤8)፣ እንደገናም ተለምኖ የኢየሩሳሌምን ቅጥር እንዲሠራ ነህምያን ላከው፤ ነህ. 2፥1-8። የፋርስ መንግሥት በግሪክ ንጉሥ በታላቁ እስክንድር በ331 ከክ. ል. ሲሸነፍ የዳንኤል ትንቢት ተፈጸመ፤ ዳን. 8፥1-8:15-22።

**ፋሲካ**፤ በዕብራይስጥ «ፓሳሕ» ማለት አለፈ ማለት ነው። የእስራኤል ልጆች በግብጽ አገር በግ አርደው፣ ደሙን በደጃፋቸው በመርጨት ከእግዚአብሔር ቍጣ ዳኑ። የእግዚአብሔር መልአክ በዚያች ሌሊት ግብጻውያንን ሲቀሥፍ፣ ደም በነበረበት ቤት አልፎ ስላልገደለ ወይም ደም የተረጨበትን ቤት ስላለፈ፣ ቀኑ ፋሲካ ተባለ። ለፋሲካ የሚታረደውም በግ ፋሲካ ይባላል፤ ዘጸ. 12፥1-13። በየዓመቱ በግ እያረዱ የእስራኤል ልጆች በመጀመሪያ ወራቸው በ14ኛው ቀን የፋሲካን በዓል ያከብራሉ። ከዚያም ምሽት እስከ አንድ ሳምንት ድረስ የቦካውን ነገር ለመብላት ስላልተፈቀደላቸው፣ የሙሉ ሳምንት በዓል የቂጣ በዓል ተባለ። የቂጣ እንጀራ መብላት የእስራኤል ልጆች በችኰላ ከግብጽ መውጣታቸውን የሚያስታውስ የመታሰቢያ ምልክት ነው፤ ዘጸ. 12፥18-20:33:34፤ ዘዳ. 16፥1-3። ኢየሱስ ክርስቶስ የተሰቀለበት ሳምንት የፋሲካ ሳምንት ነበረ፤ ሉቃ. 22፥14-16፤ ዮሐ. 18፥38-40። እርሱም ንጹሕ የእግዚአብሔር በግ ሆኖ ደሙን ስላፈሰሰልን «ፋሲካችን ክርስቶስ» ተባለ፤ 1ቆሮ. 5፥7፤ 1ጴጥ. 1፥18-19። ስለዚህ የክርስቶስ ትንሣኤ በዓል ፋሲካ ተብሎ ይጠራል።

**ፋቁሔ**፤ የሮሜልዩ ልጅ፣ ከ740 እስከ 732 ከክ. ል. የነገሠ ዐሥራ ስምንተኛው የእስራኤል ንጉሥ። ፋቂስያስን ገድሎ ነገሠ፤ ክፉ ሥራ ሠራ፤ 2ነገ. 15፥25:27:28። ከሶርያ ንጉሥም ጋር ተባብሮ በይሁዳ ነገሥታት በኢዮአታምና በአካዝ ላይ ዘመተ፤

2ነገ. 15፥37፤ 16፥5፤ ኢሳ. 7፥1:5:6። ተዋጋቸው እንጂ አላሸነፋቸውም፤ 2ዜ.መ. 28፥5-15፤ ኢሳ. 7፥4-7። በእርሱም ዘመን የአሦር ንጉሥ እየበረታ ሲሄድ፥ በገለዓድና በገሊላ የነበሩትን እስራኤላውያን ማረከ፤ 2ነገ. 15፥29። የኤላም ልጅ ሆሴዕ ገደለው፤ በእርሱም ቦታ ነገሠ፤ 2ነገ. 15፥30።

## ፋቂስያስ፤
ከአባቱ ከምናሔም በኋላ ከ742-740 ከክ. ል. የነገሠ ዐሥራ ሰባተኛው የእስራኤል ንጉሥ። ክፉም ሥራ ሠራ፤ የሠራዊቱ አለቃ የሆነው ፋቁሔ ገደለው፤ 2ነገ. 15፥23-26።

## ፋነነ፤
ሮጠ፥ ፈረጠጠ፤ 2ሳሙ. 6፥6። በራሱ ፈቃድ ሄደ፤ ኢሳ. 28፥7።

## ፋንድያ፤
የፈረስ፥ የበቅሎና የጋማ ከብት ሁሉ ፍግ። ለማብሰያ (ሕዝ. 4፥12-15)፥ ለተክል ማዳበሪያም ይሆናል፤ ሉቃ. 13፥8። በሕዝ. 4፥12-15 ላይ የተጠቀሰው ከሰው የሚወጣውንም ዐይነ ምድር ያመለክታል። ፋንድያ የመርገም ምሳሌ ነው፤ ሚል. 2፥3።

## ፋጋ፤
የቅል ከፋይ፥ የሸክላ ስባሪ ትልቅ መጠሚ፤ አሞጽ 6፥6።

## ፌርዛውያን (ፌርዜዎን)፤
በከነዓን አገር የነበረ ሕዝብ፤ ዘፍ. 13፥7፤ 34፥30፤ ዘጸ. 3፥8፤ ኢያሱ 24፥11፤ መሳ. 1፥4።

## ፌዘኛ፤
የሚነቅፍ፥ የሚያሾፍ፥ ቀልደኛ፥ ዋዘኛ፤ ዘፍ. 19፥14፤ መዝ. 1፥1፤ ምሳ. 9፥8።

## ፍልስጥኤም፥ ፍልስጥኤማውያን፤
ከካም ነገድ የወጡ፥ ከከፍቶርም የመጡ በደቡብ ከነዓን በባሕር ዳር ባለው ሜዳ የነበሩ ናቸው፤ ዘፍ. 10፥14፤ አሞጽ 9፥7። አምስት ከተማዎች ነበሯቸው። እነርሱም ጋዛ፥ አዛጦን፥ አስቀሎና፥ ጌትና አቃሮን ናቸው፤ ኢያሱ 13፥3፤ 1ሳሙ. 6፥17። ካ. 3ቀ፤ 3ሰ።

አማልክታቸው ከከነዓናውያን አማልክት ጋር በመደባለቅ ዳጎን፥ አስታሮት፥ ብዔልዜቡል ተብለዋል። አቢሜሌክ ከፍልስጥኤም ንጉሥ ከአቢሜሌክ ጋር ቃል ኪዳን ገባ፤ ዘፍ. 21፥22-34። ከዚህ ጊዜ ጀምሮ ፍልስጥኤማውያን እየበዙና በጦርነትም እየበረቱ ሄዱ። የታወቁ ከመሆናቸው የተነሣ የኖሩበት ብቻ ሳይሆን፥ ከነዓን ሁሉ ፍልስጥኤም (ፓለስታይን) ተባለ። እስራኤላውያን ከግብጽ ሲወጡ ፍልስጥኤማውያንን ፈርተው እንዳይመለሱ በዙሪያ መንገድ ወደ አገራቸው ገቡ፤ ዘጸ. 13፥17። በመሳፍንት ዘመን ፍልስጥኤማውያን እስራኤልን ወጉ፤ ታቦቱን ማረኩ፤ በኋላም ሳኦልንና ዮናታንን ገደሉ። የብረታ ብረት ሥራ ስለሚያውቁ እስራኤላውያንን የማረሻ ግብር አስገበሩ፤ 1ሳሙ. 13፥19-21።

እስራኤላውያን እግዚአብሔርን ሲከተሉ ግን ጠላቶችን አስገዝተው አሸነፉአቸው። ከእነርሱም መካከል ሰሜጋር (መሳ. 3፥31)፥ ሶምሶን (መሳ. 13-16) እና ሳሙኤል የታወቁት ናቸው፤ 1ሳሙ. 7፥1-14። ዳዊት ፍልስጥኤማዊውን ጎልያድን ገደለ፤ በዘመኑ መንግሥቱም ሠለጠነባቸው፤ 1ሳሙ. 17፤ 2ሳሙ. 19፥9፤ 21፥15-22። በኋላም ፍልስጥኤማውያን አልፎ አልፎ በጠላትነት እየተነሡ እስራኤልን አስጨነቋቸው፤ 2ዜ.መ. 21፥16፤ ኢሳ. 9፥8-12፤ ዘካ. 9፥6።



የፍልስጥኤም ወታደሮችን የሚያሳይ፤ በግብጽ ከተገኘ ቅርጸ ቅርጽ የተገለበጠ

## ፍልስፍና፤
ጠቅላላ ጥበብና ዕውቀት በግሪክ ቋንቋ ፊሎሶፍያ ማለት ዕውቀትን መውደድ ማለት ነው። እውነተኛ ፍልስፍና ስለ ሳይንስም ሆነ ስለ ሌላ ትምህርት ያለው ችሎታና ጥበብ ነው። ሐዋርያው ጳውሎስ ስለ ሐሰተኛና ክርስቶስን ስለሚያስክድ ፍልስፍና አስጠንቅቆናል፤ ቆላ. 2፥8። «ኤፊቆሮስ»፥ «ኢስጦኢክ»፥ «ግኖስቲክ» ይመ.

## ፍልፈል፤
ምድርን የሚፈረፍር፥ የሚነድል፥ አፈርን የሚቆፍል ጥቁር የዱር አይጥ፤ ኢሳ. 2፥20።

## ፍም፤
የነደደ እንጨት ወይም ከሰል። ለሙቀት፥ ምግብንም ለማብሰል እንደሚጠቅም ተጠቅሷል፤ ኢሳ. 6፥6፤ 47፥14፤ ዮሐ. 18፥18፤ 21፥9።

## ፍሪዳ፤
ለትልቅ ግብዣ የሚታረድ የሰባና የወፈረ ንጹሕ ሰንጋ ወይም ሙሲና ከብት። በብ.ኪ. ለመሥዋዕት ይቀርብ ነበር፤ 2ሳሙ. 6፥13፤ መዝ. 66፥15፤ ሉቃ. 15፥23።

## ፍሬ፤
ከሕያው ፍጥረት ሁሉ የሚገኝ (ዘፍ. 4፥3፤ ዘጸ. 23፥19)፤ ቃሉ ለሰውና ለእግዚአብሔር ሥራ ይጠቀማል፤ ማቴ. 7፥16-17፤ 12፥33፤ 21፥19:43፤ ዮሐ. 15፥2:16፤ ገላ. 5፥22።

## ፍርሃት፤
1. የበላይ የሆነን ሰው በተገቢ ረገድ ማክበር፥ መፍራት። በዚህ ዓይነት እግዚአብሔርን መፍራት የጥበብ መጀመሪያ፥ የሰውም ሁለንተና ነው፤ ምሳ. 9፥10፤ መክ. 12፥13። ሰዎች

እግዚአብሔርን ፈርተው ትእዛዙን ይፈጽማሉ፤ ኃጢአትንም ይጠላሉ፤ ዘፍ. 22፥12፤ 31፥42፤ ኤር. 32፥40፤ ሐ.ሥ. 10፥2። እንደዚሁም በሰዎች ዘንድ የበላይ የሆኑትን አክብሮ ለእነርሱ መታዘዝ ይገባል፤ ሮም 13፥7፤ 1ጴጥ. 2፥18።

2. አምላክን፥ ሰውን ወይም ማናቸውንም ነገር በመንቀጥቀጥና በድንጋጤ መፍራት። ይህ ዓይነት ፍርሃት በኃጢአት ምክንያት ወደ ዓለም ገባ፤ ዘፍ. 3፥10፤ ምሳ. 28፥1። ወንጌልን ያልተቀበሉ በፍርድ ምክንያት ፍርሃት ይይዛቸዋል፤ ሐ.ሥ. 16፥29፤ 24፥25፤ ዕብ. 10፥26:27፤ ራእ. 21፥8። አማኝ እግዚአብሔርን በፍቅር ስለሚያውቅ ከፍርሃት ባርነት ይድናል፤ ሮም 8፥15፤ 1ዮሐ. 4፥18። ሆኖም በፍርድ ቀን በእግዚአብሔር ፊት እንደሚቆም ያውቃልና እግዚአብሔርን አክብሮ በተገቢ ፍርሃት ይኖራል፤ ፊል. 2፥12፤ 1ጴጥ. 3፥15።

**ፍርድ**፤ የፍርድ ዋና አሳብ እውነትን ከሐሰት መለየት ነው፤ ዘዳ. 25፥1። መ.ቅ. በአምስት መንገድ የፍርድን ሁኔታ ይገልጣል።

1. ነገሩን ማስተዋል፤ ምሳ. 1፥3፤ 2፥8። ሰው በግብዝነት፤ ማለትም ራሱ እየፈጸማቸው ባሉት ነገሮች ላይ በሌላው እንዳይፈርድ ተከልክሏል፤ ማቴ. 7፥1-6። መ.ቅ. በግብዝነት በሰው ላይ እንዳንፈርድ ያስጠነቅቀናል፥ ምክንያቱም ፍርድን በራሳችን ላይ ያመጣልና (ሮም 2፥1)፥ በቂ መሠረት የለንም (ዮሐ. 8፥7)፥ መብት የለንም (ሮም 14፥4)፥ ለውጥም አያመጣም፤ 1ቆር. 4፥3-5።

2. የሕዝብ አስተዳዳሪዎች ያለ አድልዎ እንዲፈርዱ ታዝዘዋል፤ ዘዳ. 1፥17፤ 25፥1። «ቅጣት» ይመ.

3. በዓለም ላይ የሚፈጸም የእግዚአብሔር ሥራ። እግዚአብሔር በዚህ ዓለም በገፊዎችና በኃጢአተኞች ላይ ይፈርዳል፤ አሞጽ 6፥12:14፤ መሳ. 1፥7። እግዚአብሔር እስራኤላውያንን ሲታዘዙለት ባረካቸው ከፈቃዱ ሲወጡ ግን ቀጣቸው። ሲቀጣቸውም እንዲቀደሱ እንጂ እንዲጠፉ አልነበረም፤ ኤር. 25፥29፤ 1ጴጥ. 4፥17።

4. በዓለም መጨረሻ የሚሰጥ የመጨረሻ ፍርድ። ይህ «በእግዚአብሔር ቀን» ይፈጸማል፤ ኢሳ. 2፥12፤ አሞጽ 5፥18። ያን ጊዜ ፈራጁ ክርስቶስ ነው። በሰዎች ላይ እንደ ቃላቸው (ማቴ. 12፥36)፥ እንደ ሥራቸው (1ጴጥ. 1፥17)፥ እንደ አሳባቸው (ሮም 2፥16) ይፈርዳል። በጽድቅ ይፈርዳል፤ ሐ.ሥ. 17፥31። ያላመኑት ከአመኑት ይለያሉ፤ ማቴ. 13፥24-43:47-50፤ 25፥31-46። እንደ ጥፋታቸው ይቀጣሉ (ሮም 2፥12፤ ሉቃ. 11፥31:32፤ 12፥46-48)፥ ቅጣታቸው ዘላዓለማዊ ነው (ራእ. 20፥13-15)፥ ክርስቶስን አምነው የተከተሉ ደግሞ እንደ ሥራቸው ዋጋቸውን ይቀበላሉ (ሉቃ. 19፥16-19፤ ሮም 14፥10፤ 1ቆር. 3፥12-15፤ 2ቆር. 5፥10)፥ ለዘላዓለም በመንግሥተ ሰማያት ይኖራሉ፤ ዮሐ. 3፥16፤ ራእ. 21፥1-7።

5. ኩነኔ (የዘለዓለም ፍርድ)፤ አማኞች ከኩነኔ በታች አይደሉም፤ ሮም 8፥1። «ኩነኔ» ይመ.

**የፍርድ ቀን**፤ በዓለም መጨረሻ እግዚአብሔር ይፈርዳል። ቀኑ መቼ እንደሆነ አልተገለጠም። ነገር ግን እግዚአብሔር ወስኖታል፤ ማቴ. 24፥36፤ ሐ.ሥ. 17፥31።

**የፍርድ ወንበር**፤ ንጉሥ፥ ገዥ፥ ዳኛ፥ ፍርድ ሲሰጥ የሚቀመጥበት፤ ማቴ. 27፥19፤ ሐ.ሥ. 18፥12። ምእመናን በክርስቶስ ፍርድ ወንበር ፊት ይቆማሉ፤ ሮም 14፥10፤ 2ቆር. 5፥10።

**ፍርግያ**፤ በትንሹ እስያ በስተምዕራብ ደቡብ ያለች ጠቅላይ ግዛት። 133 ከክ.በ. የሮም ግዛት ሆነች። ጳውሎስ በሁለተኛውና በሦስተኛው የስብከት ጉዞዎቹ በፍርግያ ወንጌልን አስተማረ፤ ሐ.ሥ. 16፥6፤ 18፥23። ዛሬ ይህች ቦታ በቱርክ ውስጥ ትገኛለች። ካ. 6ቀ።

**ፍቅር**፤ ፍቅር የእግዚአብሔር ባሕርይ ነው፤ 1ዮሐ. 4፥8:16። ከሌላ ነገር ሁሉ ፍቅር ይበልጣል፤ 1ቆር. 13፥13። ፍቅር ምንድር ነው ቢባል ፍቹ በሥራው ብቻ ይታወቃል፤ 1ቆር. 13፥4-7። ፍቅር የክርስትና ሃይማኖት መሠረት ነው፤ ሰው ከሰው ጋር፥ ወይም ሰው ከእግዚአብሔር ጋር እንዲተባበር ፍቅር ያስፈልጋል፤ ማቴ. 22፥37-39፤ ማር. 12፥28-31፤ ዮሐ. 13፥34-35።

እግዚአብሔር አስቀድሞ ልጁን ኢየሱስ ክርስቶስን ወዶአል፤ ዮሐ. 17፥24። እግዚአብሔር ሕዝቡን ስለሚወድድ በክርስቶስ ሞትና ትንሣኤ ደኅንነትን ፈጸመላቸው፤ ሮም 5፥8-10፤ ዮሐ. 13፥1፤ 1ዮሐ. 4፥9:10። ማንኛውም ነገር ምእመናንን ከክርስቶስ ፍቅር አይለይም (ሮም 8፥31-39)፤ መንፈስ ቅዱስ በአማኝ ውስጥ ፍቅርን ያሳድራል፤ ሮም 5፥5፤ ገላ. 5፥22።

ምእመናንም ፍቅርን መከታተል ይገባቸዋል፤ ማቴ. 5፥43-48፤ ቆላ. 3፥14። ፍቅራቸው በመታዘዛቸው ይገለጣል፤ ዮሐ. 14፥15፤ 1ዮሐ. 3፥22:23። ለእግዚአብሔር ሲታዘዙ በእግዚአብሔር ፍቅር ይኖራሉ፤ ዮሐ. 15፥9:10።

**የፍቅር ግብዣ**፤ ወዳጅነትን ለማጠንከር አብሮ መብላት የተለመደ ነው። ምእመናን ከመጀመሪያ ጀምሮ አብረው ይበሉ ነበር፤ ይህም የፍቅር ግብዣ ተባለ። ዛቲንና ሰንበቱን፥ ማኅበርንም ይመስላል። ብዙ ጊዜ ከጌታ እራት ጋር የተያያዘ ነበር። ሆኖም ልዩ ልዩ የማይገባ ነገር ስለተጨመረ የጌታ እራት ለብቻው ሆነ፤ ሐ.ሥ. 2፥46፤ 1ቆር. 11፥17-34፤ 2ጴጥ. 2፥13፤ ይሁዳ 12።

**ፍየል**፤ ከጥንት የታወቀ ሥጋው ለመሥዋዕትና ለምግብ፥ ቆዳው ለልብስ፥ ለብራና እንዲሁም ጠጉሩ ለልብስ የሚሆን የቤት እንስሳ፤ ዘፍ. 15፥9፤ ዘሌ. 22፥19፤ ዕብ. 11፥37። በብ.ኪ. ሁለት ፍየሎች በማስተስረያ ሥነ ሥርዓት ቀን ይቀርቡ ነበር፤ አንዱ ይታረድ፥ ሁለተኛው ግን ይለቀቅ ነበር፤ ዘሌ. 16፥7-22። ፍየል ከበግ ይልቅ ጠንካራ ነው፤ በደረቅ አገር ሊኖር ይችላል፤ ጠጉሩ ለማቅ ይሆናል። ፍየሎች ክርስቶስን ያልተከተሉ ሰዎች ምሳሌ ናቸው፤ ማቴ. 25፥33።

**ፍግምግም አለ፤** ለመውደቅ ተንገዳገደ፤ ኤር. 23፥12።

**ፍጥሞ፤** በእስያ አጠገብ ያለች ትንሽ ደሴት። ሐዋርያው ዮሐንስ በዚች ደሴት ታስር ነበር፤ ራእ. 1፥9።

**ፍጥረት፤** በመጀመሪያ እግዚአብሔር የሚታየውን ነገር ከሚታየው ሳይሆን በቃሉ ፈጠረ፤ ዘፍ. 1፥1፤ ዕብ. 11፥3። ይህንም ያደረገው ስለወደደ እንጂ ለእርሱ አስፈላጊ በመሆኑ አልነበረም፤ ሐ.ሥ. 17፥25። አብ (ኢሳ. 44፥24)፥ ወልድ (ዮሐ. 1፥1-3)፥ መንፈስ ቅዱስ በመፍጠር ሥራ አንድነት አላቸው፤ ዘፍ. 1፥2። ዓለም ከተፈጠረ ወዲህ በእግዚአብሔር ኃይል ይኖራል፤ ሐ.ሥ. 17፥25፤ ቆላ. 1፥17። ዓለም የተፈጠረው የእግዚአብሔርን ክብር ለመግለጥ ነው፤ መዝ. 19፤ ሮም 1፥20:21፤ ራእ. 4፥11። ከዘፍ. 1፥1-2፥3 የሚከተለውን መገንዘብ ይገባናል።

1. እግዚአብሔር ዓለምን በስድስት ቀን ፈጠረ፥ በሰባተኛው ቀን ከመፍጠር ዐረፈ። አንዳንድ ሊቃውንት መፍጠሩን በስድስት ቀን ገለጠ ይላሉ። ቀን ሲል ረጅም ጊዜን ሊያመለክት ይችላል። «ቀን» ይመ.

2. እግዚአብሔር ለፍጥረት ሁሉ አስፈላጊውን አዘጋጀ፥ በቅደም ተከተል ፈጠራቸው። መላእክት መፈጠራቸውን እንጂ ምንጊዜ እንደተፈጠሩ መ.ቅ. አይገልጥም። ሴትም ከወንድ ብቻ እንደተገኘች ተገልጧል (ዘፍ. 2፥22)፥ ቀኑና ሰዓቱ ግን አልተገለጠም። አስቀድሞ እግዚአብሔር ግዙፍ የሆነውን ነገር ሁሉ ፈጠረ። ከዚያም በኋላ በየቀኑ ፍጥረታትን በየዓይነቱ አደረገ።

3. እግዚአብሔር ፍጥረትን በየወገኑ ፈጠረ፤ ዘፍ. 1፥12:25። አንድ ፍጥረት እንደ ዓይነቱ ይወልዳል፤ እንደ ሁኔታውም ሊለወጥ ይችላል፤ ከወገኑ ግን አይወጣም።

4. እግዚአብሔር ሁሉን መልካም አድርጎ ፈጠረ፤ 1፥4:10:12:18:21:25:31።

5. እግዚአብሔር ሰውን ከፍጥረት ሁሉ በላይ አደረገው፤ 1፥28-30፤ 2፥19። ዘፍ. 1 በጠቅላላው የፍጥረትን ነገር (ሥነ ፍጥረትን) ይገልጣል። ዘፍ. 2 ሰው በመጀመሪያ እንዴት እንደነበረ ይገልጣል።




ስለ ዓለም የድሮ ሰዎች አስተሳሰብ

